የመላው ፡ ዓለም ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፤ ተባበሩ!

# ቭ. ኢ. ሌኒን

# መንግሥትና አብዮት

## ስለመንግሥትና ወዝ አደሩ በአብዮት ውስጥ ስላለው ግዳጆች ማርክሳዊ ቴዎሪ[1]



የፕሮግሬስ ፡ የመጻሕፍት ፡ ማዘጋጃና ፡
ማተሚያ ፡ ቤት ።
ሞስኮ ።



ፕሮግሬስ ፡ ከተባለው ፡ የመጻሕፍት ፡ ማዘጋጃና ፡
ማሳተሚያ ፡ ቤት ።

«መንግሥትና ፡ አብዮት» የተባለው ፡ የሌኒን ፡ ጽሑፍ ፡ የተተረጐመው ፡ በሶቪዬት ፡ ኅብረት ፡ የኮሙኒስት ፡ ፓርቲ ፡ ማዕከላዊ ፡ ኮሚቴ ፡ ሥር ፡ ያለው ፡ የማርክሲዝም-ሌኒኒዝም ፡ ኢንስቲቲዩት ፡ ካዘጋጀው ፡ የሌኒን ፡ ሥራዎች ፡ ፫ ኛው ፡ እትም ፡ ፴፫ ቅፅ ፡ ላይ ፡ ነው ።

ተርጓሚው ፤ አምኃ ፡ ሳሙኤል ።



በሶቪዬት ፡ ኅብረት ፡ ታተመ ።

Л $\frac{10102-171}{014(01)-79}$ 656—79 0101020000

ማውጫ ።



1*

## ለአንደኛው ፡ እትም ፡ መቅድም ።

በአሁኑ ፡ ጊዜ ፡ የመንግሥት ፡ ጥያቄ ፡ በቴዎሪና ፡ በገቢር ፡ ፖለቲካ ፡ ከፍተኛ ፡ ቦታ ፡ ይይዛል ። የኢምፔሪያሊስት ፡ ጦርነት ፡ ሞኖፖሊ ፡ ካፒታሊዝምን ፡ ወደ ፡ መንግሥታዊ ፡ ሞኖፖሊ ፡ ካፒታሊዝም ፡ እንዲሸጋገር ፡ ከፍተኛ ፡ ፍጥነትና ፡ ብርታትን ፡ ሰጥቶታል ። ከጊዜ ፡ ወደ ፡ ጊዜ ፡ ከኃያላን ፡ የካፒታሊስቶች ፡ ኅብረት ፡ ጋር ፡ በጥብቅ ፡ በመተቃቀፍ ፡ ያለው ፡ መንግሥት ፡ በሠርቶ ፡ አደሩ ፡ ሰፊ ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ የሚያደርገው ፡ አሰቃቂ ፡ ጭቆና ፡ ይበልጥ ፡ እንዲብስ ፡ አድርጎታል ። ያደጉት ፡ አገሮች — «ደጀናቸው» ማለታችን ፡ ነው — ወደ ፡ ወታደራዊ ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ የቅጣት ፡ እስር ፡ ቤቶች ፡ በመለወጥ ፡ ላይ ፡ ናቸው ።

ተሰምተው ፡ የማይታወቁ ፡ የተጐታቹ ፡ ጦርነት ፡ መዓቶችና ፡ መከራዎች ፤ የሰፊውን ፡ ሕዝብ ፡ ሁኔታ ፡ አስከፊ ፡ በማድረግ ፤ ቁጣውንም ፡ እንዲጨምር ፡ አድርገውታል ። የዓለም ፡ ወዝ ፡ አደራዊ ፡ አብዮት ፡ በጉልህ ፡ በማደግ ፡ ላይ ፡ ነው ። ከመንግሥት ፡ ጋር ፡ ያለው ፡ ግንኙነትም ፡ ለአብዮቱ ፡ ገቢራዊ ፡ ትርጉም ፡ እያስገኘ ፡ ነው ።

ለብዙ ፡ አስር ፡ ዓመታት ፤ ሲነፃፀር ፡ በሰላማዊ ፡ የዕድገት ፡ ደረጃ ፤ የተጠራቀሙት ፡ የአድርባይነት ፡ ጠባዮች ፡



በመላ ፡ ዓለም ፡ የሚገኙትን ፡ አፌሽል ፡ ሶሺያሊስት ፡ ፓርቲዎችን ፡ ያጥለቀለቀው ፡ የሶሺያል-ሾቪኒዝም ፡ መስመር ፡ እንዲያድግ ፡ አድርጎታል ። ይህ ፡ በቃላት ፡ ሶሺያሊዝም ፡ በገቢር ፡ ግን ፡ ሾቪኒዝም (ትምክህተኛነት) የሆነው ፡ መስመር (ፕሌኻኖቭ ፣ ፖትሬሶቭ ፣ ብሬሽኮቭስካያ ፣ ሩባኖቪች ፣ እንዲሁም ፡ ትንሽ ፡ ደበቅ ፡ ባለ ፡ መልክ ፡ ጸረተሊ ፣ ቼርኖቭና ፡ ግብረአበሮቹ ፡ በሩሲያ ፣ ሸይደማን ፣ ሌጊን ፣ ዳቪድና ፡ ሌሎችም ፡ በጀርመን ፣ ሬኖደል ፣ ጌድ ፣ ቫንደርቬልድ ፡ በፈረንሳይና ፡ በቤልጂግም ፣ ሂንድማንና ፡ ፋቢያኖች ፡[2] በእንግሊዝ ... ወዘተ ... ወዘተ) ልዩ ፡ የሚያደርገው «የሶሺያሊዝም ፡ መሪዎች» ወራዳ ፡ ቀላማጅነት «ለራሳቸው» ብሔራዊ ፡ ቡርዥዋ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን «ለራሳቸው» መንግሥትም ፡ ጭምር ፡ መቆም ፡ ነው ፣ ምክንያቱም ፡ አብዛኞዎቹ ፡ ኃያላን ፡ መንግሥታት ፡ የሚባሉት ፡ ከረጅም ፡ ጊዜ ፡ ጀምሮ ፡ ብዙ ፡ ትናንሽና ፡ ደካማ ፡ ሕዝቦችን ፡ ይበዘብዛሉ ፣ ይጨቁናሉምና ። የኢምፔሪያሊስቶች ፡ ጦርነት ፡ ዓለምን ፡ ለመክፈልና ፡ ለመከፋፈል ፡ የተደረገ ፡ ጦርነት ፡ ነው ። ሠርቶ ፡ አደሩን ፡ ሕዝብ ፡ ከቡርዥዋው ፣ በተለይም ፡ ከኢምፔሪያሊስት ፡ ቡርዥዋው ፡ ቁራኛነት ፡ ለማላቀቅ ፡ የሚደረገው ፡ ትግል ፡ ግቡን ፡ ሊመታ ፡ የሚችለው «መንግሥትን» በሚመለከት ፡ ረገድ ፡ ያለውን ፡ የቆየ ፡ አድርባይና ፡ ማስረጃ ፡ የሌለው ፡ ስህተተኛ ፡ አስተያየት ፡ ጭምር ፡ በመዋጋት ፡ ነው ።

በመጀመሪያ ፡ ማርክስና ፡ ኤንግልስ ፡ ስለመንግሥት ፡ የሰጡትን ፡ ቴዎሪ (ንድፈ ፡ ሐሳብ) እንመረምራለን ፣ ከዚያም ፡ ይህን ፡ ቴዎሪ ፡ በሚመለከተው ፡ በኩል ፡ በተረሱ ፡ ወይንም ፡ አድርባዮች ፡ ሆን ፡ ብለው ፡ ባጣመሟቸው ፡ ነገሮች ፡ ላይ ፡ በዝርዝር ፡ እናተኩራለን ። ቀጥለንም ፡ በተለይ ፡ በዚህ ፡ ማጣመም ፡ ጉዳይ ፡ ዋና ፡ ተጠያቂ ፡ ስለሆነው ፣ በአሁኑ ፡ [illegible] ፡ የደረሰበት ፡






የሁለተኛው ፡ ኢንተርናሽናል (፲፰፻፹፱-፲፱፻፲፬ ዓ. ም.)* የታወቀው ፡ መሪ ፣ ስለካርል ፡ ካውትስኪይ ፡ እንመለከታለን ። በመጨረሻም ፡ የ ፲፱፻፭ ዓ. ም. እና ፡ በተለይም ፡ የ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የሩሲያ ፡ አብዮቶች ፡ ትምህርቶች ፡ ዋና ፡ ዋና ፡ ውጤቶችን ፡ እናቀርባለን ። የ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. አብዮት ፡ በአሁኑ ፡ ጊዜ (ነሐሴ ፡ መጀመሪያ ፡ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም.) የመጀመሪያው ፡ የመስፋፋት ፡ ደረጃውን ፡ በማገባደድ ፡ ላይ ፡ ነው ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ይህን ፡ አብዮት ፡ በአጠቃላይ ፡ የምንመለከተው ፡ በኢምፔሪያሊስት ፡ ጦርነት ፡ ምክንያት ፡ ከሚደረጉት ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ ሶሺያሊስት ፡ አብዮቶች ፡ እንደ ፡ አንድ ፡ ክፍል ፡ ብቻ ፡ ነው ። ስለዚህም ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ ሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ ስለመንግሥት ፡ ጥያቄ ፡ እንደ ፡ ገቢራዊ ፡ ፖለቲካዊ ፡ ጉዳይ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ እንደ ፡ አጣዳፊ ፡ የጊዜው ፡ ጉዳይ ፡ አድርጎ ፡ ነው ፡ የሚመለከተው ፣ ስለሆነም ፡ ሰፊው ፡ ሕዝብ ፡ በቅርብ ፡ ጊዜ ፡ ከተጫነበት ፡ የካፒታል ፡ ቀንበር ፡ ነፃ ፡ ለመሆን ፡ ምን ፡ ማድረግ ፡ እንዳለበት ፡ የማስረዳት ፡ ጉዳይ ፡ ነው ።

ደራሲው ።

ነሐሴ ፡ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም.

---

* በዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ ውስጥ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረቱ ፡ እንደ ፡ አውሮጳ ፡ አቆጣጠር ፡ ነው ። (አዘጋጅው)

በመላ : ዓለም : የሚገኙትን : አፊሽል : ሶሺያሊስት : ፓርቲዎችን : ያጥለቀለቀው : የሶሺያል-ሾቪኒዝም : መስመር : እንዲያድግ : አድርጎታል ። ይህ : በቃላት : ሶሺያሊዝም : በገቢር : ግን : ሾቪኒዝም (ትምክህተኛነት) የሆነው : መስመር (ፕሌኻኖቭ ፤ ፖትሬሶቭ ፤ ብሬሽኮቭስካያ ፤ ሩባኖቪች ፤ እንዲሁም : ትንሽ : ደበቅ : ባለ : መልክ : ጸረተሊ ፤ ቼርኖቭና : ግብረአበሮቹ : በሩሲያ ፤ ሽይደማን ፤ ሌጊን ፤ ዳቪድና : ሌሎችም : በጀርመን ፤ ሬኖደል ፤ ጌድ ፤ ቫንደርቬልድ : በፈረንሳይና : በቤልጂግም ፤ ሂንድማንና : ፋቢያኖች :[2] በእንግሊዝ ... ወዘተ ... ወዘተ) ልዩ : የሚያደርገው «የሶሺያሊዝም : መሪዎች» ወራዳ : ቀላማጅነት «ለራሳቸው» ብሔራዊ : ቡርዥዋ : ብቻ : ሳይሆን «ለራሳቸው» መንግሥትም : ጭምር : መቆም : ነው ፤ ምክንያቱም : አብዛኛዎቹ : ኀያላን : መንግሥታት : የሚባሉት : ከረጅም : ጊዜ : ጀምሮ : ብዙ : ትናንሽና : ደካማ : ሕዝቦችን : ይበዘብዛሉ ፤ ይጨቁናሉምና ። የኢምፔሪያሊስቶች : ጦርነት : ዓለምን : ለመክፈልና : ለመከፋፈል : የተደረገ : ጦርነት : ነው ። ሠርቶ : አደሩን : ሕዝብ : ከቡርዥዋው ፤ በተለይም : ከኢምፔሪያሊስት : ቡርዥዋው : ቁራኛነት : ለማላቀቅ : የሚደረገው : ትግል : ግቡን : ሊመታ : የሚችለው «መንግሥትን» በሚመለከት : ረገድ : ያለውን : የቆየ : አድርባይና : ማስረጃ : የሌለው : ስህተተኛ : አስተያየት : ጭምር : በመዋጋት : ነው ።

በመጀመሪያ : ማርክስና : ኤንግልስ : ስለመንግሥት : የሰጡትን : ቴዎሪ (ንድፈ : ሐሳብ) እንመረምራለን ፤ ከዚያም : ይህን : ቴዎሪ : በሚመለከተው : በኩል : በተረሱ : ወይንም : አድርባዮች : ሆን : ብለው : ባጣመሟቸው : ነገሮች : ላይ : በዝርዝር : እናተኩራለን ። ቀጥለንም : በተለይ : በዚህ : ማጣመም : ጉዳይ : ዋና : ተጠያቂ : ስለሆነው ፤ በአሁኑ : [illegible] : ወድቀት : የደረሰበት :



የሁለተኛው : ኢንተርናሽናል (፲፰፻፹፱-፲፱፻፲፬ ዓ. ም.)* የታወቀው : መሪ ፤ ስለካርል : ካውትስኪይ : እንመለከታለን ። በመጨረሻም : የ ፲፱፻፭ ዓ. ም. እና : በተለይም : የ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የሩሲያ : አብዮቶች : ትምህርቶች : ዋና : ዋና : ውጤቶችን : እናቀርባለን ። የ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. አብዮት : በአሁኑ : ጊዜ (ነሐሴ : መጀመሪያ : ፲፱፻፲፯ ዓ. ም.) የመጀመሪያው : የመስፋፋት : ደረጃውን : በማገባደድ : ላይ : ነው : ነገር : ግን : ይህን : አብዮት : በአጠቃላይ : የምንመለከተው : በኢምፔሪያሊስት : ጦርነት : ምክንያት : ከሚደረጉት : የወዝ : አደሩ : ሶሺያሊስት : አብዮቶች : እንደ : አንድ : ክፍል : ብቻ : ነው ። ስለዚህም : የወዝ : አደሩ : ሶሺያሊስት : አብዮት : ስለመንግሥት : ጥያቄ : እንደ : ገቢራዊ : ፖለቲካዊ : ጉዳይ : ብቻ : ሳይሆን : እንደ : አጣዳፊ : የጊዜው : ጉዳይ : አድርጎ : ነው : የሚመለከተው ፤ ስለሆነም : ሰፊው : ሕዝብ : በቅርብ : ጊዜ : ከተጫነበት : የካፒታል : ቀንበር : ነፃ : ለመሆን : ምን : ማድረግ : እንዳለበት : የማስረዳት : ጉዳይ : ነው ።

ደራሲው ።

ነሐሴ : ፲፱፻፲፯ ዓ. ም.

* በዚህ : መጽሐፍ : ውስጥ : ዓመት : ምሕረቱ : እንደ : አውሮጳ : አቆጣጠር : ነው ። (አዘጋጅው)

## ለሁለተኛው ፡ እትም ፡ መቅድም ።

ይህ ፡ ሁለተኛ ፡ እትም ፡ የታተመው ፡ በአጠቃላይ ፡ አለ ፡ ለውጥ ፡ ነው ። የተጨመረ ፡ ቢኖር ፡ ምዕራፍ ፡ ሁለት ፡ ውስጥ ፡ አንቀጽ ፡ ሶስት ፡ ብቻ ፡ ነው ።

ደራሲው ።

ሞስኮ ።
ታኅሣሥ ፡ ፲፯ ፤ ፲፱፻፲፰ ዓ. ም.

## ምዕራፍ ፡ I.

## የመደብ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብና ፡ መንግሥት ።

### ፩. መንግሥት ፡ የማይታረቁ ፡ የመደብ ፡ ቅራኔዎች ፡ ውጤት ፡ ነው ።

በአሁኑ ፡ ጊዜ ፡ የማርክስ ፡ ቴዎሪ ፡ ያጋጠመው ፡ ከታሪክ ፡ እንደምንረዳው ፤ ጭቊን ፡ መደቦችን ፡ ነፃ ፡ ለማውጣት ፡ ሲታገሉ ፡ በነበሩት ፡ አብዮታውያን ፡ ተመራማሪዎችና ፡ መሪዎች ፡ ቴዎሪዎች (ንድፈ-ሐሳቦች) ላይ ፡ ተደጋግሞ ፡ የደረሰ ፡ ነው ። ጨቋኝ ፡ መደቦች ፡ ታላላቅ ፡ አብዮታውያንን ፡ በሕይወት ፡ ሳሉ ፡ አለማቋረጥ ፡ ያሳድዳሉ ፤ ቴዎሪዎቻቸውን ፡ በከፍተኛ ፡ አረመኔአዊ ፡ ክፋት ፤ ባበደ ፡ ጥላቻና ፡ መሠረት ፡ በሌለው ፡ ውሸትና ፡ ሐሜት ፡ ይቀበሉታል ። ከሞቱ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ አልባ ፡ የለሽ ፡ ምስሎች ፡ ሊለውጧቸው ፡ ይሞክራሉ ፤ እንድያም ፡ መለኮታውያን ፡ ያደርጓቸዋል ፤ ዝነኛ ፡ ስማቸውንም ፡ በመጠቀም ፡ ጭቊን ፡ መደቦችን «ያጽናኑበታል» ፤ ያሞኙበታልም ፤ ይህም ፡ የአብዮታዊ ፡ ቴዎሪዋቸውን ፡ ይዘት ፡ በማኮላሸት ፤ አብዮታዊ ፡ ስለቱን ፡ በማዶልዶምና ፡ በማጉደፍ ፡ ነው ። በአሁኑ ፡ ጊዜ ፡ እንዲህ ፡ ባለው ፡ ማርክሲዝምን ፡ በ«ማከም» ተግባር ፡ ቡርዥዋውና ፡ በሠራተኛው ፡ ንቅናቄ ፡ ውስጥ ፡ ያሉት ፡ አድርባዮች ፡ ይስማማሉ ። የቴዎሪውን ፡ አብዮታዊ ፡ ጐን ፤ የቴዎሪውን ፡ አብዮታዊ ፡ መንፈስ ፡ ያስቀራሉ ፤ ያድበሰብሳሉ ፤ ያጣምማሉ ። ቡርዥዋው ፡ የሚቀበለውን ፤ ወይንም ፡ ሊቀበለው ፡ የሚችለውን ፡ በአንደኛ ፡ ደረጃ ፡ ያቀርባሉ ፤ ያወድሳሉም ።





ሁሉም ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስቶች ፡ አሁን «ማርክሲስቶች ፡ ናቸው» ፤ አትቀልዱባቸው! የጀርመን ፡ የቡርዥዋ ፡ ሊቃውንቶች ፤ የትላንት ፡ ማርክሲዝምን ፡ በማጥፋት ፡ አዋቂዎች ፡ ሁሉ ፡ በመደጋገም ፡ «ስለብሔራዊው ፡ ጀርመናዊው» ማርክስ ፡ ይናገራሉ ፤ እንዲያ ፡ ግሩም ፡ በሆነ ፡ ድርጅታዊ ፡ አቋም ፡ የሠራተኞች ፡ አንድነት ፡ ማኅበሮችን ፡ የዘረፉ ፡ ጠርነት ፡ ለማካሄድ ፡ ማርክስ ፡ ያስተማረ ፡ በማስመሰል!

እንዲህ ፡ ባለ ፡ ሁኔታ ፤ ተሰምቶ ፡ በማይታወቅ ፡ ስፋት ፡ ማርክሲዝም ፡ ሲጣመም ፡ የኛ ፡ ተቀዳሚ ፡ ተግባር ፡ በመጀመሪያ ፡ ማርክስ ፡ ስለመንግሥት ፡ የሰጠውን ፡ ትክክለኛ ፡ ትምህርት ፡ እንደነበረው ፡ ማድረግ ፡ ነው ። ለዚህም ፡ ከማርክስና ፡ ከኤንግልስ ፡ ሥራዎች ፡ ብዙ ፡ ረዣዥም ፡ ጥቅሶች ፡ ያስፈልጉናል ። እርግጥ ፡ ነው ፡ ረዣዥም ፡ ጥቅሶች ፡ ጽሑፉን ፡ ከባድ ፡ ያደርጉታል ፤ ተወዳጅነቱንም ፡ በመጠኑ ፡ ይቀንሱበታል ። ቢሆንም ፡ ይህንን ፡ ላለማድረግ ፡ በፍጹም ፡ አይቻልም ። አንባቢ ፡ ስለ ፡ሳይንሳዊው ፡ ሶሺያሊዝም ፡ መሥራቾች ፡ ጠቅላላ ፡ ርዕዮቶችና ፡ ስለነዚህም ፡ ርዕዮቶች ፡ ዕድገት ፡ የራሱ ፡ የሆነ ፡ ትክክለኛ ፡ አስተያየት ፡ እንዲኖረው ፤ እንደዚሁም «ካውትስኪያውያን» ርዕዮቶቹን ፡ እንዴት ፡ እንዳጣመሟቸው ፡ በመረጃ ፡ ለማረጋገጥና ፡ በግልጽ ፡ ለማሳየት ፡ ከማርክስና ፡ ከኤንግልስ ፡ ሥራዎች ፡ መንግሥትን ፡ በሚመለከተው ፡ የጻፉዋቸውን ፡ ከሆነ ፡ በሙሉ ፤ አለበለዝያ ፡ ቢያንስ ፡ ቢያንስ ፡ አስፈላጊ ፡ የሆኑትን ፡ ክፍሎች ፡ በተቻለ ፡ መጠን ፡ ሰፋ ፡ አድርገን ፡ እንጠቅሳለን ።

እጅግ ፡ በጣም ፡ በታወቀው ፡ የኤንግልስ ፡ ሥራ ፤ «የቤተ ፡ ሰብ ፤ የግል ፡ ንብረትና ፡ የመንግሥት ፡ አመጣጥ» በሚለው ፡ በ፲፰፻፹፬ ዓ. ም. በስቱትጋርት ፡ በታተመው ፡ በስድስተኛው ፡ እትም ፡ እንጀምር ።[3] እዚህ ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ ሩሲያንኛ ፡ ቋንቋ ፡ የተተረጎሙት ፡ ቁጥራቸው ፡ ብዙ ፡ ቢሆንም ፤ [illegible] ፡ ክፍል ፡ ሙሉ ፡ ስላልሆኑ ፤





ወይንም ፡ ደግሞ ፡ አጥጋቢ ፡ ስላልሆኑ ፤ የግድ ፡ ቀጥታ ፡ ከዋናው ፡ ከጀርመንኛው ፡ ጥቅሶችን ፡ ማቅረብ ፡ ሊኖርብን ፡ ነው ።

ኤንግልስ ፡ ታሪካዊ ፡ ትንተናውን ፡ በማጠቃለል ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፤ «መንግሥት ፡ በምንም ፡ ዓይነት ፡ ከውጭ ፡ በኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ላይ ፡ የተጫነ ፡ ኃይል ፡ አይደለም ። እንደዚሁም ፡ ሄጌል ፡ እንደሚያረጋግጠው ፡ መንግሥት «የግብረ ፡ ገብነት ፡ ሃሳብ ፡ ህላዌ (እውነታ)» ፤ «የአእምሮ ፡ መልክና ፡ ህላዌ (እውነታ)» አይደለም ። መንግሥት ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ የተወሰነ ፡ የዕድገት ፡ ደረጃ ፡ ውጤት ፡ ነው ፤ የመንግሥት ፡ መኖር ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ሊፈቱ ፡ በማይቻሉ ፡ ቅራኔዎች ፡ መወጠሩን ፤ ኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ሊያስወግዳቸው ፡ በማይችለውና ፡ ሊታረቁ ፡ ወደማይችሉ ፡ ተፃራሪዎች ፡ መከፈሉን ፡ የሚያረጋግጥ ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ እነዚህ ፡ ተፃራሪዎች ፤ ተቃራኒ ፡ የኤኮኖሚ ፡ ጥቅም ፡ ያላቸው ፡ መደቦች ፤ እርስ ፡ በርሳቸውና ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ በከንቱ ፡ ትግል ፡ እንዳይጠፉ ፤ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ በላይ ፡ ያለ ፡ የሚመስል ፤ ግጭቶቹን ፡ የሚቀንስና ፡ በተወሰነ «ሥነ ፡ ሥርዓት» የሚጠብቅ ፡ ኃይል ፡ አስፈለገ ። ይህ ፡ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ የመነጨ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ራሱን ፡ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ በላይ ፡ ያስቀመጠ ፤ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ከጊዜ ፡ ወደ ፡ ጊዜ ፡ ራሱን ፡ ያገለለው ፡ ኃይል ፡ መንግሥት ፡ ነው ።» (የ፮ኛው ፡ የጀርመን ፡ እትም ፤ ገጽ ፡ ፻፷፪-፻፷፫)

እዚህ ፡ ላይ ፡ ስለመንግሥት ፡ ታሪካዊ ፡ ሚናና ፡ ምንነት ፡ የማርክሲዝም ፡ መሠረታዊ ፡ ሃሳብ ፡ እጅግ ፡ ግልጽ ፡ ሆኖ ፡ ተጠቅሷል ። መንግሥት ፡ የማይታረቁ ፡ የመደብ ፡ ቅራኔዎች ፡ ውጤትና ፡ ማሳያ ፡ ነው ። መንግሥት ፡

ብቅ ፡ የሚልበት ፡ ቦታ ፤ ጊዜና ፡ ምክንያት ፡ የመደብ ፡ ቅራኔዎች ፡ ነባራዊና ፡ ሊታረቁ ፡ የማይችሉ ፡ ስለሆኑ ፡ ነው ። ወይም ፡ በሌላ ፡ አነጋገር ፤ የመንግሥት ፡ መኖር ፡ የሚያረጋግጠው ፡ የመደብ ፡ ቅራኔዎች ፡ የማይታረቁ ፡ መሆናቸውን ፡ ነው ።

ልክ ፡ በዚህ ፡ እጅግ ፡ አቢይና ፡ መሠረታዊ ፡ በሆነው ፡ ነጥብ ፡ ላይ ፡ ነው ፡ እንግዲህ ፤ በሁለት ፡ ትላልቅ ፡ መስመሮች ፡ የሚሄደው ፡ ማርክሲዝምን ፡ የማጣመም ፡ ተግባር ፡ የሚጀመረው ።

በአንድ ፡ በኩል ፡ የቡርዥዋውና ፡ በተለይ ፡ የንዑስ ፡ ቡርዥዋው ፡ ሐሳብ ፡ አቅራቢዎች ፡ በማያከራክሩ ፡ ታሪካዊ ፡ ሐቆች ፡ ኃይል ፡ ተገደው ፤ መንግሥት ፡ ሊኖር ፡ የሚችለው ፡ የመደብ ፡ ቅራኔና ፡ የመደብ ፡ ትግል ፡ ባለበት ፡ ቦታ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ቢያምኑም ፡ መንግሥት ፡ መደቦችን ፡ የሚያስታርቅ ፡ ድርጅት ፡ ነው ፡ በማለት ፡ ማርክስን «ያርማሉ» ። በማርክስ ፡ አነጋገር ፡ መደቦች ፡ የሚታረቁ ፡ ቢሆኑ ፡ ኖሮ ፡ መንግሥት ፡ ሊመሠረትም ፤ ሊቆምም ፡ ባልቻለ ፡ ነበር ። ንዑስ ፡ ቡርዥዋዎችና ፡ ሐሳበ ፡ ውሱን ፤ ሐሳበ ፡ ጠባብ ፡ ፕሮፌሰሮችና ፡ ፑብሊስስቶች ፤ ሁልጊዜና ፡ በብዛት ፡ ማርክስን ፡ በመጠቃቀስ! መንግሥት ፡ መደቦችን ፡ ያስታርቃል ፡ ይላሉ ። በማርክስ ፡ አባባል ፤ መንግሥት ፡ የመደብ ፡ ገዥነት ፡ ድርጅት ፡ ነው ፤ መንግሥት ፡ አንዱ ፡ መደብ ፡ ሌሎች ፡ መደቦችን ፡ የሚጨቁንበት ፡ ድርጅት ፡ ነው ፤ መንግሥት ፡ የመደብ ፡ ግጭቶችን ፡ ቀንሶ ፤ ጭቆናን ፡ ህጋዊና ፡ ነዋሪ ፡ የሚያደርግ «ሥነ ፡ ሥርዓትን» መፍጠር ፡ ማለት ፡ ነው ። በንዑስ ፡ ቡርዥዋው ፡ የፖለቲካ ፡ ሰዎች ፡ አስተሳሰብ ፡ ግን ፡ ሥርዓት ፡ ሲባል ፡ አንድን ፡ መደብ ፡ በሌላ ፡ መደብ ፡ መጨቆን ፡ ማለት ፡ ሳይሆን ፡ መደቦችን ፡ ማስታረቅ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ግጭትን ፡ መቀነስ ፡ ማለት ፡ ማስታረቅን ፡ እንጂ ፡ ከጭቁን ፡ መደቦች ፡ ጨቋኞችን ፡ ለመጣል ፡ በሚያደርጉት ፡



ትግል ፡ የተወሰኑ ፡ የትግል ፡ ስልቶችንና ፡ ዘዴዎችን ፡ መንጠቅ ፡ ማለት ፡ አይደለም ።

ለምሳሌ ፤ ያህል ፡ በ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. አብዮት ፡ የመንግሥት ፡ ጥያቄ ፡ ምንነትና ፡ ሚና ፡ ከፍተኛ ፡ ሥፍራ ፡ በያዘበት ፤ እንደገቢራዊ ፡ ጥያቄ ፡ አሁኑኑ ፡ እርምጃዎች ፤ እንዲያውም ፡ እርምጃዎች ፡ በሰፊው ፡ ባስፈለገበት ፡ ጊዜ ፡ ሁሉም ፡ ሶሺያሊስት-አብዮታውያንና[4] ፡ ሜንሼቪኮች[5] ፡ ወድያውና ፡ በአጠቃላይ «መንግሥት» መደቦችን «ያስታርቃል» ወደሚለው ፤ ወደ ፡ ንዑስ ፡ ቡርዥዋው ፡ ቴዎሪ ፡ ንድፈ-ሃሳብ ፡ አሽቆለቆሉ ። ብዛታቸው ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ሊባሉ ፡ የማይቻሉ ፡ የነዚህ ፡ ሁለት ፡ ፓርቲዎች ፡ የፖለቲካ ፡ ሰዎች ፡ ውሳኔዎችና ፡ ጽሑፎች ፡ ሙሉ ፡ በሙሉ ፡ በንዑስ ፡ ቡርዥዋውና ፡ በሐሳበ ፡ ውሱኑ «የማስታረቅ» ቴዎሪ ፡ የተጥለቀለቁ ፡ ናቸው ። መንግሥት ፡ ከተቃራኒው ፡ መደብ ፡ ጋር ፡ ሊታረቅ ፡ የማይችል ፡ የአንድ ፡ የተወሰነ ፡ መደብ ፡ የገዥነት ፡ ድርጅት ፡ መሆኑን ፡ የንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ዴሞክራቶች ፡ በፍጹም ፡ ሊገባቸው ፡ አይችልም ። በጠቅላላው ፡ ሶሺያሊስት-አብዮታውያንና ፡ ሜንሼቪኮች ፡ ወደ ፡ ሶሺያሊስት ፡ የሚጠጋ ፡ አነጋገር ፡ የሚጠቀሙ ፡ የንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ዴሞክራቶች ፡ እንጂ ፤ ጭራሹም ፡ ሶሺያሊስቶች ፡ እንዳልሆኑ (እኛ ፡ ቦልሼቪኮች* ፡ ሁሌ ፡ እንዳረጋገጥነው) ከሚያሳዩ ፡ ግልፅ ፡ ማስረጃዎች ፡ አንዱ ፡ በመንግሥት ፡ ላይ ፡ ያላቸው ፡ አስተሳሰብ ፡ ነው ።

በሌላ ፡ በኩል ፡ ደግሞ «የካውትስኪያውያን» ማርክሲዝምን ፡ ማጣመም ፡ ይበልጥ ፡ ረቀቅ ፡ ያለ ፡ ነው ። «በቴዎሪ ፡ ደረጃ» መንግሥት ፡ የመደብ ፡ ገዥነት (የገዥ ፡ መደብ) ድርጅት ፡ መሆኑንና ፡ የመደብ ፡ ቅራኔዎች ፡ የማይታረቁ ፡ መሆናቸውን ፡ ይቀበላሉ ። ነገር ፡ ግን ፡ የሚከተለው ፡ ሐሳብ ፡ ቸል ፡ ተብሏል ፡ ወይም ፡ ተድበስብሷል ፤

---

* ባሁኑ ፡ ጊዜ ፡ ኮሙኒስቶች ፡ ናቸው ።

ይኸውም ፡ መንግሥት ፡ ሊታረቁ ፡ የማይችሉ ፡ የመደብ ፡ ቅራኔዎች ፡ ውጤት ፡ መሆኑ ፡ ከታመነ ፤ መንግሥት ፡ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ በላይ ፡ ያለና «ከጊዜ ፡ ወደ ፡ ጊዜ ፡ ራሱን ፡ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ያገለለ» ኃይል ፡ ከሆነ ፤ ጭቁኑ ፡ መደብ ፡ ነፃ ፡ ሊወጣ ፡ የሚችለው ፡ በአመፃዊ ፡ አብዮት ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ ገዥው ፡ መደብ ፡ የመሰረተውንና «ገለልተኛነቱ» የተገለፀበትን ፡ የመንግሥቱ ፡ ሥልጣን ፡ አውታሮችን ፡ በማፍረስ ፡ ጭምር ፡ እንደሆነ ፡ ግልፅ ፡ ነው ። ማርክስ ፤ ከዚህ ፡ በታች ፡ እንደምናየው ፡ ይህንን ፡ በንድፈ-ሃሳብ ፡ ይዘቱ ፡ ግልፅ ፡ የሆነውን ፡ የማያወላዳ ፡ መደምደምያ ፡ ያደረገው ፡ ስለአብዮት ፡ ተግባሮች ፡ በተጨበጠ ፡ ታሪካዊ ፡ ትንተና ፡ ተመስርቶ ፡ ነው ። ከዚህ ፡ ቀጥለን ፡ በሰፊው ፡ እንደምናቀርበው ፡ ሁሉ ... ይህንን ፡ መደምደምያን ፡ ነው ፡ ካውትስኪይ «የረሳው» እና ፡ ያጣመመው ።

## ፪. ልዩ ፡ የታጠቁ ፡ ሰዎች ፡ ድርጅቶች ፤ እስር ፡ ቤቶች ... ወዘተ ።

ኤንግልስ ፡ በመቀጠል ፤ « ... ከአሮጌው ፡ የጋርዮሽ (የዘር ፡ ወይም ፡ የጐሳ)ሥርዓት ፡[6] ጋር ፡ ሲነፃፀር ፤ መንግሥት ፡ አንደኛ ፡ ልዩ ፡ ጠባዩ ፡ ተገዥዎቹን ፡ በክልሉ ፡ መሠረት ፡ መከፋፈል ፡ ነው ።»

ይህ ፡ መከፋፈል «የተፈጥሮ» ሊመስለን ፡ ይችላል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከአሮጌው ፡ ሥርዓት ፡ ጋር ፡ በትውልድ ፡ ወይም ፡ በዘር ፡ በተደረገው ፡ የረጅም ፡ ጊዜ ፡ ትግል ፡ ውጤት ፡ ነው ።

« ... ሁለተኛው ፡ ልዩ ፡ ባህርይ — ከምልዓተ ፡ ሕዝቡ ፡ ጋር ፡ ቀጥታ ፡ የማይጣጣም ፤ ራሱን ፡ እንደ ጦር ፡ ኃይል ፡ ያደራጀ ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ሥልጣንን ፡ መገንባት [illegible] ፡ ሥልጣን ፡ የሚ



ያስፈልግበት ፡ ምክንያት ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ወደ ፡ መደቦች ፡ ከተከፈለበት ፡ ጊዜ ፡ ጀምሮ ፡ የምልዓተ ፡ ሕዝቡ ፡ በራሱ ፡ የሚካሄድ ፡ የጦር ፡ ድርጅት ፡ ሊኖር ፡ ባለመቻሉ ፡ ነው ... ስለሆነም ፡ ይህ ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ሥልጣን ፡ በማንኛው ፡ መንግሥት ፡ ይገኛል ። በውስጡም ፡ የታጠቁ ፡ ሰዎች ፡ ብቻ ፡ ሳይሆኑ ፤ የጋርዮሽ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ የማያውቃቸው ፤ መሣርያዊ ፡ ተቀጥያዎች ፤ እስር ፡ ቤቶችና ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ የማስገደጃ ፡ ድርጅቶችም ፡ ይገኙበታል... »

ኤንግልስ ፡ በጉልህ ፡ ያብራራው ፡ ያ ፡ መንግሥት ፡ የተባለውን «ኃይልን» ነው ፤ ያ ፡ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ የመነጨ ፡ ኃይል ፡ ግን ፡ ራሱን ፡ በኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ላይ ፡ ያስቀመጠውና ፡ ከጊዜ ፡ ወደ ፡ ጊዜ ፡ ራሱን ፡ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ያገለለው ። ይህ ፡ ኃይል ፡ በመሠረቱ ፡ ምን ፡ አለው? ይህ ፡ ኃይል ፡ በቁጥጥራቸው ፡ ሥር ፡ እስር ፡ ቤቶችን ፡ ወዘተ ፤ ያሏቸው ፡ ልዩ ፡ የታጠቁ ፡ ሰዎች ፡ ድርጅቶች ፡ አሉት ።

ስለነዚህ ፡ ልዩ ፡ የታጠቁ ፡ ሰዎች ፡ ድርጅቶች ፡ ለመናገር ፡ እንችላለን ፤ ምክንያቱም ፡ የማንኛውም ፡ መንግሥት ፡ መታወቂያ ፡ ጠባይ ፡ የሆነው ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ሥልጣን ፡ ከታጠቀ ፡ ምልአተ ፡ ሕዝብና «በራሱ ፡ ከሚካሄድ ፡ የጦር ፡ ድርጅት ፡ ጋር» «ቀጥታ ፡ አይጣጣምምና ።»

እንደ ፡ ሁሉም ፡ ታላላቅ ፡ አብዮታዊ ፡ ተመራማሪዎች ፡ ኤንግልስም ፡ ጥረት ፡ የሚያደርገው ፤ ያንሰራራው ፡ ጮርቃነት ፡ ምንም ፡ ዋጋ ፡ እንደሌለው ፡ አድርጎ ፡ የሚመለከተውን ፤ በጣም ፡ ከልምድ ፡ እንደመጣ ፡ በአጉል ፡ እምነት ፡ ላይ ፡ በመመሥረት ፡ ሥር ፡ የሰደደ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ እንደሚሉት ፡ እንደአለት ፡ የጠነከረውን ፡ ጉዳይ ፡ ንቁ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ በግልጽ ፡ እንዲያዩት ፡ ነው ። ቋሚ ፡ ጦር ፡ ሠራዊትና ፡ ፖሊስ ፡ የመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ ዋና ፡ መሣሪያዎች ፡ ናቸው ። ለመሆኑ ፡ ከነዚህ ፡ የተለየ ፡ ሌላ ፡ ሊሆን ፡ ይችላል ፡ እንዴ?

እርግጥ ፡ ኤንግልስ ፡ ለሚናገራቸው ፤ ለአብዛኞቹ ፡ የአስራ ፡ ዘጠነኛው ፡ ክፍለ ፡ ዘመን ፡ መጨረሻ ፡ በአንድም ፡ ትልቅ ፡ አብዮት ፡ ላልተካፈሉ ፡ ወይንም ፡ ቀረብ ፡ ብለው ፡ ላልተመለከቱ ፡ ሰፊ ፡ አውሮፓውያን ፡ ከዚህ ፡ ሌላ ፡ ሊሆን ፡ አይችልም ። «የምልአተ ፡ ሕዝቡ ፡ በራሱ ፡ የሚካሄድ ፡ የጦር ፡ ድርጅት» ምን ፡ እንደሆነ ፡ ለነሱ ፡ በፍጹም ፡ አይገባቸውም ። ታድያ ፡ ራሳቸውን ፡ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ በላይ ፡ ያስቀመጡና ፡ ራሳቸውን ፡ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ያገለሉ ፡ ልዩ ፡ የታጠቁ ፡ ሰዎች ፡ ድርጅቶች (ፖሊስ ፤ ቋሚ ፡ ሠራዊት) ለምን ፡ አስፈለጉ ፡ ተብለው ፡ የምዕራብ ፡ አውሮፓና ፡ የሩሲያ ፡ ጮርቃዎች ፡ ሲጠየቁ ፡ ከስፐንሰር ፡ ወይም ፡ ከሚኻይሎቭስኪይ ፡ ጥቂት ፡ ሐረጎችን ፡ በመዋስ ፤ የኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ኑሮ ፡ ውስብስብነትን ፡ የተግባር ፡ መለያየትንና ፡ የመሳሰሉትን ፡ በመጠቃቀስ ፡ ለመመለስ ፡ ይሞክራሉ ።

የዚህ ፡ ዓይነቱ ፡ ጥቅስ «ሳይንሳዊ» ይመስላል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ዋናና ፡ መሠረታዊውን ፡ ማለትም ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ወደማይታረቁ ፡ ተፃራሪ ፡ መደቦች ፡ መከፈሉን ፡ በማድበስበስ ፡ ተራውን ፡ ሰው ፡ ሥራዬ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ያዳክማሉ ።

ይህ ፡ መከፈል ፡ ባይኖር ፡ ኖሮ «የምልዓተ ፡ ሕዝቡ ፡ በራሱ ፡ የሚካሄድ ፡ የጦር ፡ ድርጅት» ከጥንታዊው ፡ ባለ ፡ አርጩሜው ፡ የዝንጀሮ ፡ መንጋዎች ፡ ወይንም ፡ ከሥልጣኔ ፡ በፊት ፡ የነበሩ ፡ ሰዎች ፡ ወይንም ፡ በጐሳ ፡ ከተባበሩት ፡ ሰዎች ፡ ማኅበር ፤ በውስብስብነቱ ፤ በከፍተኛ ፡ የቴክኒክ ፡ ደረጃው ... ወዘተ ፡ በተለየ ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የዚህ ፡ ዓይነት ፡ ድርጅትም ፡ በተቻለ ፡ ነበር ።

ይህ ፡ አይቻልም ፤ ምክንያቱም ፡ የሠለጠነው ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ወደ ፡ ተፃራሪ ፤ እንዲያውም ፡ ወደማይታረቁ ፡ ተፃራሪ ፡ መደቦች ፡ ተከፍሏልና ፤ የነዚህም «በራሱ ፡ የሚካሄድ» የጦር ፡ ትጥቅ ፡ መኖር ፡ ወደ ፡ ጦር ፡ ሊያመራቸው ፡ ይችላል። መንግሥት ፡ ይቋቋማል ፤ [illegible] ፤ ልዩ ፡ የታጠቁ ፡ ሰዎች ፡ ድርጅቶች ፡ ይፈጠራሉ ፤ ስለዚህም ፡ ማንኛውም ፡ አብዮት ፡ የመንግሥት ፡ አውታሮችን ፡ በማፍረስ ፡ የመደብ ፡ ትግል ፡ እርቃነ ፡ ሥጋውን ፡ ያሳየናል ፤ ይኸውም ፡ የገዢው ፡ መደብ ፡ እሱን ፡ የሚያገለግሉትን ፡ ልዩ ፡ የታጠቁ ፡ ሰዎች ፡ ድርጅቶችን ፡ ለመጠገን ፡ እንዴት ፡ እንደሚጣጣር ፤ በአንፃሩም ፡ ጭቁኑ ፡ መደብ ፡ በዝባዦችን ፡ ሳይሆን ፡ ተበዝባዦችን ፡ ሊያገለግል ፡ የሚችል ፡ አዲስ ፡ የዚህን ፡ ዓይነት ፡ ድርጅት ፡ ለመመሥረት ፡ እንዴት ፡ እንደሚጣጣር ፡ በግልጽ ፡ ያሳየናል ።

ከዚህ ፡ በላይ ፡ ኤንግልስ ፡ በቴዎሪ ፡ መሠረት ፡ ያቀረበው ፡ ሀሳብ ፤ ማንኛውም ፡ ታላቅ ፡ አብዮት ፡ ከፊታችን ፡ የሚደቅነውን ፡ ገቢራዊ ፤ ግልጽና ፡ አልፎም ፡ ከፍተኛ ፡ ድርጊት ፡ የሚያስፈልገውን ፡ ጥያቄ ፡ ነው ። ይኸውም «በልዩ» የታጠቁ ፡ ሰዎች ፡ ድርጅቶችና «በራሱ ፡ በሚካሄደው ፡ የምልዓተ ፡ ሕዝቡ ፡ የትጥቅ ፡ ድርጅቶች» መካከል ፡ ያለው ፡ ግንኙነትን ፡ ነው ። የአውሮፓና ፡ የሩሲያ ፡ አብዮቶች ፡ ልምምዶች ፡ ይህን ፡ ጥያቄ ፡ በተጨበጠ ፡ እንዴት ፡ ግልጽ ፡ እንዳደረጉት ፡ እናያለን ።

ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ኤንግልስ ፡ ገለጻ ፡ እንመለስ ።

እሱ ፡ እንደሚያመለከተው ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፤ ለምሳሌ ፡ ባንዳንድ ፡ የሰሜን ፡ አሜሪካ ፡ ክፍሎች ፡ ይህ ፡ የማኅበረ ፡ ሰብ ፡ ሥልጣን ፡ ደካማ ፡ ነው ። (እሱ ፡ የሚያወሳው ፡ በካፒታሊስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ አልፎ ፡ አልፎ ፡ ሊሆን ፡ ስለሚችለው ፡ ሁኔታና ፡ እንዲሁም ፡ በሰሜን ፡ አሜሪካ ፡ ክፍሎች ፡ ነፃ ፡ ሰፋሪ ፡ ላቅ ፡ ባለበት ፡ በቅድመ ፡ ኢምፔሪያሊዝም ፡ ወቅቱ ፡ ነው) ነገር ፡ ግን ፡ ባጠቃላይ ፡ ሲታይ ፡ በመጠንከር ፡ ላይ ፡ ነው ።

« ... በመንግሥት ፡ ውስጥ ፡ ያሉ ፡ የመደብ ፡ ቅራኔዎች ፡ በከረሩ ፡ መጠን ፤ የሚዋሰኑ ፡ መንግሥታት ፡ ስፋት ፡ ባበጀና ፡ የምልአተ ፡ ሕዝቡ ፡ ቁጥር ፡ በጨመረ ፡

መጠን ፡ የማኅበረ ፡ ሰብ ፡ ሥልጣን ፡ ይበልጥ ፡ ይጠንከራል ። ሌላ ፡ ቢቀር ፡ ማኅበራዊ ፡ ሥልጣን ፡ በመደብ ፡ ትግልና ፡ የወረራ ፡ ውድድር ፡ ተወጥሮ ፡ መላ ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡንና ፡ እንዲያውም ፡ መንግሥትንም ፡ ጭምር ፡ ለመዋጥ ፡ ማስፈራራት ፡ ደረጃ ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ የዛሬይቱን ፡ አውሮፓ ፡ ሁኔታ ፡ እንኳ ፡ እንመልከት ...»

ይህ ፡ የተጻፈው ፡ ባለፈው ፡ መቶ ፡ ዓመት ፡ በ ፺ኛዎቹ ፡ ዓመታት ፡ መጀመሪያ ፡ ላይ ፡ ነው ። የኤንግልስ ፡ የመጨረሻ ፡ መቅድም ፡ የተጻፈው ፡ በሰኔ ፡ ፲፯ ቀን ፡ ፲፰፻፺፭ ዓ. ም. ነው ። ይህም ፡ ወደ ፡ ኢምፔሪያሊዝም ፡ መሸጋገሪያ ፡ ማለትም ፡ ሙሉ ፡ የትሬስቶች ፡ የበላይነት ፡ መያዝ ፤ የታላላቅ ፡ ባንኮች ፡ ማንሰራራት ፤ ከፍተኛ ፡ የቅኝ ፡ ግዛት ፡ ፖለቲካ ፡ መስፋፋትና ፡ የመሳሰሉት ፡ በፈረንሳይ ፡ ገና ፡ በጀመረበት ፤ በሰሜን ፡ አሜሪካና ፡ በጀርመንም ፡ ገና ፡ ደካማ ፡ በነበረበት ፡ ዘመን ፡ ነው ። ከዚያ ፡ ጊዜ ፡ ጀምሮ «የወረራ ፡ ውድድር» ወደፊት ፡ በጣም ፡ ትልቅ ፡ እርምጃ ፡ አደረገ ፤ እንዲያውም ፡ በሃያኛው ፡ ምዕት ፡ ዓመት ፡ ፳ ኛ ዎቹ ፡ ዓመታት ፡ ዓለም ፡ በነዚህ «ተወዳዳሪ ፡ ወራሪዎች» መካከል ፡ ፍጹም ፡ ተከፍላ ፡ ነበር ፤ ማለትም ፡ በታላላቅ ፡ ዘራፊ ፡ መንግሥታት ፡ መካከል ። ከዚያ ፡ ጊዜ ፡ ጀምሮ ፡ የጦርና ፡ የባሕር ፡ ትጥቅ ፡ በሚያስደንቅ ፡ አኳኋን ፡ አድጓል ፤ እንግሊዝ ፡ ወይም ፡ ጀርመን ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ የበላይ ፡ ለመሆን ፤ ቅኝ ፡ ግዛቶችን ፡ ለመከፋፈል ፡ ያደረጉት ፡ የ፲፱፻፲፬-፲፱፻፲፰ ዓ. ም. የዘረፋ ፡ ጦርነት ፡ ሁሉም ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ኃይሎች ፡ በዘራፊው ፡ የመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ ውስጥ «መዋጥ» ወደፍጹም ፡ መቅሰፍት ፡ አስጠግቶታል ።

ኤንግልስ ፡ ገና ፡ በ ፲፰፻፺፭ ዓ. ም. «የወረራዎች ፡ ውድድር» የኃያላን ፡ መንግሥታት ፡ የውጭ ፡ ፖለቲካ ፡ ዓይነተኛ ፡ ልዩ ፡ ባህርይ ፡ መሆኑን ፡ አመልክቷል ፤ ወስላታ ፡



ሶሺያል-ሾቪኒስቶች ፡ ግን ፡ በ ፲፱፻፲፬-፲፱፻፲፰ ዓመታት ፡ ልክ ፡ ይህ ፡ ውድድር ፡ ከመቸውም ፡ ጊዜ ፡ በጣም ፡ ተፋፍሞ ፡ የኢምፔሪያሊስት ፡ ጦርነትን ፡ በወለደበት ፡ ጊዜ «የራሳቸውን» ቡርዥዋ ፡ የዘረፋ ፡ ጥቅም ፡ ለማስጠበቅ ፡ እንደሽፋን ፡ የተጠቀሙባቸው ፡ ሐረጎች «የእናት ፡ አገርን ፡ መከላከል!» ፤ «ሪፑብሊኩንና ፡ አብዮቱን ፡ መከላከል!» ... ወዘተ ፡ ናቸው ።

## ፫. መንግሥት ፡ ጭቁን ፡ መደብን ፡ የመበዝበዣ ፡ መሣሪያ ፡ ነው ።

ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ በላይ ፡ ያለው ፡ ልዩ ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ኃይል ፡ ለህልውናውን ፡ ግብር ፤ የመንግሥት ፡ ብድሮች ፡ ያስፈልጉታል ።

« ... የኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ሥልጣንን ፡ በመያዝና ፡ ግብር ፡ የመዝረፍ ፡ መብትን ፡ በማግኘት» ይላል ፡ ኤንግልስ «የኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ አካሎች ፡ የሆኑት ፡ ባለሥልጣኖች ፡ አሁን ፡ ግን ፡ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ በላይ ፡ ይሆናሉ ። ሊያገኙት ፡ ቢችሉ ፡ ኖሮ ፡ እንኳ ፤ ለጐሳ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ድርጅቶች ፡ ይሰጥ ፡ የነበረው ፡ ነፃና ፡ ፈቃዳዊ ፡ አክብሮት ፡ አሁን ፡ አያረካቸውም ፡ ነበር ... » ባለሥልጣኖችን ፡ ቅዱስና ፡ የማይነኩ ፡ የሚያደርጉ ፡ ልዩ ፡ ሕጎች ፡ ይወጣሉ ። ከጐሳ ፡ ተጠሪ ፡ ይልቅ «እጅግ ፡ ውዳቂ ፡ የሆነው ፡ የፖሊስ ፡ አገልጋይ» ይበልጥ «ሥልጣን» አለው ። ነገር ፡ ግን ፡ የሠለጠነው ፡ መንግሥት ፡ የጦር ፡ ኃይል ፡ አዛዥ ፡ እንኳ ፡ ሳይቀር ፡ ለጐሳው ፡ መሪ ፡ ሕዝበ ፡ ማኅበሩ ፡ ባለው «ፈቃዳዊ ፡ አክብሮት» ሳይቀናበት ፡ አይቀርም ።

ከዚህ ፡ በላይ ፡ የመንግሥት ፡ ባለሥልጣኖች ፡ እንዴት ፡

ልዩ ፡ መብት ፡ ያለው ፡ ቦታ ፡ እንዳላቸው ፡ ተጠቅሷል ። የተጠቀሰው ፡ ዋና ፡ ነጥብ ፤ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ በላይ ፡ የሚያስቀምጣቸው ፡ ነገር ፡ ምንድነው? ይህ ፡ የቴዎሪ ፡ ጥያቄ ፡ እንዴት ፡ በፓሪስ ፡ ኮሙን ፡ በ ፲፰፻፸፩ ዓ. ም. በገቢር ፡ እንደተፈታና ፡ እንዴት ፡ በካውትስኪይ ፡ በ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. እንደተድበሰበሰ ፡ እናያለን ።

« … መንግሥት ፡ የተመሠረተው ፡ የመደቦች ፡ ቅራኔን ፡ ለመቆጣጠር ፡ በማስፈለጉ ፡ ስለሆነ ፤ እንደዚሁም ፡ የፈለቀው ፡ በነዚህ ፡ መደቦች ፡ ግጭት ፡ ምክንያት ፡ ነው ፤ በመሠረቱም ፡ መንግሥት ፡ በጣም ፡ ኃይለኛ ፡ የሆነውና ፡ በኤኮኖሚ ፡ የበላይነት ፡ ያለው ፡ መደብ ፡ ሲሆን ፡ በመንግሥቱም ፡ አማካኝነት ፡ መደቡ ፡ በፖለቲካ ፡ የበላይ ፡ ይሆናል ። በዚህም ፡ መሠረት ፡ የተጨቆነውን ፡ መደብ ፡ ለማዳፈንና ፡ ለመበዝበዝ ፡ አዲስ ፡ መሣርያ ፡ ያገኛል …» የጥንትና ፡ የፊውዳል ፡ መንግሥታት ፡ ባርያዎችንና ፡ ጭሰኞችን ፡ የበዘበዙባቸው ፡ ድርጅቶች ፡ እንደነበሩ ፡ ሁሉ ፤ «ዘመናዊው ፡ የውክልና ፡ መንግሥትም ፡ ቅጥር ፡ ጉልበትን ፡ በካፒታል ፡ የሚበዘብዝበት ፡ መሣሪያ ፡ ነው ። ቢሆንም ፡ ልዩ ፡ ሁኔታ ፡ በሚያጋጥምበት ፡ ወቅት ፡ በመዋጋት ፡ ላይ ፡ ያሉ ፡ ተፃራሪ ፡ መደቦች ፡ ኃይላቸው ፡ ተመጣጣኝ ፡ በሚሆንበት ፡ ጊዜ ፡ የመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ ለጊዜው ፡ በሁለቱም ፡ መደቦች ፡ አንፃር ፤ በመካከላቸው ፡ እንዳለ ፡ አስታራቂ ፡ ይመስል ፡ ራሱን ፡ የቻለ ፡ ይሆናል …» የአስራ ፡ ሰባተኛውና ፡ የአስራ ፡ ስምንተኛው ፡ ክፍለ ፡ ዘመን ፡ ፍጹም ፡ ንጉሣዊ ፡ አገዛዝ ፤ በፈረንሳይ ፡ የመጀመሪያውና ፡ ሁለተኛው ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ግዛት ፡ የነበረው ፡ ቦናፓርቲዝም ፤ ቢስማርክ ፡ በጀርመን ፡ የዚህ ፡ ዓይነት ፡ ነበሩ ። [illegible] ዘራባችን ፡ እንጨመ[illegible]ንውስ ፡ ቡርዥዋ ፡ መሪ



ነት ፡ ምክንያት ፡ ሶቪዬቶች (የወዝ ፡ አደር ፡ ኮሚቴዎች) ቀድሞ ፡ በተዳከሙበት ፤ ግን ፡ ቡርዥዋውም ፡ ቢሆን ፡ ቀጥታ ፡ እንዳይበታትናቸው ፡ ገና ፡ ኃይል ፡ ባነሰበት ፡ ወቅት ፤ አብዮታዊውን ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ማሳደድ ፡ በመጀመሩ ፡ የሪፑብሊካዊትም ፡ ሩሲያ ፡ የኬሬንስኪይ ፡ መንግሥትም ፡ የነዚህ ፡ ዓይነት ፡ ነው ።

ኤንግልስ ፡ ይቀጥልና «የዴሞክራቲክ ፡ ሪፑብሊክ ፡ ኃብት ፡ በተዘዋዋሪ ፡ ቢሆንም ፡ በልበ ፡ ሙሉነት ፡ ሥልጣኑን ፡ ይጠቀማል ። መጀመሪያ ፤ «ባለሥልጣኖችን ፡ ቀጥታ ፡ በጉቦ ፡ በመግዛት» አሜሪካ ፤ ሁለተኛ ፤ «መንግሥትና ፡ ዋጋ ፡ ያላቸው ፡ ሰነዶች ፡ መለዋወጫ ፡ ድርጅት ፡ በማስተባበር ። »(ፈረንሳይና ፡ አሜሪካ ።)

በአሁኑ ፡ ጊዜ ፡ ኢምፔሪያሊዝምና ፡ የባንኮች ፡ የበላይነት ፤ በማንኛውም ፡ ዴሞክራቲክ ፡ ሪፑብሊክ ፡ የሃብትን ፡ የበላይነት ፡ ለመደገፍና ፡ በሥራ ፡ ላይ ፡ ለማዋል ፤ እነዚህን ፡ ሁለት ፡ መንገዶች ፡ ወደ ፡ ልዩ ፡ ጥበብ «አሳድጓቸዋል» ። ለምሳሌ ፡ ለመጀመሪያው ፡ የሩሲያ ፡ ዴሞክራቲክ ፡ ሪፑብሊክ ፡ ወሮች «የሶሺያሊስት-አብዮታውያን[4]» እና ፡ ሜንሼቪኮች ፡[5] ከቡርዥዋው ፡ ጋር ፡ ተጋብተው ፡ በትብብሩ ፡ መንግሥት ፡ በገቡበት ፡ የጫጉላ ፡ ጊዜ ፡ ፓልቺንስኪይ ፡ ካፒታሊስቶችን ፤ ቀማኞችን ፤ ለጦርነት ፡ ያገሪቱን ፡ ባጀት ፡ የሚዘርፉት ፡ ለመቆጣጠር ፡ የተደረገውን ፡ ሙከራ ፡ አደናቀፈ ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ከካቢኔው ፡ የለቀቀው ፡ ፓልቺንስኪይ (አዎን ፤ በሌላ ፡ ፓልቺንስኪይ ፡ የተለወጠው) በካፒታሊስቶች ፡ ደመወዙ ፡ በዓመት ፡ ፻፳ ሺህ ፡ ሩብል ፡ የሆነ ፡ የሥራ ፡ ቦታ «ተሸለመ» — ይህ ፡ ምን ፡ ተብሎ ፡ ሊጠራ ፡ ይቻላል? የመንግሥትና ፡ የሲ ቀጥተኛ ፡ ወይስ ፡ የስውር ፡ ጉቦ?

ንዲኬትስ ፡ ትብብር ፡ ነው ፡ ወይስ ፡ ጓደኝነት «ብቻ»?
እነቼርኖቭና ፡ ጸረተሊ ፤ እነአቭክሴንትዬቭና ፡ ስኮቤሌቭ ፡
የሚጫወቱት ፡ ሚና ፡ ምንድነው? የሚሊዮኔሮች ፡ ዘራፊ
ዎች «ቀጥተኛ» ሽርኮች ፡ ናቸው ፡ ወይስ ፡ በስውር ፡
ብቻ ፡ ነው?

የሃብት ፡ የበላይነት ፡ በዴሞክራቲክ ፡ ሪፑብሊክ ፡
ይበልጥ ፡ ነጻ ፡ የሆነበት ፡ ምክንያት ፡ በአንዳንድ ፡ የፖለ
ቲካው ፡ መኪና ፡ ጉድለቶች ፤ ወይንም ፡ በካፒታሊዝም ፡
መጥፎ ፡ የፖለቲካ ፡ ሽፋን ፡ ስለማይወሰን ፡ ነው ። ዴሞክ
ራቲክ ፡ ሪፑብሊክ ፡ የካፒታሊዝም ፡ ተወዳዳሪ ፡ የሌለው ፡
ሽፋን ፡ ነው ፤ ስለዚህም ፡ ካፒታሊዝም ፡ ይህንን ፡ ተወ
ዳዳሪ ፡ የሌለው ፡ ሽፋን ፡(በነፓልቺንስኪይ ፤ ቼርኖቭ ፤
ጸረተሊና ፡ መሰሎቻቸው ፡ በኩል) ለማግኘት ፡ በማያሰ
ጋና ፡ በልበ ፡ ሙሉነት ፡ ሥልጣኑን ፡ ያቋቁማል ፤ ከዚያም ፡
በቡርዥዋ ፡ ዴሞክራቲክ ፡ ሪፑብሊክ ፡ ውስጥ ፡ ያፈለገው ፡
የሰዎች ፤ የድርጅቶችና ፡ የፓርቲዎች ፡ መለዋወጥ ፡ ቢደ
ረግ ፡ ሥልጣኑን ፡ አያነቃንቀውም ።

ኤንግልስ ፡ ከትልቅ ፡ እምነት ፡ ጋር ፡ አጠቃላይ ፡
የምርጫ ፡ መብትን ፡ የቡርዥዋው ፡ ገዥነት ፡ መሣሪያ ፡
ነው ፡ ብሎ ፡ እንደሚጠራው ፡ መጥቀስ ፡ ያስፈልጋል ።
የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ ልምምድን ፡ በትክክል ፡
በማስተዋል ፤ አጠቃላይ ፡ የምርጫ ፡ መብት ፤ ይላል ፡ ኤን
ግልስ ፤ «የወዝ ፡ አደሩን ፡ መደብ ፡ ብስለት ፡ መለኪያ ፡
ምልክት ፡ ነው ። ከዚህ ፡ ሌላ ፡ ባሁኑኛው ፡ ዓይነት ፡ መንግ
ሥት ፡ ምንም ፡ ሊሰጥ ፡ አይችልም ፤ ምንጊዜም ፡ አይሰ
ጥም ።»

ንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ዴሞክራቶች ፤ እንደየኛዎቹ ፡ ሶሺያ
ሊስት-አብዮታውያንና ፡ ሜንሼቪኮች ፤ እንደዚሁም ፡ የነሱ ፡
መንትያ ፡ ወንድሞቻቸው ፡ የምዕራብ ፡ አውሮፓ ፡ ሶሺ
ያል-ሾቪኒስቶችና ፡ አድርባዮች ፡ ከአጠቃላይ ፡ የምርጫ ፡
መብት [illegible] ዓይነት ፡ መን






ግሥት» በአጠቃላይ ፡ የምርጫ ፡ መብት ፡ በእርግጥ ፡ የሰ
ፊው ፡ ሠርቶ ፡ አደር ፡ሕዝብ ፡ ፍላጎት ፡ ለመግለጽና ፡ ይህንን
ም ፡ በተግባር ፡ መዋሉን ፡ ለማረጋገጥ ፡ የሚቻል ፡ ይመ
ስል ፤ እነሱ ፡ ራሳቸው ፡ ተሳስተው ፤ በሕዝቡ ፡ አንጎል ፡
ውስጥ ፡ የማይሆነውን ፡ ስሕተተኛ ፡ ሐሳብ ፡ ይቀርጻሉ ።

እዚህ ፡ ላይ ፡ ይህ ፡ ስሕተተኛ ፡ ሐሣብን ፡ ብቻ ፡ እን
ጠቅሳለን ፤ «ህጋዊ» (ማለት ፡ አድርባይ) ሶሺያሊስት ፡
ፓርቲዎች ፡ በየደረጃው ፡ በፕሮፓጋንዳና ፡ በቅስቀሳ ፡ የኤ
ንግልስን ፡ ፍጹም ፡ ግልፅ ፤ ትክክለኛና ፡ የተጨበጠ ፡
መግለጫ ፡ እንዳጣመሙት ፡ እንጠቁማለን ። ስለዚህ ፡ ኤንግ
ልስም ፡ ወደጎን ፡ ስለሚጥለው ፡ ሐሳብ ፡ ስሕተተኛነት ፤
ማርክስና ፡ ኤንግልስ ፡ «ስለአሁኑኛው» መንግሥት ፡ ያላቸ
ውን ፡ ርዕዮት ፡ ጨምረን ፡ ዝርዝር ፡ ገለፃ ፡ እናቀርባለን ።

ኤንግልስ ፡ ርዕዮቱን ፤ በጣም ፡ በታወቀው ፡ ጽሑፉ ፡
ውስጥ ፤ በሚከተሉት ፡ ቃላት ፡ አጠቃላይ ፡ አጭር ፡ መግ
ለጫ ፡ ይሰጣል ።

«መንግሥት ፡ ዘለዓለማዊ ፡ አይደለም ። ስለመንግ
ሥትና ፡ መንግሥታዊ ፡ ሥልጣን ፡ ምንም ፡ የማያውቁ ፤
መንግሥት ፡ ያልነበራቸው ፡ ኅብረተ ፡ ሰቦች ፡ ነበሩ ።
ከተወሰነ ፡ የኤኮኖሚ ፡ የዕድገት ፡ ደረጃ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡
ኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ወደ ፡ መደቦች ፡ በመከፈሉ ፡ ምክንያት ፡
መንግሥት ፡ አስፈላጊ ፡ ሆነ ። እኛ ፡ አሁን ፡ በታላቅ ፡
ፍጥነት ፡ እምንቃረበው ፡ ያለን ፡ የምርት ፡ ዕድገት ፡
ደረጃ ፡ የሚያሳየን ፡ የመደቦችን ፡ መኖር ፡ አለማስፈ
ለጉን ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፤ ለምርትም ፡ ቀጥታ ፡ እንቅፋት ፡
እንደሆኑ ፡ ነው ። መደቦች ፡ ባለፈው ፡ የግድ ፡ እን
ደተፈጠሩ ፡ ሁሉ ፡ የግድም ፡ ይጠፋሉ ። መደቦች ፡
ሲጠፉ ፡ መንግሥትም ፡ የግድ ፡ ይጠፋል ። ነፃና ፡ እኩል ፡
በሆኑ ፡ አምራች ፡ ማኅበራት ፡ ተመሥርቶ ፡ ምርትን ፡
በአዲስ ፡ መልክ ፡ የሚያደራጅ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፤ የመን

ግሥት ፡ መኪናን ፡ እንዳለ ፡ ወደሚገባው ፡ ቦታ ፡ ወደ ፡
የጥንት ፡ ታሪክ ፡ ቤተ ፡ መዘክር ፡ ይወረውራል ፤
ከፈታይ ፡ መዘውና ፡ ከነሐስ ፡ መጥረቢያ ፡ ጐን ፡
ያስቀምጠዋል ።»

በአሁኖቹ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ የፕሮፓጋንዳና ፡
የቅስቀሳ ፡ ጽሑፎች ፡ ይኸን ፡ ጥቅስ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ አይገ
ኝም ። ቢገኝም ፡ እንኳ ፡ ሲጠቅሱት ፡ ለመለኮት ፡ እንደ
ሚሰግዱ ፡ ሆኖ ፡ ነው ፡ ማለትም ፡ የሚደረገው ፡ ለኤንግልስ ፡
ሕጋዊ ፡ ክብር ፡ ተብሎ ፡ ነው ፤ ነገር ፡ ግን «የመንግሥት ፡
መኪናን ፡ እንዳለ ፡ ወደ ፡ ጥንት ፡ ታሪክ ፡ ቤተ ፡ መዘክር ፡
ለማስገባት» ምን ፡ ያህል ፡ ስፋትና ፡ ጥልቀት ፡ ያለው ፡ አብ
ዮት ፡ እንደሚያስፈልገው ፡ አይመረመርም ። እንዲያውም ፡
በብዙ ፡ ቦታዎች ፡ ኤንግልስ ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ የሚ
ለው ፡ እንኳ ፡ ምን ፡ እንደሆነ ፡ አይጠቀስም ።

## ፬. የመንግሥት «መክሰም» እና ፡ አመፃዊ ፡ አብዮት ።

የመንግሥት «መክሰም» የሚባሉት ፡ የኤንግልስ ፡
ቃላት ፡ በጣም ፡ በሰፊው ፡ የታወቁ ፡ በመሆናቸው ፡ ብዙ
ውን ፡ ጊዜ ፡ ይጠቀሳሉ ፤ እንደዚሁም ፡ የተለመደውን ፡
ማርክሲዝምን ፡ ወደ ፡ አድርባይነት ፡ የማጣመም ፡ ንጥረ-
ሃሳብን ፡ በግልጽ ፡ ያሳያሉ ፤ ስለዚህም ፡ በሰፊው ፡ እንመለ
ከታቸዋለን ። ከተወሰዱበት ፡ ሁሉም ፡ መግለጫዎች ፡ እን
ጠቅሳለን ።

«ወዝ ፡ አደሩ ፡ የመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ ይወስድና ፡
የምርት ፡ መገልገያዎችን ፡ በመጀመሪያ ፡ ደረጃ ፡ የመ
ንግሥት ፡ ያደርጋል ። በዚህም ፡ ምክንያት ፡ ራሱ ፡ ወዝ ፡





አደር ፡ መሆኑን ፡ ያስወግዳል ፤ ሁሉም ፡ የመደብ ፡
ልዩነቶችንና ፡ የመደብ ፡ ቅራኔዎችን ፡ ያጠፋል ፤
ከዚህም ፡ ጋር ፡ አብሮ ፡ የመንግሥቱን ፡ መንግሥት
ነት ፡ ያጠፋል ። በመደባዊ ፡ ቅራኔዎች ፡ ለሚንቀሳ
ቀሰው ፤ ለነበረውና ፡ እስካሁንም ፡ ላለው ፤ ኅብረተ ፡
ሰብ ፡ መንግሥት ፡ አስፈላጊ ፡ ነበር ፤ ማለትም ፡ የውጭ ፡
የምርት ፡ ሁኔታዎችን ፡ ለማኖር ፤ በተለይም ፡ ተበዝባ
ዡን ፡ መደብን ፡ በኃይል ፡ በመጨቆን ፡ ባለው ፡ ሥልተ ፡
ምርት ፡ በሚገኙት ፡ በተወሰኑ ፡ ሁኔታዎች (ባርነት ፤
ጭሰኝነት ፤ ቅጥር ፡ ጉልበት) ለማኖር ፡ የሚያገለግል ፡
የበዝባዥ ፡ መደብ ፡ ድርጅት ፡ ነው ። መንግሥት ፡
የመላ ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ኦፊሻል ፡ ወኪል ፤ የዚሁ ፡ ክም
ችት ፡ የሚታይ ፡ ኩባንያ ፡ ነበር ። እንዲህ ፡ የሆነበትም ፡
ምክንያት ፡ መንግሥቱ ፤ ዘመኑ ፡ የራሱ ፡ ለነበረው ፤
መላ ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡን ፡ የሚወክል ፡ የአንድ ፡ መደብ ፡
በመሆኑ ፡ ነው ። በጥንት ፡ ዘመን ፡ የመንግሥቱ ፡ ዜጐ
ች ፡ የነበሩት ፤ የባርያ ፡ ገዥዎች ፡ መንግሥት ፡ ነበር ፤
በመካከለኛው ፡ ክፍለ ፡ ዘመን ፡ የፊውዳል ፡ መሣፍ
ንት ፡ መንግሥት ፡ ነበር ፤ በኛ ፡ ዘመን ፡ የቡርዥዋው ፡
ነው ። በመጨረሻ ፡ መንግሥት ፡ እውነተኛ ፡ የመላ ፡
ኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ወኪል ፡ በሚሆንበት ፡ ጊዜ ፡ ራሱ ፡
መንግሥት ፡ አስፈላጊነቱን ፡ ያጣል ። አንድም ፡ የኅ
ብረተ ፡ ሰቡ ፡ መደብ ፡ ጨቁኖ ፡ ለመያዝ ፡ ካላስፈለገ ፤
የገዥ ፡ መደብና ፡ እንዲሁም ፡ ባለው ፡ የምርት ፡ ሥር
ዓተ-አልበኝነት ፡ የተነሳ ፡ የሚደረገው ፡ ነጠላ ፡ ት
ግል ፡ ከጠፋ ፤ ከዚህም ፡ ትግል ፡ የሚመነጬት ፡ ግጭ
ቶችና ፡ ትርፎች ፡ ከቀሩ ፤ ተጨቁኖ ፡ የሚያዝ ፡ ምንም ፡
ነገር ፡ የለም ፤ ስለሆነም ፡ የመጨቆኛ ፡ ልዩ ፡ ኃይል ፡
ማለትም ፡ የመንግሥት ፡ አስፈላጊነት ፡ ይቀራል ።
መንግሥት ፡ እንደ ፡ ትክክለኛ ፡ የመላ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡
ወኪል ፡ የሚወስደው ፡ የመጀመሪያ ፡ እርምጃ —

በኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ስም ፡ የምርት ፡ መገልገያዎችን ፡ መውሰድ ፡ ነው ፡ እንደመንግሥት ፡ የሚያደርገው ፡ የመጨረሻ ፡ ነፃ ፡ እርምጃው ፡ ይህ ፡ ነው ። የመንግሥት ፡ በኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ግንኙነቶች ፡ ጣልቃ ፡ ገብነት ፡ ከቦታ ፡ ቦታ ፡ ትርፍ ፡ ነገር ፡ ይሆናል ፤ ይጠፋልም ። መንግሥት ፡ ሰዎችን ፡ መግዛቱ ፡ ቀርቶ ፡ ቆሳቊሶችን ፡ ያስተዳድራል ፤ የምርት ፡ ሂደትን ፡ ይመራል ። መንግሥት ፡ ይከስማል ፡ እንጂ «አይደመሰስም »። ይህን ፡ መሠረት ፡ በማድረግ «ነፃ ፡ ሕዝባዊ ፡ መንግሥት» የሚለውን ፡ ሐረግ ፡ ምንነት ፡ መመርመር ፤ ሐረጉ ፡ ለጊዜው ፡ ለመኖር ፡ ያህል ፡ የቅስቀሳ ፡ መብት ፡ ቢኖረውም ፡ ዞሮ ፡ ዞሮ ፡ ግን ፡ ሳይንሳዊ ፡ ደካማ ፡ መሆኑን ፡ መረዳት ፡ ያስፈልጋል ። እንደዚሁም ፡ ደግሞ ፡ ይህንን ፡ መሠረት ፡ በማድረግ ፡ ሥርዓተ-አልበኞች ፡ የሚባሉት ፡ የሚጠይቁትን ፡ በአንድ ፡ ሌሊት ፡ መንግሥት ፡ መደምሰስ ፡ አለበት ፡ የሚሉትንም ፡ መመርመር ፡ ያስፈልጋል ።» («አንቲ-ዱሪንግ።» «የአቶ ፡ የቨጌኒይ ፡ ዱሪንግ ፡ ሳይንስን ፡ መጻረር» ፫ኛው ፡ የጀርመን ፡ እትም ፤ ገጽ ፡ ፫፻፩-፫፻፫)

ከነዚህ ፡ ግሩም ፡ ከሆኑ ፡ ሐሳቦች ፡ ከተሞላው ፡ የኤንግልስ ፡ ገለፃ ፡ አንድ ፡ ነጥብ ፡ ብቻ ፡ በአሁኖቹ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ፓርቲዎች ፡ እርግጠኛ ፡ የማይነጠል ፡ ሶሺያሊስት ፡ ሐሳብ ፡ ሆኗል ፤ ይህም ፡ በማርክስ ፡ አነጋገር ፡ መንግሥት «የሚከስም» መሆኑን ፡ ነው ፤ ይህ ፡ መንግሥት «ይደመሰሳል» ከሚለው ፡ የሥርዓተ-አልበኞች ፡ ቴዎሪ ፡ የተለየ ፡ ነው ። ማርክሲዝም ፡ እንዲህ ፡ ከተጐራረደ ፡ ወደ ፡ አድርባይነት ፡ ወረደ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ምክንያቱም ፡ በዚህ ፡ ዓይነት «አባባል» የሚቀረው ፡ ደብዛዛ ፡ አስተሳሰብ ፡ ስለ ፡ ቀስተኛ ፤ አዝጋሚና ፡ ቀስ ፡ በቀስ ፡ ስለሚደረገው ፡ ለውጥ ፡ ነው ፤ [illegible] ገበል ፡ የለም ፤ አብዮትም ፡



ይቀራል ፡ ማለት ፡ ነው ። አሁን ፡ ያለው ፤ በጣም ፡ የተስፋፋውና ፡ የታወቀው — እንዲህ ፡ ማለት ፡ ከተቻለ — አስተሳሰብ ፡ አለጥርጥር ፡ አብዮትን ፡ ካልተቃወመ ፡ ቢያንስ ፡ ያድበሰብሳል ።

የዚህ ፡ ዓይነት «አባባል» ለቡርዥዋው ፡ ጠቃሚ ፡ የሆነ ፤ ማርክሲዝምን ፡ የሚያጣምም ፡ መናኛ ፡ ነው ፤ በቴዎሪ ፡ ደረጃ ፡ የተመሠረተው ፡ አሁን ፡ በሰፊው ፡ ባቀረብነው ፡ የኤንግልስ «አጭር ፡ ገለፃ» ውስጥ ፡ የተጠቀሱትን ፡ በጣም ፡ አስፈላጊ ፡ የሆኑ ፡ ሁኔታዎችንና ፡ አስተሳሰቦችን ፡ እንኳ ፡ ቸል ፡ በማለት ፡ ነው ።

አንደኛ ። ገና ፡ ከመጀመሪያው ፡ ገለፃ ፡ ኤንግልስ ፡ የሚለው ፤ ወዝ ፡ አደሩ ፡ የመንግሥት ፡ ሥልጣኑን ፡ በመውሰድ «የመንግሥቱን ፡ መንግሥትነት ፡ ያጠፋል» ። ይህ ፡ ምን ፡ ማለት ፡ እንደሆነ ፡ ማሰብ ፡ «የተለመደ» አይደለም ። በጠቅላላው ፡ ይህንን ፡ ወይንም ፡ ፍጹም ፡ ችላ ፡ ይሉታል ፤ ወይንም ፡ እንደኤንግልስ «ሄጌልያዊ ፡ ድካማነት» ይቆጥሩታል ። እውነቱ ፡ ግን ፡ በነዚህ ፡ ቃላት ፡ ባጭሩ ፡ የተጠቀሰው ፡ ከታላቁ ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮቶች ፡ አንዱ ፡ የሆነው ፡ ልምድ ፡ ማለት ፡ የ ፲፰፻፸፩ ዓ. ም. የፓሪስ ፡ ኮሙን ፡ ልምድ ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ በቦታው ፡ በሰፊው ፡ እንመለከተዋለን ። እዚህ ፡ ላይ ፡ በትክክል ፡ ኤንግልስ ፡ የሚናገረው ፡ ስለ ፡ ቡርዥዋው ፡ መንግሥት ፡ በወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት «መደምሰስን» ነው ፤ ስለ ፡ መንግሥት ፡ መክሰም ፡ የሚናገሩት ፡ ቃላት ፡ ግን ፡ የሚመለከቱት ፡ ከሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ ለሚቀረው ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ መንግሥት ፡ ነው ። የቡርዥዋው ፡ መንግሥት ፡ ኤንግልስ ፡ እንደሚለው ፡ በወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት «ይደመሰሳል» እንጂ «አይከስምም» ። ከዚህ ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ የሚከስመው ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ መንግሥት ፡ ወይም ፡ ከፊል ፡ መንግሥት ፡ ነው ።

ሁለተኛ ። መንግሥት «የመጨቆኛ ፡ ልዩ ፡ መሣሪያ ፡

ነው» ። ይህ ፡ ከሙሉ ፡ ግልጽነት ፡ ጋር ፡ በኤንግልስ ፡ የተሰጠ ፡ ድንቅና ፡ በከፍተኛ ፡ ደረጃ ፡ ጥልቅ ፡ የሆነ ፡ ትርጉም ፡ ነው ። ስለዚህም ፡ ቡርዥዋው ፡ ወዝ ፡ አደሩን ፤ እፍኝ ፡ የማይሞሉ ፡ ኃብታሞች ፡ ብዙ ፡ ሚሊዮን ፡ ሠርቶ ፡ አደሮችን «ለመጨቆን ፡ የሚጠቀሙበት ፡ ልዩ ፡ ኃይል» ፤ በሌላ ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ ቡርዥዋውን «ለመጨቆን ፡ በሚጠቀምበት ፡ ልዩ ፡ ኃይል» (በወዝ ፡ አደሩ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት) መተካት ፡ አለበት ። ይህ ፡ ነው ፡ በትክክል «መንግሥት ፡ መንግሥትነቱ ፡ ይጠፋል» ማለት ። ይህ ፡ ነው ፡ በትክክል ፡ የምርት ፡ መገልገያዎችን ፡ በኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ስም ፡ የመውሰድ «ድርጊት» ማለት ። ስለዚህም ፡ የዚህ ፡ ዓይነት ፡ ያንዱ (የቡርዥዋው) «ልዩ ፡ ኃይል» በሌላ (ወዝ ፡ አደሩ) «ልዩ ፡ ኃይል» መተካት ፤ «በመክሰም» መልክ ፡ ሊሆን ፡ እንደማይችል ፡ ራሱ ፡ ግልጽ ፡ ነው ።

ሶስተኛ ። ስለመንግሥት «መክሰም» እና ፡ እንዲያውም ፡ ይበልጥ ፡ ህያውና ፡ ውብ ፡ በሆነ ፡ አገላለጽ ፡ ስለ ፡ መንግሥት «መጠውለግ» ኤንግልስ ፡ ፍጹም ፡ በግልጽና ፡ በትክክል ፡ እንደሚያመለክተው ፡ ወቅቱ «የምርት ፡ መገልገያዎች ፡ በመላ ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ስም ፡ መንግሥት ፡ ከወሰደው» በኋላ ፤ ማለትም ፡ ከሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ ነው ። ሁላችንም ፡ እንደምናውቀው ፡ በዚህ ፡ ጊዜ «የመንግሥት» ፖለቲካዊ ፡ ቅርጹ ፡ ፍጹም ፡ ሙሉ ፡ የሆነ ፡ ዴሞክራሲ ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ ለነዚህ ፡ ማርክሲዝምን ፡ ለሚያጣምሙ ፡ ወስላታ ፡ አድርባዮች ፡ ኤንግልስ ፡ የሚናገረው ፡ ስለ ፡ ዴሞክራሲ «መጥፋት»እና «መክሰም» መሆኑ ፡ ፍጹም ፡ አንጎላቸው ፡ ውስጥ ፡ አይገባም ። ይህ ፡ በመጀመሪያ ፡ ሲታይ ፡ እንግዳ ፡ ነገር ፡ ይመስላል ። ነገር ፡ ግን ፡ ይህ «የማይገባው» ፤ ዴሞክራሲም ፡ እንደዚሁ ፡ መንግሥት ፡ መሆኑን ፡ ላላሰበበት ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ ስለዚህም ፡ መንግሥት ፡ ሲጠፋ ፡ ዴሞክራሲም [illegible] ፡ መንግሥት ፡ ሥት «የማይደመሰሰው» አብዮት [illegible] ቡርዧዋውን ፡ መንግሥ [illegible] ። ጠቅላላው ፡



መንግሥት ፤ ማለትም ፡ ፍጹም ፡ ሙሉ ፡ ዴሞክራሲ «መክሰም» ብቻ ፡ ይችላል ።

አራተኛ ። ኤንግልስ «መንግሥት ፡ ይከስማል» የሚለውን ፡ ዝነኛ ፡ ሐሳቡን ፡ ከጠቀሰ ፡ በኋላ ፡ ወድያውኑ ፡ በተጨበጠ ፡ መንገድ ፡ ያስረዳል ፤ ይኸውም ፡ ይህ ፡ ሀሳብ ፡ የተሰነዘረው ፡ በአድርባዮችም ፤ በሥርዓተ-አልበኞችም ፡ አንፃር ፡ መሆኑን ፡ ነው ። ቢሆንም ፡ ኤንግልስ ፡ በመጀመሪያ ፡ ደረጃ ፡ ያስቀመጠው ፤ በአድርባዮች ፡ አንፃር ፡ ያነጣጠረው «መንግሥት ፡ ይከስማል» ከሚለው ፡ ሀሳብ ፡ ያደረገው ፡ መደምደምያን ፡ ነው ።

እንዲህ ፡ ብሎ ፡ መወራረድ ፡ ይቻላል ። ስለ ፡ መንግሥት «መክሰም» ካነበቡ ፡ ወይንም ፡ ከሰሙ ፡ 10 ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ውስጥ ፡ 9990 ኤንግልስ ፡ የዚህ ፡ ሀሳብ ፡ መደምደምያውን ፡ ያነጣጠረው ፡ በሥርዓተ-አልበኞች ፡ አንፃር ፡ ብቻ ፡ እንዳልሆነ ፡ ፍጹም ፡ አያውቁም ፡ ወይንም ፡ ፍጹም ፡ አያስታውሱም ። ከቀሩት ፡ አስር ፡ ሰዎችም ፡ ምናልባት ፡ ዘጠኙ «ነፃ ፡ ሕዝባዊ ፡ መንግሥት» ማለት ፡ ምን ፡ እንደሆነ ፤ ወይንም ፡ ይህን ፡ መፈክር ፡ መቃወም ፡ ማለት ፡ አድርባዮችን ፡ መቃወም ፡ እንደሆነ ፡ አያውቁም ። እንዲህ ፡ ነው ፡ ታሪክ ፡ የሚጻፈው! እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ነው ፡ ታላቅ ፡ አብዮታዊ ፡ ቴዎሪ ፡ በረቀቀ ፡ ዘዴ ፡ ተውገርግሮ ፡ በተስፋፋው ፡ ጮርቃነት ፡ የሚሸፈነው ። በሥርዓተ-አልበኞች ፡ አንፃር ፡ የተሰነዘረው ፡ መደምደምያ ፡ ሺ ፡ ጊዜ ፡ ተደጋግሞ ፡ ተነግሮ ፡ ነበር ፤ ግን ፡ አጐደፉት ፤ ላይ ፡ ላዩን ፡ በሰዎች ፡ ጭንቅላት ፡ ውስጥ ፡ ተዱሎ ፡ አጉል ፡ እምነት ፡ ጠነከሯል ። በአድርባዮች ፡ አንፃር ፡ የተሰነዘረው ፡ መደምደምያ ፡ ግን ፡ ተውገርግሯልም «ተረስቷልም!»

«ነፃ ፡ ሕዝባዊ ፡ መንግሥት» በ፸ኛዎቹ ፡ ዓመታት ፡ የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ የፕሮግራማቸው ፡ ጥያቄና ፡ የጊዜው ፡ መፈክራቸው ፡ ነበር ። በዚህ ፡ መፈክር ፡ ውስጥ ፡ በጉረኛ ፡ ጮርቃ ፡ መልክ ፡ ስለዴሞክራሲ ፡ ምን

ነት ፡ ከማቅረቡ ፡ ሌላ ፡ ምንም ፡ የፖለቲካ ፡ ይዘት ፡ የለውም ። ዓላማው ፡ በህጋዊ ፡ መንገድ ፡ ወደዴሞክራቲክ ፡ ሪፑብሊክ ፡ በማትኮሩ ፤ ኤንግልስ ፡ ለቅስቀሳ ፡ ያህል ፡ «ለጊዜው» ይህን ፡ መፈክር «ለመደገፍ» ዝግጁ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ ይህ ፡ መፈክር ፡ የቡርዥዋውን ፡ ማቆነጃጀት ፡ ማከሉ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፤ በጠቅላላው ፡ ስለ ፡ ማንኛውም ፡ መንግሥት ፡ ያለው ፡ ሶሺያሊስታዊ ፡ ሂስ ፡ ስለሚስት ፡ የአድርባይ ፡ መፈክር ፡ ነው ። እኛ ፡ በዘመነ ፡ ካፒታሊዝም ፡ ዴሞክራቲክ ፡ ሪፑብሊክ ፡ ለወዝ ፡ አደሩ ፡ የተሻለው ፡ የመንግሥት ፡ ዓይነት ፡ ነው ፡ ብለን ፡ እንደግፋለን ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ዴሞክራቲክ ፡ በሆነ ፡ የቡርዥዋ ፡ ሪፑብሊክም ፡ ቢሆን ፡ የሕዝቡ ፡ ዕድል ፡ የቅጥር ፡ ባርነት ፡ መሆኑን ፡ በምንም ፡ ዓይነት ፡ መዘንጋት ፡ አንችልም ። እንቀጥል ። ማንኛውም ፡ መንግሥት ፡ ጭቁን ፡ መደብን «የመጨቆኛ ፡ ልዩ ፡ ኃይል ፡ ነው ።» ስለዚህም ፡ ማንኛውም ፡ መንግሥት ፡ ነፃም ፡ አይደለም ፤ ሕዝባዊም ፡ አይደለም ። ማርክስና ፡ ኤንግልስ ፡ በ፸ኛዎቹ ፡ ዓመታት ፡ ይኸንን ፡ ለፓርቲ ፡ ጓዶቻቸው ፡ ደጋግመው ፡ ገልጸውላቸዋል ።[7]

አምስተኛ ። ስለመንግሥት ፡ መክሰም ፡ ገለጻ ፡ ባለበት ፡ የኤንግልስ ፡ ጽሑፍ ፡ ውስጥ ፤ ሁላችሁም ፡ ታስታውሳላችሁ ፡ ስለ ፡ አመፃዊ ፡ አብዮት ፡ ምንነትም ፡ ገለጻ ፡ ይገኛል ። ስለሚናውም ፡ ኤንግልስ ፡ የሰጠው ፡ ታሪካዊ ፡ ትንተና ፡ አመፃዊ ፡ አብዮትን፡ በእውነት ፡ የሚያሞግስ ፡ ሆኗል ። ይህን «ማንም ፡ አያስታውሰውም» ፤ ስለሃሳቡ ፡ ምንነት ፡ መናገር ፡ ቀርቶ ፡ ማሰብም ፡ እንኳ ፡ በዘመኑ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ፓርቲዎች ፡ የተለመደ ፡ አይደለም ፤ በየቀኑ ፡ በህዝቡ ፡ ውስጥ ፡ በሚደረገው ፡ ፕሮፓጋንዳና ፡ ቅስቀሳ ፡ ይህ ፡ ሃሳብ ፡ ምንም ፡ ዓይነት ፡ ሚና ፡ አይጫወትም ። ቢሆንም ፡ እነዚህ ፡ ሃሳቦች ፡ ከመንግሥት «መክሰም» ጋር ፡ በጥብቅ ፡ በማይነጣጠል ፡ በአንድ ፡ አካል ፡ የተያያዙ ፡ ናቸው ።





የኤንግልስ ፡ ገለጻ ፡ ይኸውና ፤

«... አመፅ ፡ በታሪክ ፡ ውስጥ» (የክፋት ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን) «ሌላም ፡ ሚና ፡ ይጫወታል ፤ ይኸውም ፡ አብዮታዊ ፡ ሚና ፡ ነው ፤ አመፅ ፤ በማርክስ ፡ ቃላት ፤ አዲስ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብን ፡ ላረገዘ ፡ ማንኛውም ፡ አሮጌ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ አዋላጅ ፡ ነው ፤[8] አመፅ ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ንቅናቄ ፡ መንገዱን ፡ የሚጠርግበት ፤ እንደ ፡ አለት ፡ የጠነከረውንና ፡ የሞተውን ፡ የፖለቲካ ፡ ቅርፅ ፡ የሚሰባብርበት ፡ መሣሪያ ፡ ነው ። ስለተጠቀሰው ፡ ሁሉ ፡ ዱሪንግ ፡ አንድም ፡ ቃል ፡ አይናገርም ። እህ! እያለና ፡ እያቃሰተ ፡ ብቻ ፡ ምናልባት ፡ ጭቆናዊ ፡ ይዞታን ፡ ለመገልበጥ ፡ ኃይል ፡ ያስፈልግ ፡ ይሆናል ፡ ብሎ ፡ ያምናል ። ያሳዝናል ፤ ምክንያቱም ፡ ማንኛውም ፡ ኃይል ፡ የሚጠቀም ፡ መልሶ ፡ ራሱን ፡ ቅስሙን ፡ ስለሚሰብረው ፡ ነው ፡ ይላል ። ይህ ፡ የሚባለው ፡ በማንኛውም ፡ አሸናፊ ፡ አብዮት ፡ የተገኘውን ፡ ትልቅ ፡ የሞራልና ፡ የመንፈስ ፡ ከፍታን ፡ ወደ ፡ ጐን ፡ በመተው ፡ ነው! ይህ ፡ የሚነገረው ፡ የኃይል ፡ ግጭት ፤ ምናልባትም ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ከውጭ ፡ የተደነቀረው ፤ ቢያንስ ፡ በሰላሳ ፡ ዓመቱ ፡ ጦርነት ፡[9] መዋረድ ፡ ምክንያት ፡ በህዝቡ ፡ ህሊና ፡ ውስጥ ፡ የተቀረጸውን ፡ ተለማማጅነትን ፡ ለማስወገድ ፡ በሚቻልበት ፡ በጀርመን ፡ ነው ። ይህ ፡ ደደብ ፤ የጃጀና ፡ የሞተ ፡ የቄስ ፡ አስተሳሰብም ፡ በታሪክ ፡ ውስጥ ፡ ከሁሉም ፡ አብዮታዊ ፡ ለሆነው ፡ ፓርቲ ፡ እንደ ፡ አርአያ ፡ ተደርጎ ፡ ይቀርባል?» (፫ኛው ፡ የጀርመን ፡ እትም ፤ የምዕራፍ IV ፡ መጨረሻ ፡ ክፍል ፡ ሁለት ፤ ገጽ ፡ ፪፺፫)

ይህ ፡ ኤንግልስ ፡ ለጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ ከ ፲፰፻፸፰ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ፲፰፻፺፬ ዓ. ም. ማለትም ፡ እስከ ፡ እለተ ፡ ሞቱ ፡ ድረስ ፡ ሳይታክት ፡ ያቀረበውን ፡

በአመፃዊ ፡ አብዮት ፡ ላይ ፡ ያለው ፡ እምነት ፡ እንዴት ፡ ከመንግሥት «መክሰም» ጋር ፡ ይጣመራል?

አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ ሁለቱንም ፡ የሚያጣምሯቸው ፡ በኤክለክቲሲዝም ፡ መንገድ ፤ በማይረባ ፡ ወይንም ፡ በችኮላ ፡ እንዲያው ፡ በተደረገ ፡ መሸሻ (ወይንም ፡ በሥልጣን ፡ ላይ ፡ ያሉትን ፡ ለማስደሰት) አንዴ ፡ አንዱን ፤ በሌላ ፡ ጊዜ ፡ ሌላውን ፡ ሐሳብ ፡ ሲሆን ፤ ከመቶው ፡ ዘጠና ፡ ዘጠኙ ፡ ጊዜ ፤ በመጀመሪያ ፡ ደረጃ ፡ የሚቀርበው «የመክሰምን» ሐሳብ ፡ ነው ። ዲያለክቲክን ፡ በኤክለክቲሲዝም ፡ ይተካል — ይህ ፡ ነው ፡ ማርክሲዝምን ፡ በሚመለከት ፡ ረገድ ፡ በአሁኖቹ ፡ ህጋዊ ፡ የሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ ሥነ ፡ ጽሑፎች ፡ በጣም ፡ ተለምዶ ፤ ተስፋፍቶ ፡ የሚገኘው ፡ ድርጊት ። የዚህ ፡ ዓይነት ፡ መተካት ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ አይደለም ፤ ይህ ፡ በክላሲካዊ ፡ የግሪክ ፡ ፍልስፍና ፡ ታሪክ ፡ እንኳ ፡ የታየ ፡ ነው ። ማርክሲዝም ፡ በአድርባይነት ፡ ማውገርገር ፤ በዲያሌክቲክ ፡ ፋንታ ፡ ኤክሌክቲሲዝምን ፡ መተካት — ይህ ፡ ነው ፡ ሕዝቡን ፡ ለማታለል ፡ የቀለለ ፡ መንገድ ፤ ይህ ፡ እውነት ፡ የሚመስል ፡ ስሕተተኛ ፡ እርካታ ፡ ይሰጣል ፤ የሂደቱን ፡ ጐኖች ፡ በሙሉ ፤ የዕድገቱን ፡ ዝንባሌዎች ፡ በሙሉ ፤ ተቃራኒ ፡ ዝንባሌዎች ፡ በሞላና ፡ ሌሎችም ፡ የሚመለከት ፡ ይመስላል ፤ በእርግጥ ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ እድገት ፡ ሂደት ፡ ምንም ፡ የተያያዘና ፡ አብዮታዊ ፡ ሐሳብ ፡ አይሰጥም ።

ከላይ ፡ እንዳልነውና ፡ ቀጥለንም ፡ በሰፊው ፡ እንደምናሳየው ፡ የማርክስና ፡ የኤንግልስ ፡ የማይቀር ፡ የአመፃዊ ፡ አብዮት ፡ የግድነት ፡ ቴዎሪ ፡ የሚመለከተው ፡ የቡርዥዋውን፡ መንግሥት ፡ ነው ። ይህ ፡ የቡርዥዋው ፡ መንግሥት ፡ «በመክሰም» ሂደት ፡ ወደ ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ መንግሥት (የወዝ ፡ አደሩ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ ሥልጣን) ሊለወጥ ፡ አይችልም ፤ እንደ ፡ ሕጉ ፡ መሠረት ፡ በአመፃዊ ፡ አብዮት ፡ እንጂ ።



ይህን ፡ ለማሞገስ ፡ በኤንግልስ ፡ የተጻፈውና ፡ እንደዚሁም ፡ በማርክስ ፡ የተደረገው ፡ የተደጋገመ ፡ መግለጫ — («የፍልስፍና ፡ ድህነት» እና «የኮሙኒስት ፡ ማኒፌስቶ» መደምደምያዎችን ፤ ስለ ፡ አመፃዊ ፡ አብዮት ፡ የግድነት ፡ ከሚያኮሩና ፡ ከግልጽ ፡ መግለጫቸው ፡ ጋር ፡ እናስታውስ ፤ ማርክስ ፡ ከ ፴ ዓመት ፡ በኋላ ፡ በ ፲፰፻፸፭ ዓ. ም. በጐታ ፡ ፕሮግራም ፡ ላይ ፡ ባቀረበው ፡ ሂስ ፡ የፕሮግራሙን ፡[10] አድርባይነት ፡ እንዴት ፡ ያለ ፡ ምህረት ፡ እንደቀጣ ፡ እንመልከት) — ይህ ፡ ሙገሳ ፡ በምንም ፡ ዓይነት «ዝንባሌ» ብቻ ፡ አይደለም ፤ ስሜት ፡ ቀስቃሽ ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፤ ክርክራዊ ፡ ማምለጫ ፡ አይደለም ። ሰፊውን ፡ ሕዝብ ፡ የዚህ ፤ በእርግጥም ፡ የዚህ ፡ የአመፃዊ ፡ አብዮት ፡ ርዕየት ፡ አስፈላጊነትን ፡ በደምብ ፡ ማስተማር ፡ የማርክስና ፡ የኤንግልስ ፡ ጠቅላላ ፡ ቴዎሪ ፡ መሠረታዊ ፡ ሃሳብ ፡ ነው ። ይህን ፡ ቴዎሪ ፡ የከዱት ፡ አሁን ፡ ያንሰራሩት ፡ ሶሺያል-ሾቪኒዝምና ፡ የካውትስካውያን ፡ ዝንባሌዎች ፡ ጉልህ ፡ በሆነ ፡ አገላለጽ ፡ ሁለቱም ፡ ይህንን ፡ ፕሮፓጋንዳና ፡ ቅስቀሳ ፡ መርሳታቸውን ፡ ያመለክታል ።

የቡርዥዋው ፡ መንግሥት ፡ ያለ ፡ አመፃዊ ፡ አብዮት ፡ በወዝ ፡ አደር ፡ መንግሥት ፡ አይተካም ። የወዝ ፡ አደር ፡ መንግሥት ፡ የሚደመሰሰው — ማለት ፡ መንግሥት ፡ በጠቅላላው ፡ የሚደመሰሰው ፡ በሌላ ፡ ሳይሆን ፡ «በመክሰም» ሂደት ፡ ነው ።

ስለነዚህ ፡ ርዕዮቶች ፡ ሰፊና ፡ የተጨበጠ ፡ ማብራሪያ ፡ የሰጡት ፡ ማርክስና ፡ ኤንግልስ ፡ እያንዳንዱን ፡ ልዩ ፡ አብዮታዊ ፡ ሁኔታ ፡ ለብቻ ፡ በማጥናት ፤ የእያንዳንዱን ፡ ልዩ ፡ አብዮት ፡ ልምምድ ፡ ትምህርቶችን ፡ በመተንተን ፡ ነው ። አሁን ፡ ወደዚህ ፡ አለጥርጥር ፡ በጣም ፡ አስፈላጊ ፡ ወደ ፡ ሆነው ፡ የቴዎሪዎቻቸው ፡ ክፍል ፡ እናልፋለን ።





## ምዕራፍ ፡ II.

## መንግሥትና ፡ አብዮት ።

## የ ፲፰፻፵፰ — ፲፰፻፶፩ ዓ. ም. ልምድ ።

### ፩. የአብዮቱ ፡ ዋዜማ ።

የመጀመሪያዎቹ ፡ የበሰሉ ፡ ማርክሳዊ ፡ ሥራዎች — «የፍልስፍና ፡ ድህነት» እና «የኮሙኒስት ፡ ማኒፌስቶ» — የወጡት ፡ ልክ ፡ በ ፲፰፻፵፰ ዓ. ም. አብዮት ፡ ዋዜማ ፡ ነው ። በዚህም ፡ ምክንያት ፡ የማርክሲዝምን ፡ አጠቃላይ ፡ መርሆዎች ፡ ከመግለጻቸው ፡ በላይ ፡ እስከተወሰነ ፡ ደረጃ ፡ ድረስም ፡ በጊዜው ፡ የነበረውን ፡ የተጨበጠ ፡ አብዮታዊ ፡ ሁኔታን ፡ ያንፀባርቃሉ ፤ ስለሆነም ፡ የነዚህ ፡ ሥራዎች ፡ ደራሲዎች ፡ የ ፲፰፻፵፰-፲፰፻፶፩ ዓመታት ፡ ልምድ ፡ መደምደምያ ፡ ከማድረጋቸው ፡ በፊት ፡ ስለመንግሥት ፡ ምን ፡ እንዳሉ ፡ መመርመሩ ፡ ጠቃሚ ፡ ነው ።

«የፍልስፍና ፡ ድህነት» በሚባለው ፡ ሥራው ፡ ማርክስ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ይጽፋል ፤

«የወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ በእድገቱ ፡ ሂደት ፡ አሮጌውን ፡ የቡርዡዋ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ በሌላ ፡ መደቦችንና ፤ ቅራኔዎቻቸውን ፡ ሊያስወግድ ፡ በሚችል ፡ ማኅበር ፡ ይተካል ፤ ምንም ፡ ዓይነት ፡ የፖለቲካ ፡ ሥልጣንም ፡ አይኖረውም ፤ ምክንያቱም ፡ የፖለቲካ ፡ ሥልጣን ፡ የቡርዡዋ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ የመደብ ፡ ቅራኔዎች ፡ ህጋዊ ፡ መልኩ ፡ ነውና ።» (የጀርመን ፡ እትም ፤ ፲፰፻፹፭ ዓ. ም. ገጽ ፡ ፪፻፪)

መደቦች ፡ ከተደመሰሱ ፡ በኋላ ፡ መንግሥት ፡ ይጠፋል ፡ ስለሚለው ፡ ሀሳብ ፡ የተሰጠውን ፡ አጠቃላይ ፡ ማብራሪያ ፤ ማርክስና ፡ ኤንግልስ ፡ ከጥቂት ፡ ወራት ፡ በኋላ ፡ በህዳር ፡ ፲፰፻፵፯ ዓ. ም. «በኮሙኒስት ፡ ማኒፌስቶ» ውስጥ ፡ ከሰጡት ፡ ማብራሪያ ፡ ጋር ፡ ማነፃፀር ፡ ትምህርታዊ ፡ ነው ።

«... የወዝ ፡ አደሩን ፡ መደብ ፡ የእድገት ፡ ደረጃ ፡ በጣም ፡ አጠቃላይ ፡ በሆነ ፡ አኳኋን ፡ ብንመለከተው ፤ ባለው ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ውስጥ ፡ በድብቅ ፡ የሚካሄድ ፡ የእርስ ፡ በርስ ፡ ጦርነት ፡ መኖሩን ፡ እናያለን ፤ ይህም ፡ ጦርነት ፡ በመፈንዳት ፡ ወደ ፡ ግልፅ ፡ አብዮት ፡ ይለወጣል ፤ ወዝ ፡ አደሩም ፡ ቡርዡዋውን ፡ በኃይል ፡ በመጣል ፡ የበላይነቱን ፡ እንዲመሰርት ፡ ያደርገዋል ... ... ከላይ ፡ እንደተመለከትነው ፡ በወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት ፡ ውስጥ ፡ የመጀመሪያው ፡ እርምጃ ፡ ወዝ አደሩን ፡ ገዥ ፡ መደብ ፡ ማድረግ ፤ ዴሞክራሲን ፡ መቀዳጀት ፡ ነው ።

የወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ የፖለቲካ ፡ የበላይነቱን ፡ በመጠቀም ፡ ከቡርዡዋው ፡ መደብ ፡ ላይ ፡ ደረጃ ፡ በደረጃ ፡ ካፒታልን ፡ ይነጥቃል ፤ መላ ፡ የምርት ፡ መሣርያዎችን ፡ በመንግሥት — ማለትም ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ እንደ ፡ ገዥ ፡ መደብ ፡ ሆኖ ፡ በተደራጀበት ፡ እጅ ፡ ያስገባል ፤ ጠቅላላውን ፡ የምርት ፡ ኃይሎች ፡ በተቻለ ፡ ፍጥነት ፡ ያባዛል ።» (፯ኛው ፡ የጀርመን ፡ እትም ፡ ፲፱፻፮ ዓ. ም. ገጽ ፡ ፴፩ እና ፡ ፴፯ ።

በዚህ ፡ ጽሑፍ ፡ ውስጥ ፡ ስለመንግሥት ፡ ጥያቄ ፡ በጣም ፡ ግሩምና ፡ በጣም ፡ አስፈላጊ ፡ የሆኑትን ፡ የማርክሲዝም ፡ ሐሳቦችን — በተለይም (ማርክስና ፡ ኤንግልስ ፡ ከፓሪስ ፡ ኮሙን ፡ በኋላ ፡ እንደሰየሙት) «የወዝ ፡ አደሩ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ ሥልጣን» ሐሳብ ፡ እናያለን ፤ ከዚያም «ከተረሱት» የማርክሲዝም «ቃላት» አንዱ ፤ በከፍተኛ ፡ ደረጃ ፡ ግሩም ፡ የሆነውን ፡ የመንግሥት ፡ ትርጉም ፡ እና

ገኛለን ። «መንግሥት — ወዝ ፡ አደሩ ፡ እንደ ፡ ገዥ ፡ መደብ ፡ የተደራጀበት ፡ ድርጅት ፡ ነው ።»

ባንሠራራው ፡ የህጋዊ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ ፓርቲዎች ፡ የፕሮፓጋንዳና ፡ የቅስቀሳ ፡ ስነ ፡ ጽሑፍ ፡ ውስጥ ፡ ስለዚህ ፡ የመንግሥት ፡ ትርጉም ፡ ምንም ፡ ማብራሪያ ፡ ቀርቦ ፡ አያውቅም ። እንዲያውም ፡ ሆን ፡ ብለው ፡ ትተውታል ፤ ምክንያቱም ፡ ከጥገና ፡ ለውጥ ፡ ጋር ፡ በፍጹም ፡ የማይታረቅ ፡ ነውና ፤ ምክንያቱም «ዴሞክራሲ ፡ በሰላም ፡ ያድጋል» ለሚባለው ፡ የተራ ፡ አድርባዮች ፡ አጉል ፡ እምነትንና ፡ የጮርቃዎች ፡ ቅዠት ፡ መራራ ፡ ጥፌ ፡ ነውና ።

ለወዝ ፡ አደሩ ፡ መንግሥት ፡ ያስፈልገዋል — ይህንን ፡ ሁሉም ፡ አድርባዮች ፤ ሶሺያል-ሾቪኒስቶችና ፡ ካውትስኪያውያኖች ፤ ማርክስ ፡ ያስተማረው ፡ ይህንን ፡ መሆኑን ፡ በማረጋገጥ ፤ ይደጋግሙታል ። ነገር ፡ ግን ፡ ለመጨመር «የሚረሱት» — አንደኛ — ማርክስ ፡ እንዳለው ፡ ለወዝ ፡ አደሩ ፡ የሚያስፈልገው ፡ የሚከስም ፡ መንግሥት ፡ ብቻ ፡ መሆኑን ፤ ማለትም ፡ ወድያውኑ ፡ መክሰም ፡ እንዲጀምር ፡ ሆኖ ፡ የተቀነባበረ ፡ የሚከስም ፡ መንግሥት ፡ መሆኑን ፤ ሁለተኛ — ለሠርቶ ፡ አደሮች «መንግሥት» ማለትም «ወዝ ፡ አደሩ ፡ እንደገዥ ፡ መደብ ፡ የተደራጀበት» እንደሚያስፈልጋቸው ፡ ነው ።

መንግሥት ፡ ልዩ ፡ የኃይል ፡ ድርጅት ፡ ነው ፤ የተወሰነ ፡ መደብን ፡ ለመጨቆን ፡ የሚያገለግል ፡ የአመፅ ፡ ድርጅት ፡ ነው ። ወዝ ፡ አደሩ ፡ የሚጨቁነው ፡ የትኛውን ፡ መደብ ፡ ነው? በእርግጥ ፤ በዝባዦን ፡ መደብ ፤ ቡርዥዋውን ፡ ብቻ ፡ ነው ። ሠርቶ ፡ አደሩ ፡ መንግሥት ፡ የሚያስፈልገው ፡ የበዝባዦችን ፡ ተቃውሞ ፡ ለመጨቆን ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ ይህንንም ፡ ሊመራውና ፡ ከግቡ ፡ ሊያደርሰው ፡ የሚችለው ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ ብቻ ፡ ነው ። ምክንያቱም ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ ብቻ ፡ እስከ ፡ መጨረሻ ፡ ድረስ ፡



አብዮታዊ ፡ በመሆኑ ፤ መላ ፡ ሠርቶ ፡ አደሮችንና ፡ ምዝብሮችን ፡ በማስተባበር ፡ ከቡርዥዋው ፡ ጋር ፡ ለመታገልና ፡ እንድያውም ፡ ፍጹም ፡ ለማጥፋት ፡ የሚችል ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ ብቻ ፡ በመሆኑ ፡ ነው ።

ጨቋኝ ፡ መደብ ፡ የብዝበዛ ፡ ፍላጎቱን ፡ ለማስጠበቅ ፡ የፖለቲካ ፡ ሥልጣን ፡ ያስፈልገዋል ፤ ማለትም ፡ በጣት ፡ ለሚቆጠሩ ፡ ስስታሞች ፡ ጥቅም ፡ አብዛኛውን ፡ ሰፊ ፡ ሕዝብ ፡ ለመጨቆን ። ጭቁን ፡ መደብ ፡ ግን ፡ የፖለቲካ ፡ ሥልጣን ፡ የሚያስፈልገው ፡ ማንኛውም ፡ ዓይነት ፡ ብዝበዛን ፡ ፍጹም ፡ ለማጥፋት ፡ ነው ። ይኸውም ፡ ለአብዛኛው ፡ ሰፊ ፡ ሕዝብ ፡ ጥቅም ፤ በጣት ፡ የሚቆጠሩትን ፡ ዘመናዊ ፡ ባርያ ፡ ገዥዎችን ፡ ማለት ፡ የመሬት ፡ ከበርቴዎችንና ፡ ካፒታሊስቶችን ፡ ለመጨቆን ፡ ነው ።

የንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ዴሞክራቶች — እነዚህ ፡ አታላይ ፡ ሶሺያሊስቶች — የመደብ ፡ ትግልን ፤ መደቦችን ፡ ማስማማት ፡ በሚለው ፡ ህልም ፡ ይለውጡታል ፤ እንደ ፡ አመለካከታቸውም ፡ ሶሺያሊስት ፡ ለውጥ ፡ ይመጣል ፡ ብለው ፡ የሚያልሙት ፡ የበዝባዥ ፡ መደብ ፡ ገዥነትን ፡ በመገልበጥ ፡ ሳይሆን ፡ ጥቂቶቹ ፡ ዓላማቸውን ፡ ለተረዱ ፡ ለአብዛኞቹ ፡ በሰላም ፡ በመታዘዝ ፡ ነው ። ይህ ፡ መንግሥት ፡ ከመደቦች ፡ በላይ ፡ ነው ፡ ከሚለው ፡ የማይለይ ፤ በገቢር ፡ የሠርቶ ፡ አደር ፡ መደቦችን ፡ ጥቅም ፡ ወደ ፡ መክዳት ፡ ያደረሰ ፡ የንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ተምኔታዊነት ፡ ነው ። ይህ ፡ ለምሳሌ ፡ በፈረንሳይ ፡ የ ፲፰፻፵፰ ና ፡ የ ፲፰፻፸፩ ዓመታት ፡ የተካሔዱ ፡ አብዮቶች ፡ ታሪክ ፡ አሳይቶናል ፤ እንዲሁም ፡ ደግሞ ፡ በ ፲፱ኛው ፡ ክፍለ ፡ ዘመን ፡ መጨረሻና ፡ በ፳ኛው ፡ ክፍለ ፡ ዘመን ፡ መጀመሪያ ፡[11] በእንግሊዝ ፤ በፈረንሳይ ፤ በኢጣልያና ፡ በሌሎችም ፡ አገሮች ፡ በተደረገው ፡ በቡርዥዋ ፡ ሚኒስቴሮች «የሶሺያሊስት» ተካፍሎ ፡ ልምድ ፡ ታይቷል ።

ማርክስ ፡ ሕይወቱን ፡ በሙሉ ፡ ከዚህ ፡ የንዑስ ፡ ቡር

ዥዋ ፡ ሶሺያሊዝም ፡ ጋር ፡ ተዋግቷል ፤ አሁን ፡ በሩሲያ፡ በሶሺያሊስት-አብዮታዊ ፡[4] ፓርቲና ፡ በሜንሼቪኮች ፡[5] ፓርቲ ፡ እንደገና ፡ ትንሳኤ ፡ እያገኘ ፡ ነው ። ማርክስ ፡ የመደብ ፡ ትግል ፡ ቴዎሪውን ፡ ሳይታክት ፡ እስከ ፡ የፖለቲካ ፡ ሥልጣን ፡ ቴዎሪና ፡ እስከ ፡ የመንግሥት ፡ ቴዎሪ ፡ ድረስ ፡ አሳድጓል ።

የቡርዥዋው ፡ ገዥነትን ፡ ለመጣል ፡ የሚቻለው ፡ በወዝ ፡ አደሩ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ ይህን ፡ ልዩ ፡ መደብ ፡ የኤኮኖሚ ፡ የኑሮ ፡ ሁኔታዎቹ ፡ ለዚህ ፡ ተግባር ፡ ያዘጋጁታል ፤ ከግቡ ፡ ለማድረስም ፡ ምቹ ፡ ሁኔታንና ፡ ኃይልን ፡ ይሰጡታል ። ቡርዥዋው ፡ አርሶ ፡ አደሩንና ፡ መላ ፡ የንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ክፍሎችን ፡ በፈረካከሰና ፡ በሰነጣጠቀ ፡ መጠን ፡ ወዝ ፡ አደሩን ፡ ያስተሳስራል ፤ ያስተባብራል ፤ ያደራጃል ። በሰፊው ፡ ምርት ፡ ውስጥ ፡ ባለው ፡ የኤኮኖሚ ፡ ተሳትፎ ፡ ሚና ፡ ምክንያት ፤ ቡርዥዋው ፡ ከወዝ ፡ አደሮቹ ፡ በበለጠ ፡ የሚበዘብዛቸውን ፤ የሚጨቁናቸውንና ፡ የሚያደቃቸውን ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ለነፃነታቸው ፡ ራሱን ፡ የቻለ ፡ ትግል ፡ ማካሄድ ፡ የማይችሉትን ፡ መላ ፡ ሠርቶ ፡ አደሮችንና ፡ ሰፊ ፡ ጭቁን ፡ ሕዝቦችን ፡ ሊመራ ፡ የሚችለው ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

ማርክስ ፡ በመንግሥት ፡ ጥያቄ ፡ በሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ የተጠቀመበት ፡ የመደብ ፡ ትግል ፡ ቴዎሪ ፡ የሚያመራን ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ የፖለቲካ ፡ ገዥነት ፤ የሱ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፤ ማለትም ፡ ቀጥታ ፡ በታጠቀ ፡ ሰፊ ፡ ሕዝብ (በሕዝባዊ ፡ ሠራዊት) የተደገፈ ፡ በፍጹም ፡ ሌላ ፡ የማይካፈልበት ፡ ሥልጣን ፡ የሚያስፈልግ ፡ መሆኑን ፡ ያረጋግጣል ። ቡርዥዋውን ፡ ለማስወገድ ፡ የሚቻለው ፤ የቡርዥዋው ፡ የማይቀረውንና ፡ ተስፋቢስ ፡ የሆነውን ፡ ተቃውሞ ፡ ለመደቆስና ፤ መላ ፡ ሰፊ ፡ ሠርቶ ፡ አደሮችንና ፡ ጭቁኖችን ፡ ለአዲስ ፡ የኤኮኖሚ ፡ ሥርዓት ፡ ለማደራጀት ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ገዥ ፡ መደብ ፡ ሲሆን ፡ ብቻ ፡ ነው ።



ወዝ ፡ አደሩ ፡ የመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ ያስፈልገዋል ፤ ማእከላዊ ፡ የኃይል ፡ ድርጅት ፤ የአመፅ ፡ ድርጅት ፤ ያስፈልገዋል ፤ ይህም ፡ የበዝባዦችን ፡ ተቃውሞ ፡ ለመደቆስና ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ብዙ ፡ የሆነውን ፡ ሰፊም ፡ ሕዝብ — አርሶ ፡ አደሩን ፤ ንዑስ ፡ ቡርዥዋውንና ፡ ከፊል-ወዝ ፡ አደሩን ፡ የሶሺያሊስት ፡ ኤኮኖሚን «እንዲያደራጁ» ለመምራት ፡ ነው ።

የወዝ ፡ አደሩን ፡ ፓርቲ ፡ በማስተማር ፤ ማርክሲዝም ፡ ሥልጣን ፡ ለመውሰድና ፡ መላውን ፡ ሕዝብ ፡ ወደ ፡ ሶሺያሊዝም ፡ ለመምራት ፡ ችሎታ ፡ ያለውን ፤ አዲሱን ፡ ሥርዓት ፡ ለመምራትና ፡ ለማደራጀት ፡ የሚችል ፤ መላ ፡ ሠርቶ ፡ አደሮችና ፡ ተበዝባዦች ፡ ያለ ፡ ቡርዥዋና ፡ ፀረ-ቡርዥዋ ፡ የሆነ ፡ የራሳቸውን ፡ ኀብረተ ፡ ሰብ ፡ ኑሮ ፡ ሲገነቡ ፡ ለአስተማሪነት ፤ ለመሪነት ፤ ለአለቃነት ፡ ችሎታ ፡ ያለውን ፤ የወዝ ፡ አደሩን ፡ ግምባር ፡ ቀደም ፡ ያስተምራል ። በአንፃሩ ፤ አሁን ፡ ያንሰራራው ፡ አድርባይነት ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ ፓርቲ ፡ አባሎች ፡ የሚያስተምረው ፡ ከሰፊው ፡ ሕዝብ ፡ ከተነጠሉት ፤ የተሻለ ፡ ደሞዝ ፡ ከሚከፈላቸው ፤ በካፒታሊዝም ፡ ደህና «ከተመቻቸው» ፤ የስነ ፡ ልደት ፡ መብታቸውን ፡ ለፍርፋሪ ፡ ከሸጡት ፤ ማለትም ፡ ሕዝቡ ፡ ከቡርዥዋ ፡ ጋር ፡ በሚያደርገው ፡ ትግል ፡ የነበራቸውን ፡ አብዮታዊ ፡ የመሪነት ፡ ሚናን ፡ ከካዱት ፡ ሠራተኞች ፡ ጋር ፡ እንዲቀላቀሉ ፡ ነው ።

«መንግሥት — ወዝ ፡ አደሩ ፡ እንደ ፡ ገዥ ፡ መደብ ፡ የተደራጀበት ፡ ድርጅት ፡ ነው» ፤ ይህ ፡ የማርክስ ፡ ቴዎሪ ፤ ወዝ ፡ አደሩ ፡ በታሪክ ፡ ውስጥ ፡ ስላለው ፡ አብዮታዊ ፡ ሚና ፡ ካለው ፡ መላ ፡ ቴዎሪው ፡ ጋር ፡ የማይለያይ ፡ ነው ። የዚህ ፡ ሚና ፡ ተፍፃሜት ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፤ የወዝ ፡ አደሩ ፡ የፖለቲካ ፡ ገዥነት ፡ ነው ።

ነገር ፡ ግን ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ መንግሥት ፡ የሚያስፈልገው ፡ ቡርዥዋውን ፡ ለመገልበጥ ፡ እንደ ፡ ልዩ ፡ የአመፅ ፡ ድርጅት ፡ ከሆነ ፤ ከዚህ ፡ የሚከተለው ፡ መደምደምያ ፡ ማድ

ረግ ፡ ይቻላል ፤ ማለት ፡ በ'ርዥዋው ፡ ለራሱ ፡ የመሠ ረተውን ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ ሳያስወግዱና ፡ ሳይደመ ስሱ ፡ የዚህ ፡ ዓይነት ፡ ድርጅት ፡ መመሥረት ፡ ይቻላልን? «የኮሙኒስት ፡ ማኒፌስቶ» ቀጥታ ፡ የሚያመራን ፡ ወደዚህ ፡ መደምደምያ ፡ ነው ፤ የ ፲፰፻፵፰-፶፩ ዓ. ም. አብዮት ፡ ልም ድን ፡ ሲያጠቃልል ፡ ማርክስ ፡ የሚናገረው ፡ ስለዚህ ፡ መደምደምያ ፡ ነው ።

## ፬. የአብዮቱ ፡ ውጤቶች ።

እኛ ፡ ስለምንፈልገው ፤ ስለ ፡ መንግሥት ፡ ጥያቄ ፡ ማር ክስ ፡ ከ፲፰፻፵፰-፶፩ ዓ. ም. አብዮት ፡ ያደረጋቸውን ፡ መደ ምደሚያዎች ፡ በማብራራት — «፲፰ ኛው ፡ የሉዊ ፡ ቦና ፓርት ፡ ብሩሜር» በተባለው ፡ ጽሁፉ ፡ እንደሚከተለው ፡ ይገልጻል ።

«... ግን ፡ አብዮቱ ፡ ጥልቀት ፡ ያለው ፡ ነው ። ገና ፡ በመካነ-ንስሀ (purgatory) በኩል ፡ በመጓዝ ፡ ላይ ፡ ነው ። ሥርዓት ፡ ጠብቆ ፡ ሥራውን ፡ እየሠራ ፡ ነው ። በታህ ሳስ ፡ ፪ ፤ ፲፰፻፶፩ ዓ. ም.» (ሉዊ ፡ ቦናፓርት ፡ መፈንቅ ለ ፡ መንግሥት ፡ ባደረገበት ፡ ቀን) «ግማሽ ፡ የዝግጅት ፡ ሥራውን ፡ ፈጽሟል ። አሁን ፡ የቀረውን ፡ ግማሽ ፡ በማሟላት ፡ ላይ ፡ ነው ። መጀመርያ ፡ ለመጣል ፡ እን ዲመች ፡ አድርጎ ፡ የፓርላማ ፡ ሥልጣንን ፡ ያሻሽ ላል ። አሁን ፡ ይህ ፡ ከተደረሰበት ፡ በኋላ ፡ የሥራ ፡ አስ ፈጻሚ ፡ ሥልጣንን ፡ አሻሽሎ ፡ ወደ ፡ ትክክለኛው ፡ ሥ ራው ፡ በማውረድ ፤ ለብቻ ፡ በማስቀረት ፤ እንደ ፡ አን ድ ፡ ነገር ፡ በራሱ ፡ አንፃር ፡ በማስቀመጥ ፡ መላ ፡ የማፍ ረስ ፡ ኃይሎችን ፡ በዚህ ፡ አንፃር ፡ ለማከማቸት ፡ ይጥ ራል» (ስርዝ ፡ የኛ ፡ ነው ።) «አብዮቱ ፡ ከተቀዳሚ ፡



ሥራው ፡ አንዱ ፡ ይህን ፡ ሁለተኛ ፡ ግማሽ ፡ ከፈጸመ ፤ አውሮፓ ፡ ከተቀመጠችበት ፡ ተነሥታ ፡ በደስታ ፤ አ ንተ ፡ አሮጌው ፡ ፍልፈል ፤ እንኳን ፡ ተጨቦድህ! ትላ ለች ።

ይህ ፡ የሥራ ፡ አስፈጻሚ ፡ ሥልጣን ፡ ከብዙ ፡ የቢ ሮክራሲና፡ወታደራዊ ፡ ድርጅቶቹ ፡ ጋር ፤ ከሰፊውና ፡ ከሰው ፡ ሠራሽ ፡ የመንግሥቱ ፡ መኪና ፡ ጋር ፤ ግማሽ ፡ ሚሊዮን ፡ የባለሥልጣኖች ፡ ሠራዊት ፤ ከግማሽ ፡ ሚሊ ዮን ፡ የጦር ፡ ሠራዊት ፡ ጋር ፡ የፈረንሳይ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብን ፡ አካል ፡ በመተብተብ ፤ የሰውነቱ ፡ ቀዳዳዎችን (pores) ፈንጥሮ ፡ የያዘ ፡ ይህ ፡ አስፀያፊ ፡ ተባይ-አካል ፡ ብቅ ፡ ያለው ፡ የፊውዳሉ ፡ ሥርዓት ፡ ተንኮታኩቶ ፡ የዘውድ ፡ አገዛዝ ፡ ሙሉ ፡ ሥልጣን ፡ በነበረበት ፡ ዘመ ን ፡ ሲሆን ፤ የፊውዳሉን ፡ ሥርዓት ፡ መውደቅም ፡ አፋጥ ኗል ። » የመጀመሪያው ፡ የፈረንሳይ ፡ አብዮት ፡ መ ተባበርን ፡ አሳድጓል ፤ «አብሮም ፡ የመንግሥት ፡ ሥል ጣን ፡ ስፋት ፤ ልዩ ፡ ጠባይና ፡ የረዳቶች ፡ ቁጥር ፡ ጨም ሯል ። ናፖሌዎን ፡ ይህን ፡ የመንግሥት ፡ መኪናውን ፡ አሟልቷል ።» ሕጋዊው ፡ የዘውድ ፡ አገዛዝና ፡ የሃም ሌው ፡ የዘውድ ፡ አገዛዝ «ከትልቅ ፡ የሥራ ፡ ክፍፍል ፡ በስተቀር ፡ ሌላ ፡ ምንም ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ አልጨመሩም ... ... በመጨረሻም ፡ ባለፓርላማው ፡ ሪፑብሊክ ፡ አብዮቱን ፡ በመቃወም ፡ ለሚያደርገው ፡ ትግል ፤ ከጭቆና ፡ እርምጃዎች ፡ ሌላ ፤ የመንግሥቱን ፡ ሥልጣን ፡ ማዕከላዊነትና ፡ ዘዴዎች ፡ ማስተባበሩን ፡ እንዲያጠ ነክር ፡ ተገዷል ። ሁሉም ፡ ለውጦች ፡ ይህንን ፡ የመ ንግሥት ፡ መኪና ፡ በመደምሰስ ፡ ፈንታ ፡ አሻሽለው ታል ።» (ስርዝ ፡ የኛ ፡ ነው ።) «አንዱ ፡ ሌላውን ፡ በመ ተካት ፡ የበላይ ፡ ለመሆን ፡ የሚታገሉት ፡ ተወዳዳሪ ፡ ፓርቲዎች ፡ ድል ፡ ሲመቱ ፡ እንደ ፡ ዋና ፡ ግባቸው ፡ የሚቆጥሩት ፡ ትልቁን ፡ የመንግሥት ፡ አካል ፡ መያዝ ፡

ነበር ። » (« ፲፰ኛው ፡ የሉዊ ፡ ቦናፓርት ፡ ብሩሜር » ገጽ ፡ ፺፰-፺፱ ፤ ሁለተኛው ፡ እትም ፤ ሃምቡርግ ፤ ፲፱፻፸ ዓ. ም.)

በዚሁ ፡ ግሩም ፡ ትንተና ፡ ማርክሲዝም « ከኮሙኒስት ፡ ማኒፌስቶ » ጋር ፡ ሲነፃፀር ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ትልቅ ፡ እርምጃ ፡ ወደፊት ፡ አድርጓል ። « በኮሙኒስት ፡ ማኒፌስቶ » ውስጥ ፡ የመንግሥት ፡ ጥያቄ ፡ የተቀመጠው ፡ በጣም ፡ አጠቃላይ ፡ በሆነ ፡ አኳኋን ፤ በጣም ፡ አጠቃላይ ፡ በሆኑ ፡ ቃላትና ፡ አገላለጽ ፡ ነው ። ከዚህ ፡ በላይ ፡ በጠቀስነው ፡ ጥቅስ ፡ ግን ፡ ጥያቄው ፡ የተቀመጠው ፡ በተጨበጠ ፡ አኳኋን ፡ ሲሆን ፤ መደምደምያውም ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ትክክል ፤ ግልፅ ፤ በገቢር ፡ ሊዳሰስ ፡ የሚችል ፡ ጉልህ ፡ ነው ፤ ማለት ፡ ያለፉት ፡ አብዮቶች ፡ ሁሉ ፡ የመንግሥት ፡ መኪናን ፡ አሻሽለውታል ፤ የሚያስፈልገው ፡ ግን ፡ መስበርና ፡ ማድቀቅ ፡ ነው ።

ይህ ፡ መደምደምያ ፡ መንግሥት ፡ በሚመለከት ፡ ረገድ ፡ የማርክሲስት ፡ ቴዎሪ ፡ ዋናና ፡ መሠረታዊ ፡ ነው ። ይህን ፡ መሠረታዊ ፡ ነጥብ ፡ ባንሠራሩት ፡ ሕጋዊ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ ፓርቲዎች ፡ ፈጽሞ ፡ መረሳቱ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፤ በታወቀው ፡ የሁለተኛ ፡ ኢንተርናሽናል ፡ ቴዎረቲክ (theoretician) በካውትስኪይም ፡ ቀጥታ ፡ ተጣሟል ።

« የኮሙኒስት ፡ ማኒፌስቶ » አጠቃላይ ፡ የታሪክ ፡ ትንተናዎችን ፡ ይሰጣል ፤ ይህም ፡ መንግሥት ፡ የገዥ ፡ መደብ ፡ ድርጅት ፡ መሆኑን ፡ እንድናይ ፡ ያስገድደናል ፤ እንደዚሁም ፤ ወደ ፡ አስፈላጊው ፡ መደምደምያ ፤ ማለት ፡ ይኸውም ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ መጀመሪያ ፡ የፖለቲካ ፡ ሥልጣንን ፡ ሳይጨብጥ ፤ የፖለቲካ ፡ የበላይነትን ፡ ሳያገኝ ፤ መንግሥትን ፡ ወደ « ወዝ ፡ አደሩ ፡ እንደ ፡ ገዥ ፡ መደብ ፡ ወደ ተደራጀ ፡ ድርጅት » ሳይለውጥ ፡ ቡርዥዋውን ፡ ለመገ



ልበጥ ፡ አይችልም [illegible] ፡ ይመራናል ። ይህ ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ መንግሥት ፡ ድል ፡ ካደረገ ፡ በኋላ ፡ ወድያውኑ ፡ መንግሥቱ ፡ መክሰም ፡ ይጀምራል ፤ ምክንያቱም ፡ የመደብ ፡ ቅራኔዎች ፡ በሌሉበት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ መንግሥት ፡ አያስፈልግምና ፤ ሊኖርም ፡ አይችልም ። ነገር ፡ ግን ፡ በታሪክ ፡ ዕድገት ፡ ሲታይ ፤ ይህ ፡ የቡርዥዋ ፡ መንግሥት ፡ እንዴት ፡ በወዝ ፡ አደር ፡ መንግሥት ፡ ይተካል ፡ የሚለው ፡ ጥያቄ ፡ አልተነሳም ።

ይህን ፡ ጥያቄ ፡ ነው ፡ ማርክስ ፡ በ ፲፰፻፵፪ ዓ. ም. ያነሳውና ፡ መልስም ፡ የሰጠበት ። የዲያሌክቲካዊ ፡ ማተሪያሊዝም (ቁስ ፡ አካልነት) ፍልስፍናውን ፡ በመከተል ፡ ማርክስ ፡ የ ፲፰፻፵፰-፵፩ ዓመታት ፡ ታላቅ ፡ አብዮት ፡ ታሪካዊ ፡ ልምድን ፡ እንደ ፡ መሠረት ፡ ይወስዳል ። እንደ ፡ ማንኛውም ፡ ጊዜ ፤ አሁንም ፡ የማርክስ ፡ ቴዎሪ ፡ በጥልቅ ፡ የፍልስፍና ፡ ፅንሰ ፡ ሀሳብና ፡ ከታሪክ ፡ ባካበተው ፡ ብዙ ፡ እውቀት ፡ ያሸበረቀ ፡ የልምድ ፡ አጠቃላይ ፡ መደምደምያ ፡ ነው ።

የመንግሥትን ፡ ጥያቄ ፡ በተጨበጠ ፡ ሁኔታ ፡ ያስቀምጠዋል ፤ — ቡርዥዋው ፡ ለገዥነት ፡ ያስፈለገውን ፡ የመንግሥት ፡ መኪና — የቡርዥዋ ፡ መንግሥት ፡ ታሪካዊ ፡ አመሠራረት ፡ እንዴት ፡ ነው? የቡርዥዋው ፡ አብዮቶች ፡ ሲካሄዱና ፡ በጭቁን ፡ መደቦች ፡ ነፃ ፡ ድርጊት ፡ ፊት ፡ ላይ ፡ ሲታይ ፤ ምን ፡ ዓይነት ፡ ለውጦች ፤ ምን ፡ ዓይነት ፡ ኤቮሉሽን ፡ አድርጓል? ይህን ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ በሚመለከት ፡ ጉዳይ ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ ተግባሮች ፡ ምን ፡ ዓይነት ፡ ናቸው?

የቡርዥዋው ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ልዩ ፡ ባህርይ ፡ የሆነው ፡ ማእከላዊ ፡ የመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ የተመሠረተ ፡ አብሶሉቲዝም (የዘውድ ፡ አገዛዝ ፡ ሙሉ ፡ ሥልጣን) በወደቀበት ፡ ዘመን ፡ ነው ። ለዚህ ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ በይበልጥ ፡ ልዩ ፡ ባህርይ ፡ የሆኑት ፡ ሁለት ፡ ድርጅቶች —

ቢሮክራሲውና ፡ ቋሚ ፡ ጦር ፡ ናቸው ። እነዚህ ፡ ድርጅቶች ፡ በብዙ ፡ ሺ ፡ ክሮች ፡ ከቡርዥዋው ፡ ጋር ፡ የተሳሰሩ ፡ መሆናቸውን ፡ ማርክስና ፡ ኤንግልስ ፡ በጽሑፎቻቸው ፡ ውስጥ ፡ ደግመው ፡ ደጋግመው ፡ ተናግረዋል ። የእያንዳንዱ ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ልምድ ፡ ይህን ፡ መተሳሰር ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ግልፅና ፡ ግሩም ፡ በሆነ ፡ አኳኋን ፡ ያሳያል ። ከራሱ ፡ ከግሉ ፡ መራራ ፡ ልምድ ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ ይህ ፡ መተሳሰር ፡ መኖሩን ፡ ተገንዝቧል ፣ ተምሯል ። ለዚህ ፡ ነው ፡ ይህ ፡ መተሳሰር ፡ የማይቀር ፡ መሆኑን ፡ የሚያሳየውን ፡ ሳይንስ ፡ በቀላሉ ፡ የሚገባውና ፡ ጠንክሮም ፡ የሚማረው ፣ ይህን ፡ ሳይንስ ፡ ንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ዴሞክራቶች ፡ በድንቁርና ፡ ወይም ፡ በደንታ ፡ ቢስነት ፡ አይቀበሉትም ፣ ወይም ፡ አስፈላጊ ፡ ገቢራዊ ፡ መደምደምያዎች ፡ ማድረግን ፡ በመርሳት ፣ እንዲያውም ፡ በባሰ ፡ ደንታ ፡ ቢስነት « ባጠቃላይ » ይቀበሉታል ።

ቢሮክራሲና ፡ ቋሚ ፡ ጦር ፡ በቡርዥዋ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ሰውነት ፡ ላይ ፡ ያሉ « መዥገሮች » ናቸው ፣ እነዚህ ፡ ተባዮች ፡ የተፈጠሩት ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ በውስጡ ፡ ባሉት ፡ ተፃራሪ ፡ ቅራኔዎች ፡ በመሰንጣጠቁ ፡ ነው ፣ እነዚህ ፡ ተባዮች ፡ የኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ አስፈላጊ ፡ የሰውነት ፡ ቀዳዳዎችን « ፈንጥረው ፡ የያዙ » ናቸው ። አሁን ፡ በሕጋዊው ፡ ሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ ያንሰራራው ፡ የካውትስኪይ ፡ አድርባይት ፣ መንግሥት ፡ የተባይ ፡ ህዋስ ፡ ነው ፣ የሚለውን ፡ ርዕየት ፡ የሚመለከተው ፡ እንደልዩ ፡ የሥርዓት-አልበኝነት ፡ መለያ ፡ ባህርይ ፡ ነው ። አዎ ፣ ማርክሲዝምን ፡ የማጣመም ፡ ተግባር ፡ በጣም ፡ የሚጠቅመው ፡ ለነዛ « የእናት ፡ ሃገርን ፡ መከላከል!» የሚለውን ፡ ፅንሰ ፡ ሀሳብ ፡ በመጠቀም ፡ የኢምፔሪያሊስት ፡ ጦርነትን ፡ በመሸፋፈንና ፡ በማቆነጃጀት ፡ ሶሺያሊዝምን ፡ ተሰምቶ ፡ ወደማይታወቅ ፡ አዘቅት ፡ ለሚጥሉ ፡ ጮርቃዎች ፡ ነው ፣ ይህ ፡ ያለ ፡ ጥርጥር ፡ ማርክሲዝምን ፡ ማጣመም ፡ ነው ።



ፊውዳሊዝም ፡ ከወደቀበት ፡ ጊዜ ፡ ጀምሮ ፡ አውሮፓ ፡ ባየቻቸው ፡ በጣም ፡ ብዙ ፡ የቡርዥዋ ፡ አብዮቶች ፡ ዘመን ፡ የቢሮክራሲውና ፡ የወታደራዊው ፡ አውታር ፡ አደገዋል ፣ ተሻሽለዋል ፣ ጠንክረዋልም ። በተለይም ፡ ወደ ፡ ትልቁ ፡ ቡርዥዋ ፡ ወገን ፡ በጣም ፡ የሚሳበውና ፡ በዚህ ፡ አውታር ፡ አማኻኝነት ፡ በከፍተኛ ፡ ደረጃ ፡ ለሱ (ለትልቁ ፡ ቡርዥዋ) የሚታዘዘው ፡ ንዑስ ፡ ቡርዥዋው ፡ ነው ። ይህ ፡ አውታር ፡ ለሃብታም ፡ ገበሬዎች ፣ ለእጅ ፡ ሥራ ፡ አዋቂዎች ፣ ለነጋዴዎችና ፡ ለመሳሰሉት ፣ ሲነፃፀር ፡ ምቹ ፣ ሰላማዊና ፡ ክብር ፡ ያለው ፡ ሥራ ፡ ይሰጣል ፣ ይህ ፡ የተሰጣቸው ፡ ሥራ ፡ ሰዎቹ ፡ ከሕዝቡ ፡ በላይ ፡ እንዲሆኑ ፡ ያደርጋቸዋል ። ከየካቲት ፡ ፳፯ ቀን ፡ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. በኋላ ፡[12] በነበረው ፡ መንፈቅ ፡ ውስጥ ፡ በሩሲያ ፡ የሆነውን ፡ እንውሰድ ። በፊት ፡ በተቻለ ፡ መጠን ፡ ለጥቁር ፡ መቶዎች ፡ ይሰጡ ፡ የነበሩት ፡ የሥልጣን ፡ ሹመቶች ፡ አሁን ፡ የካዴቶች[13] ፣ ሜንሼቪኮችና[4] ፡ የሶሺያሊስት-አብዮታውያን ፡[5] የአላማቸው ፡ ግብ ፡ ሆነዋል ። በመሠረቱ ፡ ምንም ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ ያለው ፡ የጥገና ፡ ለውጥ ፡ ለማድረግ ፡ አያስቡም ፣ ጥረታቸው ፡ ለውጡን « እስከ ፡ ሕገ ፡ መንግሥት ፡ አዘጋጅ ፡ ምክር ፡ ቤቱ ፡ ስብሰባ ፡ ድረስ » ለማዘግየትና ፣ ከዚያም ፡ የምክር ፡ ቤቱን ፡ ስብሰባ ፡ ቀስ ፡ በቀስ ፡ እስከ ፡ ጦርነቱ ፡ መጨረሻ ፡ ድረስ ፡ ለመጎተት ፡ ነው! ምርታቸውን ፡ ለመከፋፈል ፣ ብዙ ፡ ደመወዝ ፡ የሚከፈልበት ፡ የሚኒስተርነትን ፣ የረዳት ፡ ሚኒስተርነትን ፣ አገረ ፡ ገዥነትን ፣ ወዘተ ... ሹመት ፡ ለመያዝ ፡ ግን ፡ አልዘገዩም ፣ የምክር ፡ ቤት ፡ ስብሰባም ፡ አልጠበቁም! በመላ ፡ ሀገሩ ፡ በእያንዳንዱ ፡ ማእከላዊና ፡ ክፍለ ፡ ሀገር ፡ አስተዳደሮች ፡ ከላይ ፡ እስከ ፡ ታችም ፡ የተካሄደው ፣ ይህ « ምርትን » የመካፈልና ፡ የመከፋፈል ፡ ተግባር ፡ አገዛዙን ፡ ለማስተባበር ፡ የተደረገ ፡ ጨዋታ ፡ ብቻ ፡ ነበር ። የግማሹ ፡ ዓመት ፡ — ከየካቲት ፡ ፳፯ እስከ ፡ ነሐሴ ፡ ፳፯ ነባራዊ ፡ መደም

ደሚያ ፡ ያለ ፡ ጥርጥር ፡ እንዲህ ፡ ነው ፤ የጥገና ፡ ለውጦች ፡ ወደ ፡ ጐን ፡ ተትተዋል ፤ የሥልጣን ፡ ሹመቶች ፡ ግን ፡ ተከፋፍ ለው ፡ ጨርሰዋል ፤ በመከፋፈል ፡ ላይ ፡ የተደረጉ « ስህተቶች » እንደገና ፡ ጥቂት ፡ መከፋፈል ፡ በማድረግ ፡ ታርመዋል ።

ነገር ፡ ግን ፡ የቢሮክራሲው ፡ አውታር ፡ ይበልጥ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ የቡርዥዋና ፡ የንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ፓርቲዎች (ሩሲ ያን ፡ እንደ ፡ ምሳሌ ፡ ከወሰድን — በካዴቶች ፤ በሶሺያሊ ስት-አብዮታውያንና ፡ በሜንሼቪኮች ፡ መካከል) « እንደ ገና ፡ መከፋፈል » በተደረገ ፡ መጠን ፤ ለጭቁን ፡ መደቦ ችና ፡ ለመሪያቸው ፡ ለወዝ ፡ አደሩ ፡ ይበልጥ ፡ ግልፅ ፡ የሚሆነው ፤ በመላ ፡ በቡርዥዋ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ላይ ፡ ያላ ቸው ፡ የማይታረቅ ፡ ጥላቻ ፡ ነው ። ከዚህም ፡ የተነሳ ፤ ሁሉም ፡ የቡርዥዋ ፡ ፓርቲዎች ፤ በጣም ፡ ዴሞክራቲክና « አብዮታዊ-ዴሞክራቲክ » የሆኑትም ፡ ሳይቀሩ ፤ በአብዮታ ዊው ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ላይ ፡ የጭቆናው ፡ እርምጃ ፡ ማጥበ ቅን ፤ የጭቆና ፡ አውታሩ ፤ ማለትም ፡ ያ ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ ማጠንከርን ፡ ያስፈልጋቸዋል ። ይህ ፡ የሁኔታ ዎች ፡ አካሄድ ፡ አብዮቱ ፡ በመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ ላይ « የማፍረስ ፡ ኃይሎችን ፡ ሁሉ ፡ እንዲያከማች » ያስገድ ደዋል ፤ የአብዮቱ ፡ ዓላማ ፡ ያለውን ፡ የመንግሥት ፡ መኪ ና ፡ ማሻሻል ፡ አይደለም ፤ የመንግሥት ፡ መኪናውን ፡ ማፍ ረስና ፡ መደምሰስ ፡ እንጂ ።

ጉዳዩ ፡ በዚህ ፡ መንገድ ፡ እንዲቀርብ ፡ ያደረገው ፤ ሎጂካል ፡ አስተሳሰብ ፡ አይደለም ፤ እውነተኛ ፡ እድገት ፤ ህያው ፡ የሆነ ፡ የ ፲፰፻፵፰-፶፩ ዓ. ም. ልምድ ፡ እንጂ ። ማርክስ ፡ ምን ፡ ያህል ፡ በከፍተኛ ፡ ጥንቃቄ ፡ የታሪካዊውን ፡ ልምድ ፡ ተጨባጭ ፡ መሰረት ፡ እንደሚከተል ፡ የሚያሳ የን ፡ ሐቅ ፤ በ ፲፰፻፶፪ ዓ. ም. ይህ ፡ የሚደመሰሰው ፡ የመ ንግሥት ፡ መኪና ፡ በምን ፡ መተካት ፡ እንደአለበት ፡ የሚ ለውን ፡ ጥያቄ ፡ ገና ፡ በግልጽ ፡ አላነሳውም ። ያኔ ፡ የነበረው ፡ ልምድ ፡ ይህን ፡ ጥያቄ ፡ ለማንሳት ፡ መሠረት ፡ ገና ፡ አልሰ



ጠም ፡ ነበርና ፤ በ[illegible] ታሪክ ፡ ጥያቄ ውን ፡ በአጀንዳ ፡ እንደ[illegible] ዓ. ም. በትክክለኛ ፡ ሳይንሳዊ ፡ አመለካከት ፡ ማረጋገጥ ፡ ይቻል ፡ የነበረው ፤ የወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት ፡ በመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ ላይ « የማፍረስ ፡ ኃይሎችን ፡ አከማችቶ » የመንግሥት ፡ መኪናን ፡ « የማፍረስ » ተግባር ፡ ደረጃ ፡ ላይ ፡ መድረ ሱን ፡ ነው ።

እዚህ ፡ ላይ ፡ ማርክስ ፡ ልምድን ፤ አመለካከቶችንና ፡ መደምደምያዎችን ፡ ከሶስቱ ፡ ዓመት ፡ ፲፰፻፵፰-፶፩ ዓ. ም. የፈረንሳይ ፡ ታሪክ ፡ ሰፋ ፡ ላለ ፡ ሁኔታ ፡ ማጠቃለሉ ፡ ትክክል ፡ ነውን ፡ የሚል ፡ ጥያቄ ፡ ሊነሣ ፡ ይችላል ። ይህ ን ፡ ጥያቄ ፡ ከመተንተናችን ፡ በፊት ፡ መጀመሪያ ፡ አንድ ፡ የኤንግልስን ፡ አስተያየት ፡ እናስታውሳለን ፤ ቀጥለን ፡ ጭብጥ ፡ ነገሮችን ፡ እንመረምራለን ።

ኤንግልስ ፡ ለ፫ኛው ፡ እትም « የ፲፰ኛው ፡ ብሩሜ ር » ባቀረበው ፡ መቅድም ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ይጽ ፋል ፤ « ፈረንሳይ ፤ ታሪካዊ ፡ የመደብ ፡ ትግል ፡ ከ ሌሎች ፡ አገሮች ፡ ይበልጥ ፡ በማንኛውም ፡ ጊዜ ፡ እስከ ፡ ፍጹም ፡ መጨረሻ ፡ ድረስ ፡ የተካሄደባት ፡ አገር ፡ ናት ። በውስጣቸው ፡ ይህ ፡ የመደብ ፡ ትግል ፡ የተካ ሄደባቸውና ፡ የዚህን ፡ ውጤት ፡ የተጠቃለለባቸው ፤ ተለዋዋጭ ፡ የፖለቲካ ፡ ቅርፆች ፡ በጣም ፡ ኃይለኛ ፡ በሆኑ ፡ መንገዶች ፡ መልክ ፡ የያዙባት ፡ አገር ፡ ናት ። በመካከለኛው ፡ ክፍለ ፡ ዘመን ፡ የፊውዳሊዝም ፡ እምብር ት ፡ የነበረችው ፤ ከዳግማዊ ፡ ትንሳኤ (Renaissance) ወዲ ህ ፡ ለተዋሀደ ፡ የዘውድ ፡ አገዛዝ ፡ ጥሩ ፡ ምሳሌ ፡ የነበረ ች ፡ ሃገር ፤ ፈረንሳይ ፤ በታላቁ ፡ አብዮት ፡ ፊውዳሊዝም ን ፡ አውድማ ፤ በሌሎች ፡ የአውሮፓ ፡ አገሮች ፡ ውስጥ ፡ ተደርጐ ፡ የማይታወቅ ፡ ፍጹም ፡ ክላሲካዊ ፡ የሆነ ፡ የቡርዥዋ ፡ ገዥነት ፡ መሠረተች ። እንደዚሁም ፡ በማደ

ግ ፡ ላይ ፡ ያለው ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ከገዥው ፡ ቡርዥዋ ፡ ጋር ፡ የሚያደርገው ፡ ትግል ፤ የትም ፡ አገር ፡ ታይቶ ፡ የማይታወቅ ፤ የከረረ ፡ መልክ ፡ ታይቶበታል ።» (ገጽ ፡ ፩ ፤ ፲፱፻፯ ዓ. ም.)

የመጨረሻው ፡ አስተያየት ፡ ጊዜው ፡ አልፎአል ፤ ምክንያቱም ፡ ከ ፲፰፻፸፩ ዓ. ም. ወዲህ ፡ የፈረንሳይ ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ አብዮታዊ ፡ ትግል ፡ ለጊዜው ፡ ዝግ ፡ ብሏልና ፤ ቢሆንም ፡ ይህ ፡ ዝግታ ፡ ምን ፡ ያህልም ፡ ረጅም ፡ ቢሆን ፤ ወደፊት ፡ በሚመጣው ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ አብዮት ፡ ፈረንሳይ ፡ የመደብ ፡ ትግል ፡ እስከ ፡ ፍጹም ፡ መጨረሻ ፡ የሚደረግባት ፡ ክላሲካዊ ፡ ሀገር ፡ ከመሆን ፡ አያግዳትም ።

ሆኖም ፡ እስቲ ፡ በ ፲፱ኛው ፡ ምእት ፡ ዓመት ፡ መጨረሻና ፡ በ ፳ ኛው ፡ ምእት ፡ ዓመት ፡ መጀመሪያ ፡ ላይ ፡ የነበረው ፤ የሰለጠኑት ፡ አገሮች ፡ ታሪክ ፡ ገረፍ ፡ አድርገን ፡ እንመልከተው ። እዚህም ፡ ያ ፡ ሂደት ፡ በቀስታ ፤ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ዓይነት ፡ መልክ ፤ ይበልጥ ፡ ሰፋ ፡ ባለ ፡ መስክ ፡ መካሄዱን ፡ እናያለን — ባንድ ፡ በኩል ፡ በሪፑብሊካዊ ፡ አገሮች (በፈረንሳይ ፤ በአሜሪካ ፤ በስዊዘርላንድ) እና ፡ በዘውድ ፡ አገዛዝ ፡ አገሮች (እንግሊዝ ፤ እስከተወሰነ ፡ ደረጃ ፡ ድረስ — ጀርመን ፤ ኢጣልያ ፤ የእስካንዲናቪያ ፡ አገሮች ፤ ወዘተ) «የፓርላማ ፡ ሥልጣን» እድገት ፤ በሌላ ፡ በኩል ፡ የቡርዥዋ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ መሠረቱ ፡ ሳይለወጥ ፤ የሥልጣን ፡ ሹመቱን « ምርት » የተካፈሉና ፡ የተከፋፈሉ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ የቡርዥዋና ፡ የንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ፓርቲዎች ፡ ለሥልጣን ፡ መታገል ፤ በመጨረሻም ፤ « የሥራ ፡ አስፈጻሚ ፡ ሥልጣን » ፤ የቢሮክራሲውና ፡ ወታደራዊ ፡ አውታርም ፡ መሻሻልና ፡ መጠንከር ፡ ነው ።

እነዚህ ፡ ባህርያት ፡ ለሁሉም ፡ የካፒታሊስት ፡ መንግሥት ፡ ዘመናዊ ፡ ኤቮሉሽን ፡ ባጠቃላይ ፡ የጋራ ፡ መሆናቸውን ፡ ቅንጣት ፡ ያህል ፡ ጥርጥር ፡ የለም ። ፈረንሳይ ፡ በሶ





ስቱ ፡ ዓመታት ፤ ፲፰፻፵፰-፶፩ ዓ. ም. ፤ ውስጥ ፡ የ ፡ ለሁሉም ፡ ካፒታሊስት ፡ ዓለ[illegible] ልዩ ፡ [illegible] ፡ የእድገት ፡ ሂደት ፡ ፈጠን ፤ ጠንከር ፤ ሰብሰብ ፡ ባለ ፡ መልክ ፡ አሳይቷል ።

በተለይም ፡ ኢምፔሪያሊዝም — ይህ ፡ የባንክ ፡ ካፒታል ፡ ዘመን ፤ የትላልቅ ፡ ካፒታሊስት ፡ ሞኖፖሊዎች ፡ ዘመን ፤ የሞኖፖሊ ፡ ካፒታሊዝም ፡ ወደ ፡ መንግሥታዊ-ሞኖፖሊያዊ ፡ ካፒታሊዝም ፡ ያደገበት ፡ ዘመን — በግልፅ ፡ ያሳየው « የመንግሥት ፡ መኪና » በጣም ፡ መጠንከርንና ፡ በዘውድ ፡ አገዛዝ ፡ ባሉትም ፡ ሆነ ፤ ነፃ ፡ ናቸው ፡ በሚባሉት ፡ ሪፑብሊካዊ ፡ አገሮች ፡ ውስጥ ፤ በወዝ ፡ አደሩ ፡ ላይ ፡ የሚያደርጉት ፡ ጭቆናን ፡ ለማጠንከር ፡ የቢሮክራሲውና ፡ የወታደራዊው ፡ አውታሩ ፡ ተሰምቶ ፡ በማይታወቅ ፡ አኳኋን ፡ ማደጉን ፡ ነው ።

የዓለም ፡ ታሪክ ፡ ከ ፲፰፻፶፪ ዓ. ም. ይበልጥ ፡ በአሁኑ ፡ ጊዜ ፡ የመንግሥት ፡ መኪናውን « ለማፍረስ » የወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት « መላ ፡ ኃይሉን ፡ ወደ ፡ ማከማቸት » ተወዳዳሪ ፡ በሌለው ፡ ስፋት ፤ ማምራቱ ፡ ጥርጥር ፡ የለውም ።

ወዝ ፡ አደሩ ፡ የፈረሰውን ፡ በምን ፡ ይተካዋል ፡ ለሚለው ፡ ጥያቄ ፡ የፓሪስ ፡ ኮሙን ፡ ከፍተኛ ፡ ትምህርታዊ ፡ መሠረት ፡ ሰጥቷል ።

## ፫. ማርክስ ፡ በ ፲፰፻፶፪ ዓ. ም. ጥያቄውን ፡ እንዳቀረበው ።*

በ ፲፱፻፯ ዓ. ም. ሜሪንግ «Neue Zeit»[14] (XXV, ፪ ፤ ገጽ ፡ ፪፻፩) በተባለው ፡ መጽሔት ፡ ማርክስ ፡ በመጋቢት ፡ ፭ ቀን ፤ ፲፰፻፶፪ ዓ. ም. ለቬይደመየር ፡ ከጻፈው ፡ ደብዳቤ ፡

---

* ይህ ፡ አርእስት ፡ በሁለተኛው ፡ እትም ፡ የተጨመረ ፡ ነው ።

ጥቅስ ፡ አትሞ ፡ ነበር ፡፡ በዚህ ፡ ደብዳቤ ፡ ውስጥ ፤ በነገራችን ፡ ላይ ፤ የሚከተለው ፡ ግሩም ፡ የሆነ ፡ አስተያየት ፡ ይገኝበታል ፤

«ይህን ፡ በሚመለከት ፤ በዘመናዊው ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ውስጥ ፡ መደቦች ፡ መኖራቸውን ፤ በነሱም ፡ መካከል ፡ የመደብ ፡ ትግል ፡ መኖሩን ፡ ፈለሰፈ ፡ ተብሎ ፡ ለኔ ፡ አስተያየት ፡ መስጠት ፡ የለበትም ፡፡ ከኔ ፡ በፊት ፡ ቀደም ፡ ብሎ ፡ የቡርዥዋ ፡ የታሪክ ፡ ሊቃውንት ፡ ስለ ፡ መደብ ፡ ትግል ፡ ታሪካዊ ፡ እድገት ፡ በሰፊው ፡ ገልጸዋል ፤ የቡርዥዋ ፡ የኤኮኖሚ ፡ ሊቃውንትም ፡ ደግሞ ፡ ስለ ፡ መደቦች ፡ የኤኮኖሚ ፡ አውታር ፡ ጽፈዋል ፡፡ እኔ ፡ ያደረግኩት ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ ቢኖር ፡ የሚከተለውን ፡ ማረጋገጤ ፡ ነው ፡፡ ይኸውም ፤ ፩. የመደቦች ፡ መኖር ፡ ከተወሰነ ፡ ታሪካዊ ፡ የምርት ፡ እድገት ፡ ደረጃ ፡ ጋር ፡ ብቻ ፡ የተያያዘ ፡ መሆኑን ፤ (historiche Entwicklungsphasen der Produktion) ፤ ፪. የመደብ ፡ ትግል ፡ የግድ ፡ ወደ ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ የሚያመራ ፡ መሆኑን ፤ ፫. ይህ ፡ የበላይ ፡ ገዥነቱ ፡ ራሱ ፡ የሚያቅደው ፡ ሁሉን ፡ መደቦች ፡ አጥፍቶ ፡ ወደ ፡ መደብ ፡ አልባው ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ለመሸጋገር ፡ ብቻ ፡ እንደሆነም ፡ ነው ፡፡»

ማርክስ ፡ በነዚህ ፡ ቃላት ፤ እጅግ ፡ በጣም ፡ ግልፅ ፡ በሆነ ፡ መንገድ ፡ የገለፀው ፤ አንደኛ — የሱ ፡ ቴዎሪ ፡ ከቡርዥዋው ፡ ግምባር ፡ ቀደምና ፡ በጣም ፡ ጥልቅ ፡ ተመራማሪዎች ፡ ቴዎሪ ፡ የሚለይበትን ፡ ዋናና ፡ መሰረታዊ ፡ ሃሳብን ፡ ሲሆን ፤ ሁለተኛ — የመንግሥት ፡ ቴዎሪው ፡ ንጥረ ፡ ሀሳብን ፡ ነው ፡፡

የማርክስ ፡ ቴዎሪ ፡ ዋና ፡ ነጥብ ፡ የመደብ ፡ ትግል ፡ ነው ፤ እያሉ ፡ ሁሌ ፡ ይናገራሉ ፤ ይጽፋሉም ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡



ይህ ፡ ትክክል ፡ አይደለም ፡፡ ከዚህ ፡ ስህተት ፡ የተነሳ ፡ ሁል ጊዜ ፡ የሚመነጨው ፡ [illegible] ማርክሲዝምን ፡ ማጣመምና ፡ ማርክሲዝም ፡ ለቡርዥዋው ፡ እንዲስማማ ፡ ሆኖ ፡ ማውገርገርን ፡ ነው ፡፡ ምክንያቱም ፡ የመደብ ፡ ትግል ፡ ቴዎሪን ፡ የፈለሰፈው ፡ ማርክስ ፡ አይደለም ፤ ከማርክስ ፡ በፊት ፡ ቡርዥዋው ፡ ነው ፤ በጠቅላላ ፡ አነጋገር ፡ ደግሞ ፡ ለቡርዥዋው ፡ ይህ ፡ ተስማሚ ፡ ነው ፡፡ የመደብ ፡ ትግልን ፡ ብቻ ፡ የሚቀበል ፡ ገና ፡ ማርክሲስት ፡ አይደለም ፤ ገና ፡ ከቡርዥዋው ፡ አስተሳሰብ ፡ ክልልና ፡ ከቡርዥዋው ፡ ፖለቲካ ፡ ያልተላቀቀ ፡ ሆኖ ፡ ሊገኝ ፡ ይችላል ፡፡ ማርክሲዝምን ፡ በመደብ ፡ ትግል ፡ ብቻ ፡ መወሰን ፤ ማለት ፡ ማርክሲዝምን ፡ መጉረድ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ማጣመም ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ማርክሲዝምን ፡ ለቡርዥዋው ፡ ተስማሚ ፡ አድርጎ ፡ ዝቅ ፡ ማድረግ ፡ ማለት ፡ ነው ፡፡ ማርክሲስት ፡ ነው ፡ ሊባል ፡ የሚቻለው ፡ በመደብ ፡ ትግል ፡ የሚያምን ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፤ በዚህ ፡ እምነት ፡ ላይ ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ እምነት ፡ ሲጨምርበት ፡ ብቻ ፡ ነው ፡፡ ይህ ፡ ነው ፡ በማርክሲስትና ፡ በተራው ፡ ንዑስ (እንደዚሁም ፡ ትልቅ) ቡርዥዋ ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ በጣም ፡ ጥልቅ ፡ የሆነ ፡ ልዩነት ፡፡ በዚሁ ፡ መሠረታዊ ፡ ነጥብ ፡ ነው ፡ ማርክሲዝም ፡ እውነት ፡ ተረድተንና ፡ ተቀብለነው ፡ እንደሆን ፡ የምንፈተነው ፡፡ ስለሆነም ፡ የአውሮፓ ፡ ታሪክ ፡ በወዝ ፡ አደሩ ፡ ፊት ፡ ይህን ፡ ጥያቄ ፡ እንደ ፡ ገቢራዊ ፡ ጉዳይ ፡ ባቀረበበት ፡ ጊዜ ፡ ሁሉም ፡ አድርባዮችና ፡ ጠጋኞች ፡ ብቻ ፡ ሳይሆኑ ፤ ሁሉም ፡ ካውትስካውያኖችም (በጠጋኝነትና ፡ በማርክሲዝም ፡ መካከል ፡ ሲያወላውሉ ፡ የነበሩ ፡ ሰዎችም) ጭምር ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ ከሚቃወሙት ፡ አሳፋሪ ፡ ጮርቃዎችና ፡ ንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ዴሞክራቶች ፡ ጋር ፡ መሆናቸውን ፡ ማረጋገጣቸው ፡ አያስገርምም ፡፡ በነሀሴ ፡ ፲፱፻፲፰ ዓ. ም. ፤ ማለትም ፡ የዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ የመጀመሪያ ፡ እትም ፡ ከወጣ ፡ በኋላ ፡ ብዙ ፡ ዓመታት ፡

አልፎ ፡ የተጻፈው «የወዝ ፡ አደሩ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት» የተባለው ፡ የካውትስኪይ ፡ ጽሑፍ ፡ ንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ማርክሲዝምን ፡ እንዴት ፡ እንደሚያጣምሙትና ፡ በቃላት ፡ በሱ ፡ እየተመጻደቁ ፡ በተግባር ፡ ግን ፡ እንዴት ፡ ክፉኛ ፡ እንደሚክዱት ፡ የሚያሳይ ፡ ጥሩ ፡ ምሳሌ ፡ ነው ። (« የወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮትና ፡ ከሃዲው ፡ ካውትስኪይ » የተባለውን ፡ የኔን ፡ ጽሁፍ ፡ ተመልከት ። ፔትሮግራድ ፤ ሞስኮ ፡ ፲፱፻፲፰ ዓ. ም.) ።

ዘመናዊው ፡ አድርባይነት ፤ በዋናው ፡ አፈቀላጤው ፤ ቀድሞ ፡ ማርክሲስት ፡ በነበረው ፡ ካርል ፡ ካውትስኪይ ፡ አማኻኝነት ፤ ከላይ ፡ ማርክስ ፡ ከጠቀሰው ፡ ከቡርዥዋው ፡ አቋም ፡ ጋር ፡ ይሞዳሞዳል ፤ ምክንያቱም ፡ ይህ ፡ አድርባይነት ፡ የመደብ ፡ ትግል ፡ የሚወስነው ፡ በቡርዥዋው ፡ ግንኙነት ፡ ክልል ፡ ነው ። (በዚህ ፡ ክልል ፡ ውስጥ ፤ ከዚህ ፡ ሳይወጣ ፡ አንድም ፡ የተማረ ፡ ሊበራል ፡ የመደብ ፡ ትግልን « በመሠረቱ » አልቀበልም ፡ አይልም!) አድርባይነት ፡ የመደብ ፡ ትግል ፡ እጅግ ፡ መሠረታዊ ፡ እስከሆነው ፡ ነጥብ ፤ እስከ ፡ ከካፒታሊዝም ፡ ወደ ፡ ኮሙኒዝም ፡ ሽግግር ፡ ወቅት ፡ ድረስ ፤ እስከ ፡ የቡርዥዋው ፡ መገልበጥና ፡ ሙሉ ፡ በሙሉ ፡ መደምሰስ ፡ ድረስ ፡ አያስፋፋውም ። በእውነቱ ፡ ግን ፡ ይህ ፡ ወቅት ፡ የማይታለፍ ፤ ታይቶ ፡ የማይታወቅ ፡ መራራ ፡ የመደብ ፡ ትግል ፤ ታይቶ ፡ በማይታወቅ ፡ በተካረረ ፡ መልክ ፡ የሚካሄድበት ፡ ወቅት ፡ ነው ፤ ስለዚህም ፡ የዚሁ ፡ ወቅት ፡ መንግሥት ፡ የግድ ፡ በአዲስ ፡ መንገድ ፡ ዴሞክራቲክ (ለወዝ ፡ አደሩና ፡ ምንም ፡ ለሌላቸው ፡ ባጠቃላይ) ፤ በአዲስ ፡ መንገድ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ መንግሥት (በቡርዥዋው ፡ ላይ) መሆን ፡ አለበት ።

እንቀጥል ። የማርክስን ፡ የመንግሥት ፡ ቴዎሪ ፡ ንጥረ-ሀሳብ ፡ ተገንዝበዋል ፡ ለማለት ፡ የሚቻለው ፡ የአንድን ፡ መደብ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ የሚያስፈልገው ፡ ለማንኛውም ፡ በመደብ ፡ ለተከፈለ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፤





ቡርዥዋውን ፡ ለጣል ፡ ለወ[illegible] ፡ [illegible] ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፤ ከካፒታሊዝም ፡ እስከ « መደብ ፡ አልባው ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ » እስከ ፡ ኮሙኒዝም ፡ ላለው ፡ መላ ፡ ታሪካዊ ፡ ወቅትም ፡ ጭምር ፡ መሆኑን ፡ የገባቸው ፡ ብቻ ፡ ናቸው ። የቡርዥዋው ፡ መንግሥታት ፡ በመልክ ፡ በጣም ፡ የተለያዩ ፡ ናቸው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ውስጠ ፡ መሠረታቸው ፡ አንድ ፡ ነው ። ይኸውም ፤ እነዚህ ፡ መንግሥታት (መልካቸው ፡ ቢለያይም) ያው ፡ መሠረታቸው ፡ የግድ ፡ የቡርዥዋው ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ ነው ። ከካፒታሊዝም ፡ ወደ ፡ ኮሙኒዝም ፡ መሸጋገር ፡ በእርግጥ ፡ ብዙና ፡ የተለያየ ፡ መልክ ፡ ያላቸው ፡ የፖለቲካ ፡ መልኮችን ፡ ይሰጣል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ውስጠ ፡ መሠረቱ ፡ የግድ ፡ አንድ ፡ መሆን ፡ አለበት ፤ ይኸውም ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ III.

## መንግሥትና ፡ አብዮት ።

## የፓሪስ ፡ ኮሙን ፡ የ ፲፰፻፸፩ ዓ. ም. ልምድ ።

## የማርክስ ፡ ትንተና ።

### ፩. የኮሙናሮች ፡ ሙከራ ፡ ጀግንነት ፡ ምን ፡ ላይ ፡ ነው?

በ ፲፰፻፸፪ ዓ. ም. በበልግ ፡ ወራት ፡ ከኮሙኑ ፡ ጥቂት ፡ ወራት ፡ በፊት ፤ ማርክስ ፡ መንግሥቱን ፡ ለመጣል ፡ የሚደረግ ፡ ማንኛውም ፡ ሙከራ ፡ የተስፋ ፡ መቁረጥ ፡ ቂልነት ፡ መሆኑን ፡ በማረጋገጥ ፡ የፓሪስ ፡ ወዝ ፡ አደሮችን ፡ ማስጠንቀቁ ፡ የታወቀ ፡ ነው ።[15] ነገር ፡ ግን ፡ በመጋቢት ፡ ፲፰፻፸፩ ዓ. ም. በወዝ ፡ አደሩ ፡ ላይ ፡ ቆራጥ ፡ ውጊያ ፡ በተጫነበትና ፡ እሱም ፡ በተቀበለበት ፡ ጊዜ ፤ አመጽ ፡ በሥራ ፡ ላይ ፡ በዋለበት ፡ ጊዜ ፤ ምንም ፡ እንኳ ፡ ምልክቶቹ ፡ መጥፎ ፡ ቢሆኑም ፡

ማርክስ ፡ በታላቅ ፡ ደስታ ፡ ነበር ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ አብዮት ፡ የተቀበለው ። እንደ ፡ ስመ-ጥፉው ፡ ማርክሲዝምን ፡ የካደ ፡ ሩሲያዊው ፡ ፕሌኻኖቭ ፤ ማርክስ « ያለ ፡ ጊዜው ፡ የተነሳ » ንቅናቄ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ በጥራዝ ፡ ነጠቅነት ፡ ውግዘት ፡ ላይ ፡ እኝኝ ፡ አላለም ። ማርክሲዝምን ፡ የካደው ፡ ፕሌኻኖቭ ፡ በኅዳር ፡ ፲፰፻፸፩ ዓ. ም. የወዝ ፡ አደሩንና ፡ የአርሶ ፡ አደሩን ፡ ትግል ፡ በማበረታታት ፡ መንፈስ ፡ ጽፎ ፡ በኋላ ፡ በታህሳስ ፡ ፲፰፻፸፩ ዓ. ም. ግን ፡ በሊበራልነት « መሳርያ ፡ ማንሳት ፡ አያስፈልግም ፡ ነበር » እያለ ፡ ጮኸ ።

ቢሆንም ፡ ማርክስ ፡ የኮሙናሮችን ፡ ጀግንነት ፤ ራሱም ፡ እንዳለው « ሰማይን ፡ በማናወፃቸው » በአድናቆት ፡ ብቻ ፡ አልተወሰነም[16] ። ምንም ፡ እንኳ ፡ ግቡን ፡ ባይመታም ፡ ይህ ፡ ሰፊ ፡ አብዮታዊ ፡ ንቅናቄ ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ አስፈላጊ ፡ የሆነ ፡ ታሪካዊ ፡ ልምድ ፡ እንደሆነ ፤ የዓለም ፡ አቀፍ ፡ ወዝ ፡ አደራዊ ፡ አብዮት ፡ አንድ ፡ እርምጃ ፡ ወደፊት ፡ መራመዱን ፤ ከብዙ ፡ ምእት ፡ ፕሮግራሞችና ፡ ሀሳቦች ፡ ይበልጥ ፡ ይህ ፡ ገቢራዊ ፡ እርምጃ ፡ በጣም ፡ አስፈላጊ ፡ መሆኑን ፡ ማርክስ ፡ ተገንዝቧል ። ስለሆነም ፡ ይህን ፡ ልምድ ፡ በመተንተን ፤ ከሱም ፡ የታክቲክ ፡ ትምህርቶችን ፡ ቀስሞ ፡ በዚህ ፡ ልምድ ፡ መሰረት ፡ ቴዎሪውን ፡ እንደገና ፡ መመርመር — ይህ ፡ ነበር ፡ የማርክስ ፡ ዋናው ፡ ጥረት ።

ማርክስ « በኮሙኒስት ፡ ማኒፌስቶ » አንድ « እርማት » ማድረግ ፡ አስፈላጊ ፡ መሆኑን ፡ የተገነዘበው ፤ « እርማቱም » ያደረገው ፡ የፓሪስ ፡ ኮሙናሮችን ፡ አብዮታዊ ፡ ልምድ ፡ በመመርመር ፡ ነው ።

ለአዲሱ ፡ የጀርመን « የኮሙኒስት ፡ ማኒፌስቶ » እትም ፡ በሁለቱም ፡ ደራሲዎቹ ፡ የተጻፈው ፡ የመጨረሻ ፡ መቅድም ፡ በሰኔ ፡ ፳፬ ቀን ፡ ፲፰፻፸፪ ዓ. ም. ነው ። በዚህ ፡ መቅድም ፡ ውስጥ ፡ ደራሲዎቹ ፤ ካርል ፡ ማርክስና ፡ ፍሬደሪክ ፡ ኤንግልስ « የኮሙኒስት ፡ ማኒፌስቶ » ፕሮግራም « አሁን ፡ በአንዳንድ ፡ ቦታዎች ፡ አርጅቷል » ይላሉ ።



በመቀጠልም ፡ የሚከተለውን ፡ ይጽፋሉ ፤ « ... በተለይም ፡ ኮሙ[illegible] ፡ ያረጋገጠው ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ አለ ፤ ይኸውም « ወዝ ፡ አደሩ ፡ ያለውን ፡ ዝግጁ ፡ የመንግሥት ፡ መኪናን ፡ በመውረስ ፡ ለራሱ ፡ ጥቅም ፡ ሊገለገልበት ፡ የማይችል ፡ መሆኑን ፡ ነው » ... »

በዚህ ፡ ጥቅስ ፡ በሁለተኛው ፡ ትእምርተ ፡ ጥቅስ ፡ ውስጥ ፡ ያሉትን ፡ ቃላት ፡ ደራሲዎቹ ፡ የወሰድዋቸው « የርስ ፡ በርስ ፡ ጦርነት ፡ በፈረንሳይ » ከተባለው ፡ የማርክስ ፡ መጽሐፍ ፡ ውስጥ ፡ ነው ።

ስለሆነም ፤ ማርክስና ፡ ኤንግልስ ፡ የፓሪስ ፡ ኮሙንን ፡ አንድ ፡ መሠረታዊና ፡ ዋና ፡ ትምህርት ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ከፍተኛ ፡ ጠቃሚነት ፡ እንዳለው ፡ ስለተገነዘቡ ፤ « በኮሙኒስት ፡ ማኒፌስቶ » እንደ ፡ ጠቃሚ ፡ እርማት ፡ አስገብተውታል ።

በተለይ ፡ ይህ ፡ ትልቅ ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ ያለው ፡ እርማት ፡ በአድርባዮቹ ፡ እንደተጣመመ ፡ መጥቀስ ፡ ተገቢ ፡ ነው ። የዚህ ፡ እርማት ፡ ፍች ፡ ከመቶ ፡ ለዘጠና ፡ ዘጠኙ ፡ ካልሆነ ፤ ቢያንስ ፡ ከአስሩ ፡ ለዘጠኙ « የኮሙኒስት ፡ ማኒፌስቶ » አንባቢዎች ፡ ምናልባት ፡ የታወቀ ፡ አይደለም ። ስለዚህ ፡ ማጣመም ፡ ተግባር ፡ በሰፊው ፤ ስለማጣመም ፡ ጉዳይ ፡ በሚመለከተው ፡ ልዩ ፡ ምዕራፍ ፡ ውስጥ ፡ እንመለስበታለን ። ግን ፡ እዚህ ፡ ሳንጠቅሰው ፡ የማናልፈው ፡ አሁን ፡ ባቀረብነው ፡ ዝነኛ ፡ የማርክስ ፡ ጥቅስ ፡ ላይ ፡ የተሰነዘረ ፡ ስድ « አስተያየትን » ነው ፤ ይኸውም ፡ ማርክስ ፡ ሥልጣን ፡ በመጨበጥ ፡ ፈንታ ፡ ቀስተኛ ፡ እድገትና ፡ የመሳሰሉትን ፡ ለሚለው ፡ ሀሳብ ፡ የበለጠ ፡ ዋጋ ፡ እንደሰጠ ፡ አድርጎ ፡ የሚቆጥረውን ፡ ነው ።

እውነቱ ፡ የዚህ ፡ ቀጥተኛ ፡ ተቃራኒ ፡ ነው ። የማርክስ ፡ ሀሳብ ፡ የሚለው ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ « ያለውን ፡ ዝግጁ ፡ የመንግሥት ፡ መኪና » እንድያው ፡ በመያዝ ፡ ብቻ ፡

መወሰን ፡ የለበትም ፤ መሰባበር ፤ ማፈራረስ ፡ አለበት ፡ ነው ፡ እንጂ ።

ሚያዝያ ፡ ፲፪ ቀን ፡ ፲፰፻፸፩ ዓ. ም. ፤ ማለትም ፡ ልክ ፡ ኮሙን ፡ በሚካሄድበት ፡ ጊዜ ፤ ማርክስ ፡ ለኩገልማን ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ጽፏል ፤

« ... « የ ፲፰ ኛው ፡ ብሩሜር » የመጨረሻውን ፡ ምዕራፍ ፡ ብትመለከት ፡ የሚከተለውን ፡ የኔን ፡ መግለጫ ፡ ታገኛለህ — የሚቀጥለው ፡ የፈረንሳይ ፡ አብዮት ፡ ሙከራ ፤ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ እንደነበረው ፡ የቢሮክራሲያዊ-ወታደራዊ ፡ መኪናን ፡ ከአንዱ ፡ እጅ ፡ ወደ ፡ ሌሎች ፡ ለማዘዋወር ፡ ሳይሆን ፤ ለማፈራረስ ፡ ነው » (ስርዝ ፡ የማርክስ ፤ ጀርመንኛው ፡ zerbrechen) ። « ይህ ፡ ነው ፡ የማንኛውም ፡ የአህጉሩ ፡ እውነተኛ ፡ ሕዝባዊ ፡ አብዮት ፡ ተቀዳሚ ፡ ተግባር ። የኛ ፡ ጀግና ፡ የፓሪስ ፡ ጓዶችም ፡ ሙከራ ፡ ይህ ፡ ነው ። » («Neue Zeit», XX ፤ ፩ ፤ ፲፱፻፩-፲፱፻፪ ዓ. ም. ፤ ገጽ ፡ ፯፻፱) (ማርክስ ፡ ለኩገልማን ፡ የጻፉት ፡ ደብዳቤዎች ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ ታትመው ፡ ሲወጡ ፡ አንዱን ፡ እትም ፡ ያዘጋጀሁትና ፡ መቅድም ፡ የጻፍኩት ፡ እኔው ፡ ነኝ ።)

« የቢሮክራሲያዊ-ወታደራዊ ፡ መኪናን ፡ ማፈራረስ » የሚሉት ፡ ቃላት ፡ በአጭሩ ፡ የሚገልጹት ፡ መንግሥትን ፡ በሚመለከት ፡ ረገድ ፡ በአብዮት ፡ ጊዜ ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ ተግባር ፡ ምን ፡ እንደሆነ ፡ የሚያሳይ ፡ ዋና ፡ የማርክሲዝም ፡ ትምህርት ፡ ነው ። ይህ ፡ ትምህርት ፡ ፍፁም ፡ የተረሳ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፤ እንድያውም ፡ ባንሰራራው ፡ ካውትስካዊነት ፡ ማርክሲዝምን « በመተርጎም » ቀጥታ ፡ ተጣሟል!

« በ ፲፰ኛው ፡ ብሩሜር » የማርክስን ፡ ጥቅስ ፡ በሚመለከተው ፤ ከዚህ ፡ በላይ ፡ የሚያስፈልገውን ፡ በሞላ ፡ አቅርበናል ።





ከዚህ ፡ በላይ ፡ ባ[illegible] ፡ የ[illegible] ፡ ገለጻ ፤ በተለይ ፡ ሁለት ፡ ነጥቦችን ፡ [illegible] ፡ አ[illegible] ፡ [illegible] ፤ አንደኛ — መደምደምያውን ፡ የሚወስነው ፡ በክፍለ ፡ አገር (በአውሮፓ — ተ) ነው ። ይህ ፡ በ ፲፰፻፸፩ ዓ. ም. ግልጽ ፡ ነበር ፤ ምክንያቱም ፡ እንግሊዝ ፡ ገና ፡ ንፁህ ፡ የካፒታሊስት ፤ አገር ፡ ጥሩ ፡ ምሳሌ ፡ ነበረች ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ያለ ፡ ወታደራዊ ፡ ድርጅትና ፡ እስከተወሰነ ፡ ደረጃም ፡ ያለ ፡ ቢሮክራሲ ፡ ነው ። ስለዚህም ፡ ነው ፡ ማርክስ ፤ አብዮት ፤ እንዲያውም ፡ ሕዝባዊ ፡ አብዮት ፡ ያለ ፡ ተቀዳሚ ፡ ተግባር ፡ ማለትም « ያለው ፡ ዝግጁ ፡ የመንግሥት ፡ መኪና » ሳይፈርስ ፡ ይቻል ፡ መስሎ ፡ የታየባትንና ፤ ይቻልም ፡ የነበረባትን ፡ እንግሊዝን ፡ ለይቶ ፡ የተዋት ።

አሁን ፡ በ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. ፤ በአንደኛው ፡ ትልቁ ፡ የኢምፔሪያሊስት ፡ ጦርነት ፡ ዘመን ፤ ይህ ፡ ማርክስ ፡ የጠቀሰው ፡ ነጥብ ፡ ትክክለኛ ፡ አይደለም ። በመላ ፡ ዓለም ፤ ትላልቅና ፡ የመጨረሻ ፡ የአንግሎ-ሳክሶን « ነፃነት » ወኪሎች ፡ የሆኑት ፤ ወታደራዊ ፡ ድርጅትና ፡ ቢሮክራሲም ፡ ያልነበራቸው ፡ ሁለቱም ፡ እንግሊዝና ፡ አሜሪካ ፤ አሁን ፡ ሁሉንም ፡ በቁጥጥራቸው ፡ ሥር ፡ ባደረጉ ፤ ሁሉንም ፡ በሚጨቁኑ ፤ የመላ ፡ አውሮጳ ፡ የቆሻሻና ፡ የደም ፡ ረግረግ ፡ በሆኑት ፡ በቢሮክራሲያዊ-ወታደራዊ ፡ ድርጅቶች ፡ ፍጹም ፡ ተውጠዋል ። አሁን ፡ በእንግሊዝም ፡ ሆነ ፡ በአሜሪካ « የእውነተኛ ፡ ሕዝባዊ ፡ አብዮት ፡ ተቀዳሚ ፡ ተግባር ፡ የሆነ » (በ ፲፱፻፲፬-፲፯ ዓመታት ፡ ተቋቁሞ ፡ እስከ « የአውሮጳ » ፤ የመላ ፡ ኢምፔሪያሊስት ፡ አገሮች ፡ ፍጹምነት ፡ የተሻሻለውን) « ያለውን ፡ የመንግሥት ፡ መኪናን » ማፍረስ ፤ መደምሰስ ፡ ነው ።

ሁለተኛ ፤ የቢሮክራሲያዊ-ወታደራዊውን ፡ የመንግሥት ፡ መኪናን ፡ መደምሰስ « የያንዳንዱ ፡ እውነተኛ ፡ ሕዝባዊ ፡ አብዮት ፡ ተቀዳሚ ፡ ተግባር ፡ ነው » የሚለው ፡ የማርክስ ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ጥልቅ ፡ የሆነ ፡ አስተያየት ፡

ልዩ ፡ ጥንቃቄን ፡ ይጠይቃል ። « ሕዝባዊ » አብዮት ፡ የሚለው ፡ ሀሳብ ፡ ከማርክስ ፡ የፈለቀ ፡ እንግዳ ፡ ነገር ፡ ይመስላል ፤ የሩሲያ ፡ የፕሌኻኖቭ ፡ ተከታዮችና ፡ ሜንሼቪኮች[5] ፤ እነዚህ ፡ ማርክሲስቶች ፡ እንዲባሉ ፡ የሚሹ ፡ የስትሩቬ ፡ ተከታዮች ፤ ይህ ፡ አስተያየት ፡ ማርክስ « ምላሱ ፡ አድጦት » የተናገረው ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ምናልባት ፡ ለማረጋገጥ ፡ በቻሉ ፡ ይሆናል ። ማርክሲዝምን ፡ እስከ ፡ ወራዳ ፡ የሊብራልነት ፡ ማጣመም ፡ ድረስ ፡ ዝቅ ፡ በማድረጋቸው ፡ ለነሱ ፡ ከቡርዥዋው ፡ አብዮትና ፡ ከወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት ፡ ተፃራሪነት ፡ ወድያ ፡ ሌላ ፡ ምንም ፡ ነገር ፡ የለም ፤ ይህ ፡ ተፃራሪነትም ፡ ቢሆን ፡ እነሱ ፡ የሚገነዘቡት ፡ ፍፁም ፡ ሙት ፡ በሆነ ፡ መንገድ ፡ ነው ።

የ ፳ኛውን ፡ ምእት ፡ ዓመት ፡ አብዮቶችን ፡ እንደምሳሌ ፡ አድርገን ፡ ብንወስድ ፤ የፖርቱጋልም ፡ ሆነ ፡ የቱርክ ፡ አብዮቶች ፤ ሁለቱም ፡ እርግጥ ፡ የቡርዥዋ ፡ አብዮቶች ፡ እንደሆኑ ፡ መቀበል ፡ አለብን ። ቢሆንም ፡ አንዳቸውም « ሕዝባዊ » አብዮት ፡ አይደሉም ፤ ምክንያቱም ፡ ሰፊው ፡ ሕዝብ ፤ አብዛኛው ፡ ምልአተ ፡ ሕዝብ ፡ ነቅቶ ፡ ራሱን ፡ ችሎ ፡ ነፃ ፡ በሆነ ፡ መንገድ ፡ የራሱ ፡ የሆኑትን ፡ የኤኮኖሚና ፡ የፖለቲካ ፡ ጥያቄዎች ፡ ይዞ ፡ በበቂ ፡ አልተሳተፈም ። በአንፃሩ ፤ የ ፲፱፻፭-፯ ዓመታት ፡ የሩሲያ ፡ የቡርዥዋ ፡ አብዮት ፤ ምንም ፡ እንኳ ፡ አንዳንዴ ፡ የፖርቱጋልና ፡ የቱርክ ፡ አብዮቶች ፡ እንዳጋጠማቸው « ግሩም ፡ የሆኑ » ድሎችን ፡ ባይጎናፀፍም ፤ ያለጥርጥር « እውነተኛ ፡ ሕዝባዊ » አብዮት ፡ ነበር ፤ ምክንያቱም ፡ ሰፊው ፡ ሕዝብ ፤ አብዛኛው ፡ ምልአተ ፡ ሕዝብ ፤ በጭቆናና ፡ በብዝበዛ ፡ የተደቆሱት ፤ በጣም ፡ ዝቅተኛ ፡ የሆኑ ፡ የኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ክፍሎች ፡ ራሳቸውን ፡ ችለው ፡ ነፃ ፡ በሆነ ፡ መንገድ ፡ ተነስተዋል ፤ በአብዮቱ ፡ መላ ፡ ሂደትም ፡ ጥያቄዎቻቸውና ፡ በሚፈርሰው ፡ አሮጌ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ፋንታ ፡ በፈለጉት ፡ መንገድ ፡ አዲሱን ፡ ኅብ





ረተ ፡ ሰብ ፡ ለመ[illegible]ራትው ፡ ጉልህ ፡ ሁኖ ይታያል ።

በአውሮፓ ፡ በ ፲፰፻፸፩ ዓ. ም. በየትም ፡ አገር ፡ ውስጥ ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ ብዛት ፡ ከሕዝቡ ፡ አብዛኛው ፡ አልነበረም ። በእውነት ፡ አብዛኛውን ፡ ሕዝብ ፡ ወደ ፡ እንቅስቃሴው ፡ ሊስብ ፡ የሚችል ፤ « ሕዝባዊ » አብዮት ፡ ነው ፡ ሊባል ፡ የሚቻለው ፡ ወዝ ፡ አደሩንና ፡ አርሶ ፡ አደሩንም ፡ ካቀፈ ፡ ብቻ ፡ ነው ። እነዚህ ፡ ሁለቱም ፡ መደቦች ፡ ናቸው « ሕዝብን » የሚመሰርቱት ። እነዚህ ፡ ሁለቱ ፡ መደቦች ፡ የሚተባበሩበት ፡ ምክንያት « ወታደራዊ-ቢሮክራሲያዊ ፡ የመንግሥት ፡ መኪናው » ሁለቱንም ፡ ይጨቁናቸዋል ፤ ይደቁሳቸዋል ፤ ይበዘብዛቸዋል ። ይህን ፡ የመንግሥት ፡ መኪናን ፡ መስበር ፤ መደምሰስ — ትክክለኛው « የሕዝቡ » ፍላጎት ፡ ነው ፤ ማለት ፡ የአብዛኛው ፡ ወዝ ፡ አደርና ፡ የአብዛኛው ፡ አርሶ ፡ አደር ፡ ነው ፤ ይህ ፡ ሁሉ ፡ የድሀ ፡ አርሶ ፡ አደሮችና ፡ የወዝ ፡ አደሮች ፡ ነፃ ፡ ኅብረት « ተቀዳሚ ፡ ተግባር » ሲሆን ፤ ያለዚህ ፡ ኅብረት ፡ ዴሞክራሲ ፡ ጠንካራ ፡ አይደለም ፤ የሶሺያሊስት ፡ ለውጥም ፡ ሊደረግ ፡ አይቻልም ።

እንደሚታወቀው ፡ ሁሉ ፤ የፓሪስ ፡ ኮሙን ፡ ይህን ፡ ኅብረት ፡ ለመመስረት ፡ ጐዳናውን ፡ ተልሞ ፡ ነበር ፤ ቢሆንም ፡ በአንዳንድ ፡ የውስጥና ፡ የውጭ ፡ ሁኔታዎች ፡ ምክንያት ፡ ግቡን ፡ ሳይመታ ፡ ቀረ ።

ስለሆነም ፤ ማርክስ ፡ ስለ « እውነተኛ ፡ ሕዝባዊ ፡ አብዮት » የተናገረው ፤ ስለንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ልዩ ፡ ባህርይ ፡ ቅንጣትም ፡ ታህል ፡ ሳይረሳ (ስለነሱ ፡ ብዙ ፡ ጊዜና ፡ ሁልጊዜ ፡ ተናግሯል) ፤ በ ፲፰፻፸፩ ዓ. ም. በአብዛኞቹ ፡ የአውሮፓ ፡ መንግሥታት ፡ የነበረውን ፡ ተጨባጭ ፡ የመደቦች ፡ ሚዛን ፡ በጥንቃቄ ፡ በማጤን ፡ ነው ። በሌላ ፡ በኩል ፡ ደግሞ ፤ ማርክስ ፡ እንደጠቀሰው ፤ የመንግሥት ፡ መኪናን « ለመሰባበር » የሚፈልጉት ፡ ወዝ ፡ አደሩና ፡ አርሶ ፡ አደሩ ፡ ለጥቅማቸው ፡ ብለው ፡ ነው ፤ ይህም ፡ ዓላማ ፡ ያስተባብራቸ

ዋል ፤ ይኸውም « ተባይን » የማስወገድና ፡ በሌላ ፡ በአዲስ ፡ ነገር ፡ የመተካት ፡ የጋራ ፡ ተግባር ፡ ከፊታቸውም ፡ ይደ ቅናል ።

ሆኖም ፡ በምን ፡ መተካት ፡ አለበት?

## ፪. የተሰባበረው ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ በምን ፡ መተካት ፡ አለበት?

ለዚህ ፡ ጥያቄ ፡ በ ፲፰፻፵፰ ዓ. ም. « በኮሙኒስት ፡ ማኒ ፌስቶ » ውስጥ ፡ ማርክስ ፡ የሰጠው ፡ መልስ ፡ ፍጹም ፡ ግል ፅ ፡ ያልሆነ ፡ ነበር ፤ በትክክል ፡ ለመናገር ፤ መልሱ ፡ ተግባ ሮችን ፡ ይጠቁማል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የሚፈታበትን ፡ መን ገድ ፡ አያሳይም ። የተሰባበረው ፡ የመንግሥት ፡ መኪና « ወዝ ፡ አደሩ ፡ እንደ ፡ ገዥ ፡ መደብ ፡ ሆኖ ፡ በተደራጀበት ፡ ድርጅት » ፤ « ዴሞክራሲን ፡ በተጎናፀፈበት » መተካት ፡ አለበት — ይህ ፡ ነበር « በኮሙኒስት ፡ ማኒፌስቶ » የ ተሰጠው ፡ መልስ ።

ማርክስ ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ እንደገዥ ፡ መደብ ፡ የሚሆ ንበት ፡ ድርጅት ፡ ምን ፡ ዓይነት ፡ የተጨበጡ ፡ ቅርፆች ፡ ሊ ኖሩት ፡ ይገባል ፤ በተለይም ፡ ይህ ፡ ድርጅት ፡ እንዴት ፡ ብሎ ፡ ነው ፡ በጣም ፡ ፍፁምና ፡ ደምበኛ ፡ ከሆነው « የዴ ሞክራሲ ፡ መጎናፀፍ » ጋር ፡ የሚዋሀደው ፤ ለሚሉት ፡ ጥያቄዎች ፡ መልስ ፡ የጠበቀው ፡ ከሰፊ ፡ እንቅስቃሴ ፡ ልምድ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ ከተምኔታዊነት ፡ አልነበረም ።

የኮሙን ፡ ልምድ ፤ ትንሽም ፡ ቢሆንም ፡ « የርስ ፡ በርስ ፡ ጦርነት ፡ በፈረንሳይ » በተባለው ፡ መጽሐፉ ፤ ማርክስ ፡ በከፍተኛ ፡ ጥንቃቄ ፡ ትንተና ፡ አድርጎበታል ። ከዚሁ ፡ መፅሐፍ ፡ ውስጥ ፡ በጣም ፡ አስፈላጊ ፡ የሆኑትን ፡ ክፍ ሎች ፡ እንጠቅሳለን ፤

በመካከለኛው ፡ ክፍለ ፡ ዘመን ፡ መንጭቶ ፡ በ ፲፱



ምእት ፡ ዓመት « [illegible] ፡ ሥል ጣን ፤ ከዘወተር ፡ አካሎቹ — ከቋሚ ፡ ጦሩ ፤ ከፖሊሱ ፤ ከቢሮክራሲው ፤ ከካህናቱ ፤ ከፍርድ ፡ ቤቱ ፡ ጋር » አንድ ፡ ላይ ፡ አድጓል ። በካፒታልና ፡ በጉልበት ፡ መካከል ፡ መደባዊ ፡ ተፃራሪነት ፡ ባደገ ፡ መጠን «የመ ንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ ወዝ ፡ አደሩን ፡ መደብ ፡ ለመጨ ቆን ፡ ከጊዜ ፡ ወደ ፡ ጊዜ ፡ ይበልጥ ፡ የማኅበራዊ ፡ ኃይ ል ፡ ባህርይ ፤ የገዥ ፡ መደብ ፡ መኪና ፡ ባህርይ ፡ ይዟ ል ። በመደብ ፡ ትግል ፡ ውስጥ ፡ አንድ ፡ እርምጃ ፡ ወደ ፊት ፡ ከሆነው ፡ ከማንኛውም ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፤ የመ ንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ ፍጹም ፡ የጨቋኝነት ፡ ባህርይ ፡ ከጊዜ ፡ ወደ ፡ ጊዜ ፡ በይበልጥ ፡ ጉልህ ፡ እየሆነ ፡ ሔደ ።» ከ ፲፰፻፵፰-፵፱ ዓመታት ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ የመንግ ሥት ፡ ሥልጣን « ካፒታል ፡ ጉልበትን ፡ ሲወጋ ፡ ብሄራዊ ፡ መሳሪያው » ይሆናል ። ሁለተኛው ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ አገዛዝ ፡ ይህን ፡ ያረጋግጣል ።

« የንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ አገዛዝ ፡ ቀጥተኛ ፡ ተፃራሪ ፡ ኮሙኑ ፡ ነበር ። » « ኮሙን ፡ የሪፑብሊኩ ፡ ልዩ ፡ ቅር ፅ ፡ ሁኖ ፤ ይህ ፡ ሪፑብሊክ ፡ ማስወገድ ፡ የነበረበት ፡ የመደብ ፡ ገዥነት ፡ የዘውዳዊውን ፡ አገዛዝ ፡ ቅርፅ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፤ በጠቅላላው ፡ የመደብ ፡ ገዥነትን ፡ ነበር ... »

የዚህ ፡ ወዝ ፡ አደራዊ ፤ ሶሺያሊስት ፡ ሪፑብሊክ « ልዩ » ቅርፅ ፡ ምን ፡ ነበር? ለመመስረት ፡ የተጀመረው ፡ መንግሥት ፡ ምን ፡ ዓይነት ፡ ነበር?

«... የኮሙን ፡ የመጀመሪያ ፡ አዋጅ ፡ ቋሚ ፡ ጦሩን ፡ መደምሰስና ፡ በሱም ፡ ፋንታ ፡ የታጠቀ ፡ ሕዝብ ፡መተ ካት ፡ ነበር ... »

ይህ ፡ ጥያቄ ፡ በአሁኑ ፡ ጊዜ ፡ በእያንዳንዱ ፡ ራሱን ፡ ሶሺያሊስት ፡ ነኝ ፡ ብሎ ፡ በሚጠራ ፡ ፓርቲ ፡ ፕሮግራም ፡ ውስጥ ፡ ይገኛል ። ግን ፡ ፕሮግራማቸው ፡ ምን ፡ ዋጋ ፡ እንደ አለው ፡ በኛዎቹ ፡ ሶሺያሊስት-አብዮታውያንና[4] ፡ በሜንሼቪኮች[5] ፡ ድርጊት ፡ በጉልህ ፡ ይታያል ፤ በተለይም ፡ ከየካቲት ፡ ፲፱፻፲፯ አብዮት ፡ በኋላ ፡ ይህንን ፡ ጥያቄ ፡ በተግባር ፡ ከማሳየት ፡ አሻፈረን ፡ ሲሉ!

« … ኮሙን ፡ የተቋቋመው ፡ በአጠቃላይ ፡ ምርጫ ፡ ከልዩ ፡ ልዩ ፡ የፓሪስ ፡ ቀበሌዎች ፡ ከተመረጡ ፤ የከተማ ፡ መማክርት ፡ ነበር ። እነዚህም ፡ ተጠያቂ ፡ ኃላፊነት ፡ ነበራቸው ፤ በማንኛውም ፡ ጊዜም ፡ ሊሻሩ ፤ ሊለወጡ ፡ ይችላሉ ። እርግጥ ፡ ነው ፤ ከእነሱም ፡ አብዛኛዎቹ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፤ ወይንም ፡ የታወቁ ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ ተጠሪዎች ፡ ነበሩ …
… እስከዚያ ፡ ጊዜ ፡ ድረስ ፡ የድሮው ፡ መንግሥት ፡ መሳሪያ ፡ የነበረው ፡ የፖሊስ ፡ ሠራዊት ፡ ወድያውኑ ፡ የፖለቲካ ፡ ተግባሮቹ ፡ በሙሉ ፡ ተሰርዘዋል ፤ አባሎቹ ፡ በተፈለገ ፡ ጊዜ ፡ ሊለወጡ ፡ ሊሻሩ ፡ ወደሚችሉበት ፤ ተጠሪነቱ ፡ ለኮሙን ፡ ወደሆነው ፡ ድርጅት ፡ ተለውጧል … ሌሎች ፡ የአስተዳደር ፡ ቅርንጫፎች ፡ በለሥልጣኖችም ፡ እንደዚሁ … ከኮሙን ፡ አባሎች ፡ ጀምሮ ፤ ከላይ ፡ እስከ ፡ ታች ፤ ማኅበራዊ ፡ አገልግሎት ፡ የሚሰራው ፡ በወዝ ፡ አደሩ ፡ ደመወዝ ፡ ልክ ፡ ነበር ። ለከፍተኛ ፡ የመንግሥት ፡ ማዕርጎች ፡ ለውክልና ፡ ይሰጡ ፡ የነበሩት ፡ ማንኛውም ፡ ልዩ ፡ መብቶችና ፡ ልዩ ፡ ወጪዎች ፡ ከማዕርጎቹ ፡ መወገድ ፡ ጋር ፡ አብረው ፡ ጠፉ … ኮሙኑ ፡ የአሮጌውን ፡ አገዛዝ ፡ የቆሳቁሳዊ ፡ ኃይል ፡ መሳሪያዎች ፡ የነበሩትን ፡ ቋሚ ፡ ጦርንና ፡ ፖሊሱን ፡ ካስወገደ ፡ በኋላ ፤ ወድያውኑ ፡ የመንፈስ ፡ ጭቆና ፡ መሳሪያ ፡ የነበረውን ፡ የጳጳሳትን ፡ ኃይል ፡



መስበር ፡ ቀጥሏል … የፍርድ ፡ ቤት ፡ ባለሥልጣኖች ም ፡ ያ ፡ [illegible] ፡ አጥተዋል … በግልፅ ፡ መመረጥ ፡ ነበረባቸው ፤ በኃላፊነት ፡ የሚጠየቁና ፡ የሚሻሩም ፡ የሚለወጡም ፡ መሆን ፡ ነበረባቸው … »[17]

እንግዲህ ፤ ኮሙን ፡ የተሰበረውን ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ ይበልጥ ፡ በሙሉ ፡ ዴሞክራሲ « ብቻ » የለወጠው ፡ ይመስላል ፤ ማለትም ፡ ቋሚ ፡ ጦሩን ፡ መደምሰስ ፤ መላ ፡ ባለሥልጣኖችን ፡ መምረጥና ፡ ሲያስፈልግም ፡ መሻርና ፡ መለወጥ ፡ ነው ። በሥራ ፡ ላይ ፡ ሲታይ ፡ ግን ፡የለውጡ ፡ ከፍተኛ ፡ ፍች ፤ አንድ ፡ ዓይነት ፡ ድርጅቶችን ፡ በመሰረቱ ፡ ልዩ ፡ በሆኑ ፡ በሌላ ፡ ድርጅቶች ፡ መተካት ፡ ብቻ ፡ ማለት ፡ ነው ። ይህ ፡ ነው ፡ በትክክል « የመጠን (quantity) ወደ ፡ ጥራት (quality) መለወጥ ፤» ዴሞክራሲ ፡ ሳይጓደልና ፡ ሳይቋረጥ ፤ በአጠቃላይም ፡ እንደሚታሰበው ፡ ከተደረገ ፤ ከቡርዥዋ ፡ ዴሞክራሲ ፡ ወደ ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ ዴሞክራሲ ፡ ይለወጣል ፤ መንግሥት (=ያንድን ፡መደብ ፡ መጨቆኛ ፡ ልዩ ፡ ኃይል) ከእንግዲህ ፡ እንድያው ፡ እንደመንግሥት ፡ አይሆንም ።

ቡርዥዋውንና ፡ የሱን ፡ ተቃውሞ ፡ ለማጥፋት ፡ አሁንም ፡ ገና ፡ ያስፈልጋል ። ይህ ፡ ለኮሙን ፡ በተለይ ፡ በጣም ፡ አስፈላጊ ፡ ነበር ፤ የመውደቂያውም ፡ አንዱ ፡ ምክንያት ፡ ይህንን ፡ ተግባር ፡ በከፍተኛ ፡ ቆራጥነት ፡ ስላልፈፀመ ፡ ነው ። የመጨቆኛው ፡ ድርጅት ፡ በባርነት ፤ በጭሰኝነት ፤ በቅጥር ፡ ባርነት ፡ ዘመናት ፡ ሁሉ ፡ እንደነበረው ፡ የጥቂቶች ፡ ሳይሆን ፡ እዚህ ፡ ላይ ፡ የአብዛኛው ፡ ምልአተ ፡ ሕዝብ ፡ ነው ። ስለዚህም ፡ አብዛኛው ፡ ሕዝብ ፡ ራሱ ፡ የሚጨቁኑትን ፡ ከደመሰሰ ፤ ለመጨቆኛ ፡ የሚሆን « ልዩ ፡ ኃይል » ጨርሶ ፡ አያስፈልግም! በዚህ ፡ ዓይነት ፡ መንግሥት ፡ መክሰም ፡ ይጀምራል ። ልዩ ፡ መብት ፡ ካላቸው ፡ የጥቂቶች ፡ ልዩ ፡

ድርጅቶች (ልዩ ፡ መብት ፡ ካላቸው ፡ ባለስልጣኖች ፤ የቋሚ ፡ ጦር ፡ ሹማምንት) ፈንታ ፡ አብዛኛው ፡ ሰፊ ፡ ሕዝብ ፡ ራሱ ፡ እነዚህን ፡ ተግባሮች ፡ ቀጥታ ፡ ሊያሟላ ፡ ይችላል ። ስለሆነም ፡ የመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ ተግባሮች ፡ ይበልጥ ፡ ሕዝባዊ ፡ በሆኑ ፡ መጠን ፡ የዚሁ ፡ ሥልጣን ፡ መኖር ፡ አስፈላጊነት ፡ ይበልጥ ፡ እየቀነሰ ፡ ይሄዳል ።

እዚህ ፡ ላይ ፡ ማርክስ ፡ ትልቅ ፡ ዋጋ ፡ የሰጣቸው ፡ የሚከተሉትን ፡ የኮሙን ፡ እርምጃዎች ፡ በተለይ ፡ ግሩም ፡ ናቸው ፤ ለወኪሎች ፡ ይሰጥ ፡ የነበረው ፡ ማንኛውም ፡ ልዩ ፡ ወጭ ፡ ማስቀረት ፤ ለባለሥልጣኖች ፡ ይደረግ ፡ የነበረው ፡ ማንኛውም ፡ የገንዘብ ፡ ልዩ ፡ መብት ፡ ማስወገድ ፤ በመንግሥቱ ፡ ውስጥ ፡ የሚያገለግሉ ፡ የሁሉም ፡ ሰዎች ፡ ክፍያ « ከወዝ ፡ አደሩ ፡ ደመወዝ » እኩል ፡ ማስተካከል ። ይህ ፡ በግልፅ ፡ የሚያሳየው ፡ ከቡርዥዋ ፡ ዴሞክራሲ ፡ ወደ ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ ዴሞክራሲ ፡ መሸጋገሩን ፤ ከጨቋኞች ፡ ዴሞክራሲ ፡ ወደ ፡ ተጨቋኞች ፡ ዴሞክራሲ ፡ መለወጡን ፤ መንግሥት ፡ እንደ « ልዩ ፡ ኃይል » ያንድን ፡ መደብ ፡ መጨቆኑ ፡ ቀርቶ ፡ በአብዛኛው ፡ ሰፊ ፡ ሕዝብ ፤ በወዝ ፡ አደሩና ፡ በአርሶ ፡ አደሩ ፡ ጠቅላላ ፡ ኃይል ፡ ጨቋኞችን ፡ መደምሰሱን ፡ ነው ። በተለይ ፡ በዚህ ፡ ነጥብ ፡ ላይ ፡ ነው ፤ ምናልባትም ፡ የመንግሥትን ፡ ጥያቄ ፡ በሚመለከት ፡ በኩል ፤ በጣም ፡ አስፈላጊ ፡ የሆነው ፡ የማርክስ ፡ ትምህርት ፡ ዋና ፡ ነጥብ ፡ ይበልጥ ፡ የተረሳው! ስፍር ፡ ቁጥር ፡ በሌላቸው ፡ የታወቁ ፡ ትችቶች ፡ ውስጥ ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ምንም ፡ አይናገሩም ። ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ላለመናገር « ተወስኗል » ፤ልክ ፡ ጊዜው ፡ እንዳለፈበት « የዋህነት » ፤ ይህ ፡ ልክ ፡ ክርስትያኖች ፡ የክርስትና ፡ ሃይማኖት ፡ የመንግሥታዊ ፡ ሃይማኖት ፡ ቦታ ፡ ሲያገኝ ፤ የጥንቱ ፡ ክርስትና ፡ ሃይማኖት « የዋህነት » ከነዴሞክራሲያዊ ፤ አብዮታዊ ፡ መንፈሱ ፡ ጋር « እንደረሱት » ሁሉ ፡ ነው ።

የከፍተኛ ፡ የመንግሥት ፡ ባለሥልጣኖች ፡ ክፍያ ፡



መቀነስ ፡ እንድያው « ለአመሉ » የዋህ ፤ ጥንታዊ ፡ ዴሞክራቲዝም ፡ ይመስላል ። ካዲሱ ፡ አድርባይነት « መስራቾች » አንዱ ፤ ድሮ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራት ፡ የነበረው ፡ ኤድዋርድ ፡ ቤርንስተይን «በጥንታዊ» ዴሞክራሲ ፡ ላይ ፡ ካንዴም ፡ ሁለቴ ፡ ደጋግሞ ፡ ስድ ፡ የቡርዥዋ ፡ ፌዞችን ፡ ጕንጕኗል ። እንደ ፡ ሁሉም ፡ አድርባዮችና ፤ እንደ ፡ አሁኖቹ ፡ ካውትስካውያን ፤ እሱም ፡ በፍጹም ፡ ያልገባው ፤ አንደኛ — ከካፒታሊዝም ፡ ወደ ፡ ሶሺያሊዝም ፡ ለመሸጋገር ፡ ወደ« ጥንታዊ » ዴሞክራሲ ፤ ጥቂት « ወደ ፡ ኋላ ፡ ሳይመለሱ » የማይቻል ፡ መሆኑን ፡ ነው (ካልሆነማ ፤ አለበለዚያ ፡ አብዛኛው ፡ ምልአተ ፡ ሕዝብ ፤ ብሎም ፡ አንድም ፡ ሳይቀር ፡ መላ ፡ ምልአተ ፡ ሕዝቡ ፡ መንግሥታዊ ፡ ተግባሮቹን ፡ ለማካሄድ ፡ እንዴት ፡ ይችላል?) ፤ ሁለተኛ — ካፒታሊዝምንና ፡ የካፒታሊስት ፡ ባህልን ፡ መሠረት ፡ ያደረገ « ጥንታዊ ፡ ዴሞክራሲ » ከጋርዮሽ ፡ ወይንም ፡ ከቅድመ ፡ ካፒታሊስት ፡ ዘመናት ፡ ካለው ፡ ጥንታዊ ፡ ዴሞክራሲ ፡ ጋር ፡ አንደ ፡ ዓይነት ፡ አይደለም ። የካፒታሊስት ፡ ባህል ፡ ከፍተኛ ፡ ሰፊ ፡ ምርትን ፤ ፋብሪካዎችን ፤ የሃዲድ ፡ መንገዶችን ፤ የፖስታ ፡ አገልግሎትን ፤ ስልክንና ፡ የመሳሰሉትን ፡ ፈጥሯል ፤ ይህንንም ፡ በመመርኮዝ ፡ የአሮጌው «የመንግሥት ፡ ስልጣን» አብዛኞቹ ፡ ተግባሮች ፡ በጣም ፡ ስለሚቃለሉ ፡ የሚቀሩት ፡ እጅግ ፡ ቀላል ፡ የሆኑ ፡ የምዝገባ ፤ ፋይል ፡ መያዝንና ፡ የመቆጣጠር ፡ ተግባሮች ፡ ይሆናሉ ፤ እነዚህ ፡ ተግባሮች ፡ ማንም ፡ ማንበብና ፡ መጻፍ ፡ የሚችል ፡ ሰው ፡ ሊያከናውናቸው ፡ ይችላል ፤ እነዚህ ፡ ተግባሮች ፡ በተለመደው « በወዝ ፡ አደሩ ፡ ደመወዝ » ሊፈፀሙ ፡ ይችላሉ ፤ ስለዚህም ፡ እነዚህ ፡ ተግባሮች ፡ የማንኛውም « የበላይ ፡ ባለስልጣንነት » ማንኛውም ፡ የልዩ ፡ መብት ፡ ምክንያቶች ፡ ሊያስወግዱ ፡ ይችላሉ ፤ (ይገደዳሉም) ።

መላ ፡ ሹማምንቶችን ፤ አንድም ፡ ሳይቀር ፡ በማንኛውም ፡ ጊዜ ፡ መምረጥ ፤ መሻር ፡ መለወጥ ፤ ደመወዛቸውም ፡





በተራው «ወዝ ፡ አደር ፡ ደመወዝ » ልክ ፡ ማስተካከል ፤ እነዚህ ፡ ቀላልና «ግልፅ » የሆኑ ፡ ዴሞክራቲክ ፡ እርም ጃዎች ፡ የወዝ ፡ አደሮችንና ፡ የአብዛኛው ፡ አርሶ ፡ አደሮ ችን ፡ ፍላጎት ፡ ፍፁም ፡ በማስተባበር ፤ ከካፒታሊዝም ፡ ወደሶሺያሊዝም ፡ እንደሚያሸጋግር ፡ ድልድይ ፡ ሆነው ፡ ያገለግላሉ ። እነዚህ ፡ እርምጃዎች ፡ መንግሥቱን ፡ እንደ ገና ፡ ማደራጀትን ፡ ይመለከታሉ ፤ የኅብረተ ፡ ሰቡን ፡ ንፁህ ፡ ፖለቲካዊ ፡ መደራጀት ፡ ይጠይቃሉ ። ነገር ፡ ግን ፤ እርግጥ ፡ ነው ፤ እነዚህ ፡ ሙሉ ፡ ትርጉማቸውና ፡ ፍቻቸው ፡ የሚ ያገኙት ፡ « የበዝባዦች ፡ መበዝበዝ » ሲከናወን ፡ ወይም ፡ ሲዘጋጅ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ ማለትም ፡ የምርት ፡ መገልገያዎች ፡ ከካፒታሊስት ፡ የግል ፡ ንብረትነት ፡ ወደ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ አዊ ፡ ንብረትነት ፡ ሲለወጥ ፡ ነው ።

ማርክስ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ጽፎአል ፤ « ኮሙኑ ፡ የሁ ሉም ፡ የቡርዥዋ ፡ አብዮቶች ፡ የነበረውን ፡ መፈክር ፤ ማለት ፡ ርካሽ ፡ የአስተዳደር ፡ ድርጅት ፡ በሥራ ፡ ላይ ፡ አረጋግጧል ፤ ይኸውም ፡ ሁለቱ ፡ ትላልቅ ፡ የወጭ ፡ ምንጮች ፡ የሆኑትን ፤ ወታደሩንና ፡ ቢሮክራሲውን ፡ በመደምሰስ ፡ ነው ። »

ከገበሬውም ፤ እንደሌሎቹ ፡ የንኡስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ክፍ ሎች ፤ በጣም ፡ ጥቂቶቹ ፡ ብቻ « ወደ ፡ ላይ ፡ ይወጣሉ » ፤ በቡርዥዋዊ ፡ አስተሳሰብ « ሰዎች ፡ ይሆናሉ » ፤ ማለትም ፡ ወይ ፡ ይከብራሉ ፤ ቡርዥዋ ፡ ይሆናሉ ፤ ወይ ፡ የደላቸውና ፡ ልዩ ፡ መብት ፡ ያላቸው ፡ ባለሥልጣኖች ፡ ይሆናሉ ። ገበሬ ዎች ፡ ባሉበት ፡ ማናቸውም ፡ ካፒታሊስት ፡ አገር (አብዛ ኞቹ ፡ ካፒታሊስት ፡ አገሮች ፡ እንዲህ ፡ ያሉ ፡ ናቸው) ፤ አብዛኛው ፡ ሰፊ ፡ አርሶ ፡ አደር ፡ በአገዛዙ ፡ የተጨቆነ ፡ ነው ፤ ስለዚህም ፡ አገዛዙን ፡ ለመጣል ፡ በናፍቆት ፡ ይጠባበ ቃል ፤ « ርካሽ » አገዛዝን ፡ በናፍቆት ፡ ይጠባበቃል ። ይ



ኸንንም ፡ ከግቡ ፡ ለማድረስ ፡ የሚችለው ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ ይኸንን ፡ ሲፈጽም ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ አብሮም ፡ መንግሥቱን ፡ በሶሺያሊስታዊ ፡ መልክ ፡ በማደራጀት ፡ ረገ ድ ፡ አንድ ፡ እርምጃ ፡ ያደርጋል ።

## ፫. የፓርላሜንታሪዝም ፡ መደምሰስ ።

« ኮሙን ፤ ይላል ፡ ማርክስ ፤ መሆን ፡ የነበረበት ፤ ፓርላሜንታዊ ፡ ሳይሆን ፤ የሚሠራ ፡ ድርጅት ፡ ነው ፤ አንድ ፡ ላይ ፡ ህግ ፡ አውጪም ፤ አስፈጻሚም ፡ መሆን ፡ ነበረበት ...

... በሶስት ፡ ወይም ፡ በስድስት ፡ ዓመት ፡ ውስጥ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ የትኛው ፡ የገዥ ፡ መደብ ፡ አባል ፡ በ ፓርላማ ፡ ውስጥ ፡ ሕዝቡን ፡ እንዲወክልና ፡ እንዲ ጨቁን (ver und zertreten) በመወሰን ፡ ፈንታ ፤ አጠቃላይ ፡ ምርጫ ፡ በኮሙን ፡ የተደራጀውን ፡ ሕዝብ ፡ ማገልገል ፡ ነበረበት ፤ ይኸውም ፤ የግለሰብ ፡ ምርጫ ፡ መብት ፡ ማንኛው ፡ ሌላ ፡ ቀጣሪ ፡ ሠራተኞችን ፤ ሠራተኛ ፡ ተ ቆጣጣሪዎችንና ፡ የሂሳብ ፡ ሹሞችን ፡ ለሥራው ፡ ለመመ ልመል ፡ እንደሚጠቀምበት ፡ ሁሉ ፡ ነው ።»

ይህ ፡ በ ፲፰፻፸፩ ዓ. ም. በፓርላሜንታሪዝም ፡ ላይ ፡ የተደረገው ፡ ግሩም ፡ ሒስ ፤ ባንሠራራው ፡ ሶሺያል-ሾቪ ኒዝምና ፡ አድርባይነት ፡ ምክንያት ፡ አሁን « ከተረሱት » የማርክሲዝም « ቃላት » አንዱ ፡ ሆኗል ። ቅጥር ፡ ሚኒስ ትሮችና ፡ ፓርላሜንታውያኖች ፤ ወዝ ፡ አደሩን ፡ የከዱና ፡ የጊዚያችን « ገቢራዊ » ሶሺያሊስቶች ፡ በፓርላሜንታሪ ዝም ፡ ላይ ፡ ሒስ ፡ የማቅረቡን ፡ ጉዳይ ፡ በሞላ ፡ ለሥር ዓተ-አልበኞች ፡ ትተውታል ፤ በዚሁ ፡ አስደናቂና ፡ ተገቢ ፡ መሠረትም ፡ በነሱ ፡ አባባል ፡ በፓርላሜንታሪዝም ፡ ላይ ፡

የሚደረግ ፡ ማንኛውም ፡ ሒስ «ሥርዓተ-አልበኝነት »
ነው!! ስለዚህም « የአደጉት » የፓርላሜንትያዊ ፡ አገሮች ፡
ወዝ ፡ አደሮች ፤ እንዲህ ፡ ያሉ « ሶሺያሊስቶችን » ፤ እን
ደነ ፡ ሸይደማኖች ፤ ዳቪዶች ፤ ሌጊኖች ፤ ሳምባቶች ፤ ሬ
ኖደሎች ፤ ሄንደርሶኖች ፤ ቫንደርቬልዶች ፤ ስታውኒንጎች ፤
ብራንቲንጎች ፤ ቢሶላቲዎችና ፡ ኩባንያዎቻቸው ፡ የመሳሰሉ
ትን ፡ በመጥላት ፤ ከጊዜ ፡ ወደ ፡ ጊዜ ፡ እየጨመረ ፡ የሚ
ሄድ ፡ ድጋፍ ፤ ምንም ፡ እንኳ ፡ የአድርባይነት ፡ የእናት ፡
ልጅ ፡ ቢሆንም ፤ ለሥርዓተ-አልበኛ-ሲንዲካሊዝም ፡ መስ
ጠታቸው ፡ ሊያስገርመን ፡ አይገባም ።

ነገር ፡ ግን ፡ ለማርክስ ፡ አብዮታዊ ፡ ዲያሌክቲክ ፤
ፕሌኻኖቭ ፤ ካውትስኪይና ፡ ሌሎችም ፡ እንዳደረጉት ፡
ሁሉ ፤ ምን ፡ ጊዜም ፡ ባዶና ፡ ጊዜ ፡ ያመጣው ፡ አረፍተ ፡
ነገርና ፡ የአሻንጉሊት ፡ ጩኸት ፡ አልነበረም ። በተለይም ፡
አብዮታዊ ፡ ሁኔታ ፡ በሌለበት ፡ ጊዜ ፡ ቢያንስ ፡ የቡርዥዋ ፡
ፓርላሜንታሪዝም « በረትን » እንኳ ፡ መጠቀም ፡ ባለመ
ቻላቸው ፡ ማርክስ ፡ ሥርዓተ-አልበኞችን ፡ ያለ ፡ ርህራ
ሄ ፡ የመውቀስ ፡ ችሎታ ፡ ነበረው ፤ ይሁንና ፡ ማርክስ ፡ በፓ
ርላሜንታሪዝም ፡ ላይ ፡ በእርግጥ ፡ አብዮታዊ ፡ የወዝ ፡
አደር ፡ ሒስ ፡ የማቅረብ ፡ ችሎታም ፡ ነበረው ።

በጥቂት ፡ ዓመታት ፡ ውስጥ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ የትኛው ፡
የገዥ ፡ መደብ ፡ አባል ፡ በፓርላማ ፡ አማኻኝነት ፡ ሕዝ
ቡን ፡ እንደሚጨቁንና ፡ እንደሚረግጥ ፡ መወሰን — ይህ ፡
ነው ፡ የቡርዥዋ ፡ ፓርላሜንታሪዝም ፡ እውነተኛ ፡ ንጥረ ፡
ሃሳብ ፤ ይህ ፡ በፓርላማዊ-ሕጋዊ ፡ የዘውድ ፡ አገዛዝ ፡ ብቻ ፡
ሳይሆን ፡ በዴሞክራቲክ ፡ ሪፑብሊኮችም ፡ ጭምር ፡
ነው ።

ነገር ፡ ግን ፡ የመንግሥትን ፡ ጥያቄ ፡ ብናቀርብና ፡ ፓርላ
ሜንታሪዝም ፡ እንደአንድ ፡ የመንግሥቱ ፡ ተቋም ፡ ብንቆ
ጥረውና ፡ ይህን ፡ ጉዳይ ፡ በወዝ ፡ አደሩ ፡ ተግባር ፡ አኳያ ፡



ብንመለከት ፤ ከፓርላሜንታሪዝም ፡ ማምለጫው ፡ ምንድ
ነው? ከዚህስ ፡ እንዴት ፡ መላቀቅ ፡ ይቻላል?

አሁንም ፤ አሁንም ፡ ደግምን ፡ እንላለን ፤ የኮሙንን ፡
ልምድ ፡ በማጥናት ፡ የተመሰረቱት ፡ የማርክስ ፡ ትምህ
ርቶች ፡ እጅግ ፡ ስለተረሱ ፡ ለጊዜያችን « ሶሺያል-ዴሞክ
ራቶች » (የጊዜያችንን ፡ ሶሺያሊዝም ፡ የከዱ-ብለህ ፡
አንብብ!) የሥርዓተ-አልበኛና ፡ የአድኃሪ ፡ ካልሆነ ፡ በስተ
ቀር ፤ ሌላ ፡ በፓርላሜንታሪዝም ፡ ላይ ፡ የሚደረግ ፡ ሒስ ፡
በእውነት ፡ ሊገባቸው ፡ አይችልም ።

እርግጥ ፡ ነው ፡ ከፓርላሜንታሪዝም ፡ ማምለጫው ፡
የውክልና ፡ ተቋሞችንና ፡ የምርጫ ፡ መርህን ፡ በመደ
ምሰስ ፡ አይደለም ፤ የውክልና ፡ ተቋሞችን ፡ ከወሬ ፡ ቋት
ነት ፡ ወደሚሰሩ ፡ ድርጅቶች ፡ በመለወጥ ፡ ነው ፡ እንጂ ።
« ኮሙን ፡ መሆን ፡ የነበረበት ፡ ፓርላሜንታዊ ፡ ሳይሆን ፡
የሚሰራ ፡ ድርጅት ፡ ነው ፤ አንድ ፡ ላይ ፡ ሕግ ፡ አውጪም ፤
አስፈጻሚም ፡ መሆን ፡ ነበረበት ።

« ፓርላሜንታዊ ፡ ሳይሆን ፤ የሚሠራ ፡ ድርጅት ፡ ነ
ው » ፤ ይህ ፡ የተባለው ፡ ቀጥታ ፡ በዘመናዊ ፡ ፓርላሜን ፡
ታውያንና ፡ በፓርላሜንታዊ ፡ የሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ እግ
ር ፡ ላሾች ፡ ፊት ፡ ነው! ማንኛውም ፡ ፓርላሜንታዊ ፡ አገርን ፡
ተመልከቱ ፤ ከአሜሪካ ፡ እስከ ፡ ስዊዘርላንድ ፤ ከፈረ
ንሳይ ፡ እስከ ፡ እንግሊዝ ፤ ኖርዌይና ፡ ሌሎችም ፤ በነዚ
ህ ፡ አገሮች ፡ እውነተኛው « የመንግሥት »ስራ ፡ የሚሠ
ራው ፡ በስተጀርባ ፡ ሲሆን ፡ የሚያስፈጽሙት ፡ የአስተዳ
ደር ፡ ክፍሎች ፤ የጽሕፈት ፡ ቤቶችና ፡ የጦር ፡ መምሪ
ያዎች ፡ ናቸው ። ፓርላማ ፡ የተቋቋመበት ፡ ዋና ፡ ዓላማ ፡
በአሉባልታ ፡ ብቻ « ተራውን ፡ ሕዝብ »ለማታለል ፡ ነው ።
ይህም ፡ በጣም ፡ ትክክል ፡ በመሆኑ ፤ የሩሲያ ፡ ሪፑብሊክ ፤
የቡርዥዋ-ዴሞክራቲክ ፡ ሪፑብሊክ ፡ እንኳ ፡ ሳትቀር ፤
ያለውን ፡ ፓርላማ ፡ ከማቋቋሟ ፡ በፊት ፡ እነዚህ ፡ የፓር
ላማ ፡ ሃጢአቶችን ፡ በሙሉ ፡ አሳይታ ፡ ነበር ። እንደነ ፡






ስኮቤሌቭና ፡ ጸረተሊ ፤ ቼርኖቭና ፡ አቭክሴንትዬቭ ፡
የመሳሰሉት ፡ የብስብሱ ፡ ጮርቃነት ፡ ጀግኖች ፤ በነው
ረኛው ፡ የቡርዥዋ ፡ ፓርላሜንታሪዝም ፡ ዓይነት ፡ ሶቪዬቶ
ችን ፡ ለማጐደፍ ፤ ወደባዶ ፡ የወሬ ፡ ቋቶች ፡ ለመለወጥ ፡
በቅተዋል ። በሶቪዬቶች ፡ ውስጥ « ሶሺያሊስት » ሚኒስ
ትሮች ፡ የዋህ ፡ ሰዎችን ፡ በንግግርና ፡ በውሳኔዎች ፡ ያታል
ላሉ ። በአገዛዙ ፡ ውስጥ ፡ የማያቋርጥ ፡ መጐተት ፡ አለ ፤
ይህ ፡ በአንድ ፡ በኩል ፤ በተቻለ ፡ ብዛት ፡ ሶሺያሊስት-
አብዮታውያንና ፡ ሜንሼቪኮች ፡ በየተራ ፡ ወደ « ፍት
ፍቱ » ጥሩ ፡ ገቢና ፡ ክብር ፡ ወዳላቸው ፡ ቦታዎች ፡ ለማስ
ጠጋት ፡ ሲሆን ፤ በሌላ ፡ በኩል ፡ ደግሞ ፡ የሕዝቡን « ሕሊ
ና ፡ ለማሰር » ነው ። የጽሕፈት ፡ ቤቶችና ፡ የመምሪያ ፡
ድርጅቶች ፡ ግን «የመንግሥቱን »ሥራ « ይሠራሉ»!

« ዴሎ ፡ ናሮዳ »[18] የተባለው ፡ የገዢው ፡ የሶሺያሊ
ስት ፡ አብዮታዊ ፡ ፓርቲ ፡ ልሳን ፡ በርእስ ፡ አንቀፅ ፡ ጽሑ
ፉ « ሁሉም »በፖለቲካ ፡ ሽርሙጥና ፡ የተሰማሩበት ፡
« የጥሩ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ » ሰዎች ፡ ተወዳዳሪ ፡ ከሌለው ፡
ግልፅነት ፡ ጋር ፡ እንዳመነው ፤ « በሶሺያሊስቶቹ » (ይቅ
ርታ ፡ አድርጉልን) የሚመሩት ፡ ሚኒስትሮች ፡ እንኳ ፡ ሳ
ይቀሩ ፤ መላ ፡ የቢሮክራሲው ፡ አውታር ፡ ሳይቀር ፡ የነበረ
ው ፡ በመሰረቱ ፡ አልተለወጠም ፤ የሚሠራውም ፡ በአ
ሮጌው ፡ መንገድ ፡ ነው ፤ በተጀመሩት ፡ አብዮታዊ ፡ እርም
ጃዎች ፡ ላይም ፡ ፍጹም « ነፃ » በሆነ ፡ አኳኋን ፡ አሻጥር ፡
ይሠራሉ! ይህ ፡ ኑዛዜ ፡ ባይኖርም ፡ እንኳ ፡ የሶሺያሊስት-
አብዮታውያንና ፡ የሜንሼቪኮች ፡ በመንግሥቱ ፡ አገዛዝ ፡
የመሰግሰግ ፡ ህያው ፡ ታሪክ ፡ ይኸን ፡ አያረጋግጥም ፡
እንዴ? እዚህ ፡ መጠቀስ ፡ ያለበት ፡ ነገር ፡ ቢኖር ፡ ከካ
ዴቶች[13] ፡ ጋር ፡ በሚኒስቴርነት ፡ ቡድን ፡ ሆነው ፡ እነ
አቶ ፡ ቼርኖቭ ፤ ሩሳኖቭ ፤ ዘንዚኖቭና ፡ ሌሎችም « የዴሎ ፡ ና
ሮዳ » አዘጋጆች ፡ በፍጹም ፡ ህፍረተቢስነት ፤ ቅንጣት ፡
ታህል ፡ እንኳ ፡ ሳያፍሩ ፤ ልክ ፡ እንደ ፡ ኢምንት ፡ ነገር ፡



በመቁጠር ፡ እንደሚሉት ፤ « በነሱ » የሚኒስትሮች ፡
ሁሉም ፡ እንደነበረው ፡ ነው ፤ ምንም ፡ ነገር ፡ አልተለወ
ጠም!! የገጠሩን ፡ ተራ ፡ ሕዝብ ፡ ለማታለል ፡ አብዮታዊ ፡
ዴሞክራሲያዊ ፡ ሀረጎችን ፡ መለፈፍ ፤ የካፒታሊስቶችን ፡
« ልብ ፡ ለማረስ » ቢሮክራሲያዊ ፡ የጽሕፈት ፡ ቤቶ
ችን ፡ ስንክሳር ፡ ማብዛት — ይኸውላችሁ ፤ ይህ ፡ ነው ፡
« የሀቀኛው » ኅብረት ፡ ንጥረ ፡ ሀሳብ ።

ኮሙን ፡ ወራዳውንና ፡ ብስብሱን ፡ የቡርዥዋ ፡ ኅብ
ረተ ፡ ሰቡ ፡ ፓርላሜንታሪዝምን ፡ የሚለውጠው ፡ የሃሳ
ብና ፡ የክርክር ፡ ነፃነት ፡ ወደ ፡ ማታለያ ፡ ተግባር ፡ ወደማ
ይሸቀለቀልበት ፡ ተቋም ፡ ነው ፤ ምክንያቱም ፡ ፓርላሜን
ታሪውያኖች ፡ ራሳቸው ፡ ህጉን ፡ አርቅቀው ፤ ራሳቸው ፡
መፈጸም ፡ አለባቸው ፤ ራሳቸው ፡ በሥራ ፡ ላይ ፡ አውለው፡
ምን ፡ ዓይነት ፡ ውጤት ፡ እንደሚሰጥ ፡ መመርመር ፡ አለ
ባቸው ፤ በመራጮቻቸው ፡ ፊትም ፡ ቀጥታ ፡ ተጠያቂነት ፡
አለባቸውና ። የውክልና ፡ ተቋሞች ፡ ይኖራሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡
ፓርላሜንታሪዝም ፡ እንደልዩ ፡ ኃይል ፤ እንደ ፡ ህግ ፡ አው
ጪና ፡ ህግ ፡ አስፈጻሚን ፡ የመሰለ ፡ የሥራ ፡ ክፍፍል ፤
ለእንደራሴዎች ፡ ልዩ ፡ መብት ፡ ያለው ፡ ቦታ ፡ መስጠት ፤
እዚህ ፡ አይኖርም ። ያለ ፡ የውክልና ፡ ተቋም ፡ ዴሞክራሲ ፤
እንዲያውም ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ ዴሞክራሲ ፡ ሊኖር ፡ ይች
ላል ፡ ብሎ ፡ መገመት ፡ አይቻልም ፤ ነገር ፡ ግን ፤ በቡርዥ
ዋ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ላይ ፡ ያለን ፡ ሒስ ፡ ለኛ ፡ እንዲያው ፡
ባዶ ፡ ቃላት ፡ ካልሆነ ፤ የቡርዥዋውን ፡ ገዥነት ፡ ለመ
ጣል ፡ የምናደርገው ፡ ጥረት ፤ ሜንሼቪኮችና ፡ ሶሺያሊስ
ት-አብዮታውያን ፡ ሸይደማኖችና ፡ ሌጊኖች ፤ ሳምባቶ
ችና ፡ ቫንደርቬልድስ ፡ እንደሚያደርጉት ፡ ከወዝ ፡ አደሩ ፡
ድምፅን ፡ ለመልቀም ፡ የሚጠቀሙበት « የምርጫ » ሀረግ ፡
ብቻ ፡ ካልሆነ ፤ የኛ ፡ ቁርጠኛና ፡ እውነተኛ ፡ ፍላጎት ፡ ከሆ
ነ ፤ ዴሞክራሲ ፡ ያለ ፡ ፓርላሜንታሪዝም ፡ ሊኖር ፡ ይች
ላል ፤ መኖርም ፡ አለበት ።





እዚህ ፡ ላይ ፡ መጥቀሱ ፡ ትምህርታዊ ፡ የሚመስለን ፤ ለኮሙንና ፡ ለወዝ ፡ አደሩ ፡ ዴሞክራሲ ፡ አስፈላጊ ፡ ስለሆኑት ፡ ስለእነዛ ፡ ባለሥልጣኖች ፡ ተግባሮች ፡ በሚናገርበት ፡ ጊዜ ፡ ማርክስ ፡ ለማነፃፀር ፡ የሚወስደው « የማንኛውም ፡ ሌላ ፡ አሰሪ » ሠራተኞችን ፡ ነው ፤ ማለትም ፡ ተራ ፡ የካፒታሊስት ፡ የሥራ ፡ ድርጅት « ወዝ ፡ አደሮችን ፤ ተቆጣጣሪዎችንና ፡ የሂሳብ ፡ ሹሞችን » ነው ።

ማርክስ « አዲስ » ኅብረተ ፡ ሰብን ፡ ደረሰ ፡ ወይም ፡ ፈለሰፈ ፡ በማለት ፡ ቅንጣት ፡ ታህል ፡ ተምኔታዊነት ፡ የለበትም ። እሱ ፡ ያጠናው ፡ አዲስ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ከአሮጌው ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ መወለዱን ፡ እንደሕጋዊ ፡ ሥነ ፡ ፍጥረታዊ ፡ ታሪካዊ ፡ ሂደት ፡ ነው ፤ ከሁለተኛው (ከአሮጌው)ወደ ፡ አንደኛው (ወደ ፡ አዲሱ) የሽግግር ፡ ቅርፆችን ፡ ነው ። ማርክስ ፡ ጭብጥ ፡ የሆነውን ፡ የሰፊ ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ እንቅስቃሴ ፡ ልምድን ፡ ወስዶ ፡ በመመርመር ፤ ከዚሁም ፡ ገቢራዊ ፡ ትምህርቶችን ፡ ለመቅሰም ፡ ይጥራል ። ታላላቅ ፡ አብዮተኞች ፡ ፈላስፎች ፡ ምንም ፡ ሳይፈሩ ፡ ከታላላቅ ፡ የጭቁን ፡ መደብ ፡ እንቅስቃሴዎች ፡ ልምድ ፡ እንደተማሩ ፡ ሁሉ ፤ ምን ፡ ጊዜም ፡ ቢሆን ፡ እንቅስቃሴዎቹን (እንደ ፡ ፕሌኻኖቭ « መሳርያ ፡ ማንሳት ፡ አያስፈልግም ፡ ነበር » ፤ ወይንም ፡ እንደ ፡ ፀረተሊ « አንድ ፡ መደብ ፡ በራሱ ፡ መደብ ፡ መወሰን ፡ አለበት » እንዳሉት ፡ ዓይነት) ፤ በጥራዝ ፡ ነጠቅነት « የሞራል ፡ ፌዝ » እንዳልተመለከቱአቸው ፡ ሁሉ ፤ ማርክስም ፡ ከኮሙኑ «ተምሯል » ።

ቢሮክራሲ ፡ ወድያውኑ ፤ የትም ፡ ቦታ ፡ እስከ ፡ መጨረሻ ፡ መደምሰስ ፡ አለበት ፡ የሚለው ፡ ከጥያቄ ፡ ውጭ ፡ ነው ። ይህ ፡ ተምኔታዊነት ፡ ነው ። ይሁን ፡ እንጂ ፡ ወድያውኑ ፡ አሮጌውን ፡ የቢሮክራሲ ፡ መኪናን ፡ መስበርና ፡ ወድያውኑ ፡ ማንኛውም ፡ ቢሮክራሲን ፡ ደረጃ ፡ በደረጃ ፡ ለማስወገድ ፡ የሚያስችል ፡ አዲስ ፡ መኪናን ፡ ለመመስረት ፡ መጀመር ፡ ግን ፡ ተምኔታዊ ፡ አይደለም ፤ ይህ ፡



የኮሙኑ ፡ ልምድ ፡ ትምህርት ፡ ነው ፤ ይህ ፡ የአብዮታዊው ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ቀጥተኛና ፡ አጣዳፊ ፡ ተግባር ፡ ነው ።

ካፒታሊዝም « የመንግሥት »አስተዳደርን ፡ ሥራ ፡ ያቃልላል ፤ « አለቃነትን » ወደ ፡ ጐን ፡ እንዲተው ፡ በማድረግ ፡ ነገሩን « ወዝ ፡ አደሮችን ፤ ተቆጣጣሪዎችንና ፡ የሂሳብ ፡ ሹሞችን » በመላ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ስም ፡ ለመቅጠር ፡ ወደሚችል ፡ ወደ ፡ ወዝ ፡ አደሮች (እንደ ፡ ገዢ ፡ መደብ) መደራጀት ፡ ያመራዋል ።

እኛ ፡ ተምኔታውያን ፡ አይደለንም ። ወድያውኑ ፡ ያለ ፡ ማንኛውም ፡ አስተዳደር ፤ ያለ ፡ ማንኛውም ፡ ታዛዥነት ፡ መሄድ ፡ አለብን ፡ ብለን « አናልምም » ። እነዚህ ፡ የሥርዓተ ፡ አልበኞች ፡ ህልሞች ፡ ናቸው ። የሚመሰረቱት ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ ተግባር ፡ ካለመገንዘብ ፡ የተነሳ ፡ ስለሆነ ፡ ከሥረ ፡ መሠረታቸው ፡ ለማርክሲዝም ፡ ባእድ ፡ ናቸው ፤ በገቢርም ፡ የሚያገለግሉት ፤ ሰዎች ፡ ሌላ ፡ እስከሚሆኑ ፤ እስከሚለወጡ ፡ ድረስ ፡ በሚል ፡ ፈሊጥ ፤ ሶሺያሊስት ፡ አብዮቱን ፡ ለመጐተት ፡ ብቻ ፡ ነው ። አይደለም ፤ እኛ ፡ የምንፈልገው ፡ ሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ አሁን ፡ እንዳለው ፤ ካለው ፡ ሕዝብ ፡ ጋር ፡ ነው ፤ ከመታዘዝ ፤ ከቁጥጥር ፤ « ከተቆጣጣሪዎችና ፡ ከሂሳብ ፡ ሹሞች » ካልተላቀቀ ፡ ሕዝብ ፡ ጋር ፡ ነው ።

ይሁን ፡ እንጂ ፤ ታዛዥነቱ ፡ ለታጠቀው ፤ የመላ ፡ ጭቁንና ፡ ሠርቶ ፡ አደር ፡ ሕዝቦች ፡ ግምባር ፡ ቀደም ፡ ለሆነው ፤ ማለትም ፡ ለወዝ ፡ አደሩ ፡ መሆን ፡ አለበት ። የመንግሥት ፡ ባለሥልጣኖች ፡ ልዩ « አለቃነትን » ፤ ወድያውኑ ፤ ሳይውል ፡ ሳያድር ፤ በቀላል ፡ ወደ « የተቆጣጣሪዎችና ፡ የሂሳብ ፡ ሹሞች » ሥራ ፡ መለወጥ ፡ መጀመር ፡ ይቻላል ፤ መጀመርም ፡ አለበት ፤ እነዚህ ፡ ተግባሮች ፡ በሙሉ ፡ አሁን ፡ በአብዛኛው ፡ የከተማ ፡ ነዋሪ ፡ ሕዝብ ፡ ችሎታ ፡ መጠን ፡ በመሆናቸው « በወዝ ፡ አደሩ ፡ ደመወዝ » ሊከናወኑ ፡ ይችላሉ ።

እኛ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፤ ራሳችን ፡ ካለው ፡ ካፒታሊዝም ፡ ከመሠረተው ፡ በመነሳት ፤ እንደሠራተኞች ፡ በራሳችን ፡ ልምድ ፡ በመመርኰዝ ፤ የታጠቁ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ መንግሥታዊ ፡ ሥልጣን ፡ የሚደግፈው ፡ ጥብቅና ፡ ጠንካራ ፡ ሥነ ፡ ሥርዓትን ፡ በማቋቋም ፤ ከፍተኛ ፡ ምርትን ፡ እናደራጃለን ፤ የመንግሥት ፡ ባለሥልጣኖችን ፡ ሚና ፡ እኛ ፡ የምንሰጣቸውን ፡ ትእዛዝ ፡ ወደሚፈጽሙ ፤ በሃላፊነት ፡ ወደሚጠየቁ ፤ ወደሚሻሩ ፡ ወደሚለወጡ ፤ በመጠኑ ፡ ወደሚከፈሉ « ተቆጣጣሪዎችና ፡ የሂሳብ ፡ ሹሞች » (እርግጥ ፤ ከሁሉም ፡ ፈርጅ ፤ ዓይነትና ፡ ደረጃ ፡ ቴክኒሽያኖች ፡ ጭምር) እናደርጋቸዋለን — ይህ ፡ ነው ፡ የኛ ፡ ወዝ ፡ አደራዊ ፡ ተግባር ፤ ከዚህ ፡ ነው ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት ፡ ግቡን ፡ ሲመታ ፡ መጀመር ፡ የሚቻለው ፤ ያለበትም ። በከፍተኛ ፡ ምርት ፡ የተመሰረተ ፡ የዚህ ፡ ዓይነት ፡ ጅምር ፡ ራሱ ፡ ደረጃ ፡ በደረጃ ፡ የማንኛውም ፡ ቢሮክራሲ « መክሰምን » ያስከትላል ፤ እንደዚሁም ፡ ደረጃ ፡ በደረጃ ፡ ሥነ ፡ ሥርዓት — ቅንፍ ፡ የሌለበት ፡ ሥነ ፡ ሥርዓት ፤ ከቅጥር ፡ ባርነት ፡ ጋር ፡ የማይመሳሰል ፡ ሥነ ፡ ሥርዓት ፡ ወደ ፡ መመሥረት ፡ ይመራናል ፤ በዚህ ፡ ሥነ ፡ ሥርዓት ፡ ስር ፡ የቁጥጥርና ፡ የተጠሪነት ፡ ሥራዎች ፡ ከጊዜ ፡ ወደጊዜ ፡ እየቀለሉ ፡ ስለሚሄዱ ፡ እያንዳንዱ ፡ ሰው ፡ በየተራ ፡ ይሰራቸዋል ፤ ከዚህም ፡ የተለመዱ ፡ ይሆናሉ ፤ በመጨረሻም ፡ የሕዝቡ ፡ ልዩ ፡ ክፍሎች ፡ ልዩ ፡ ተግባሮች ፡ መሆናቸው ፡ ይቀራል ።

አንድ ፡ የአለፈው ፡ ክፍለ ፡ ዘመን ፡ ፸ ኛዎቹ ፡ ዓ. ም. አስተዋይ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራት ፡ የፖስታ ፡ አገልግሎትን ፡ የሶቪያሊስት ፡ ኤኮኖሚ ፡ ሥርዓት ፡ ጥሩ ፡ ምሳሌ ፡ ነው ፡ ሲል ፡ ሰይሞታል ። ይህ ፡ በጣም ፡ ትክክል ፡ ነው ። በአሁኑ ፡ ጊዜ ፡ የፖስታ ፡ አገልግሎት ፡ በመንግሥታዊ-ካፒታሊስታዊ ፡ ሞኖፖሊ ፡ መልክ ፡ የተደራጀ ፡ ነው ። ኢምፔሪያሊዝም ፡ ደረጃ ፡ በደረጃ ፡ ትሬስቶችን ፡ ሁሉ ፡ ተመሳሳይ ፡ መልክ ፡ ወዳላቸው ፡ ድርጅቶች ፡ በመለወጥ ፡ ላይ ፡ ነው ። በ



ሥራና ፡ በረሃብ ፡ በተጐሳቆሉት «ተራ »ሠርቶ ፡ አደሮች ፡ ላይ ፡ እዚህም ፡ የተዘረጋው ፡ ያው ፡ የቡርዥዋ ፡ ቢሮክራሲ ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፤ የኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ የአመራር ፡ ሜካኒዝም ፡ እዚህ ፡ ዝግጁ ፡ ነው ። ካፒታሊስቶች ፡ ከተፈነገሉ ፤ በታጠቀ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ ጠንካራ ፡ ክንድ ፡ የነዚህ ፡ በዝባዦች ፡ ተቃውሞ ፡ ከተደመሰሰና ፤ የዘመናዊው ፡ መንግሥት ፡ የቢሮክራሲ ፡መኪና ፡ ከተንኮታኮተ ፤ « ከተባይ » ነፃ ፡ የሆነ ፡ በከፍተኛ ፡ ቴክኒክ ፡ የተሟላ ፡ ሜካኒዝም ፡ ይኖረናል ፤ ይህንንም ፡ ሜካኒዝም ፡ የተባበሩት ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ ራሳቸው ፡ ቴክኒሺያኖችን ፤ ተቆጣጣሪዎችንና ፡ የሂሳብ ፡ ሹሞችን ፡ ቀጥረው ፤ እንደ ፡ ሁሉም « የመንግሥት » ባለሥልጣኖች ፡ ለሁሉም ፡ በወዝ ፡ አደሩ ፡ ደመወዝ ፡ ልክ ፡ እየከፈሉ ፡ ራሳቸው ፡ በደንብ ፡ ሊያካሂዱት ፡ ይችላሉ ። ይህ ፡ ነው ፡ መላ ፡ ትሬስቶችን ፡ በሚመለከት ፡ በኩል ፡ ወድያውኑ ፡ በሥራ ፡ ላይ ፡ መዋል ፡ ያለበት ፡ የተጨበጠ ፡ ገቢራዊ ፡ ተግባር ፤ የዚህ ፡ ተግባር ፡ በሥራ ፡ ላይ ፡ መዋል ፡ ሰርቶ ፡ አደሮችን ፡ ከብዝበዛ ፡ ይገላገላል ፤ ይህ ፡ ተግባር ፡ ኮሙኑ ፡ በገቢር ፡ ማዋል ፡ የጀመረው (በተለይም ፡ መንግሥትን ፡ በማቋቋም ፡ በኩል) ልምድን ፡ ያጤነ ፡ ነው ።

ቴክኒሺያኖች ፤ ተቆጣጣሪዎችና ፡ የሂሳብ ፡ ሹሞች ፤ እንደዚሁም ፡ መላ ፡ ሹማምንቶች ፡ የሚያገኙት ፡ ክፍያ «ከወዝ ፡ አደሩ ፡ ደመወዝ » እንዳይበልጥ ፤ የአገሪቱ ፡ ኤኮኖሚ፡ በሙሉ ፡ እንደፖስታ ፡ አገልግሎት ፡ ዓይነት ፡ ሆኖ ፡ ተደራጅቶ ፡ በታጠቀው ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ቁጥጥር ፡ ስርና ፡ በታጠቀው ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ መሪነት ፡ ስር ፡ መሆን ፡ አለበት — ይህ ፡ነው ፡ የኛ ፡ አጣዳፊ ፡ ዓላማ ፤ የዚህ ፡ ዓይነት ፡ መንግሥት ፤ በዚህ ፡ ዓይነት ፡ የኤኮኖሚ ፡ መሰረት ፡ የተመሠረተ ፡ መንግሥት ፡ ያስፈልገናል ። ይህ ፡ ነው ፡ የፓርላሜንታሪዝም ፡ መደምሰስና ፡ የውክልና ፡ ተቋሞችን ፡ ማቆየት ፡ የሚሰጠን ፤ ይህ ፡ ነው ፡ ሠርቶ ፡ አደር ፡ መደቦችን ፡ ቡርዥዋው ፡ በተቋሞቹ ፡ ከሚያደርገው ፡ ሽርሙጥና ፡ የሚገላግላቸው ።

## ፬. የብሄራዊ ፡ አንድነትን ፡ ማደራጀት ።

« … ኮሙን ፡ ሊያዳብረው ፡ ጊዜ ፡ ያላገኘለት ፡ የብሄራዊ ፡ አንድነት ፡ አጭር ፡ ንድፍ ፡ በግልፅ ፡ እንደሚያሳየን ፡ ኮሙን … የመጨረሻ ፡ ትንሿ ፡ ገጠር ፡ ሳትቀር ፡ የፖለቲካ ፡ ቅርፅ ፡ ልትሆን ፡ ነበር … የፓሪስም « ብሄራዊ ፡ መልእክተኞች » ከኮሙኖች ፡ በተመረጡ ፡ ነበር ።

«… በማእከላዊው ፡ አገዛዝ ፡ እጅ ፡ ገና ፡ የቀሩት ፡ ጥቂቶች ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በጣም ፡ አስፈላጊ ፡ የሆኑ ፡ ተግባሮች — ሆን ፡ ብለው ፡ መወገድ ፡ አለባቸው ፡ እያሉ ፡ እንዳጣመሙት ፡ ሳይሆን ፤ ለኮሙን ፡ መተላለፍ ፡ ነበረባቸው ፤ ማለትም ፡ ጥብቅ ፡ ሃላፊነት ፡ ለነበራቸው፡ ባለሥልጣኖች …

… ብሄራዊ ፡ አንድነት ፡ የሚፈርስበት ፡ ምክንያት ፡ አልነበረም ፤ እንድያውም ፡ በአንፃሩ ፡ በኮሙናል ፡ ደምብ ፡ መሠረት ፡ የሚደራጅበት ፡ እንጂ ። ብሄራዊ፡ አንድነት ፡ እውነታ ፡ መሆን ፡ የነበረበት ፤ ይህንን ፡ አንድነት ፡ በሥራ ፡ ላይ ፡ አውላለሁ ፡ እያለ ፤ ከአንድነቱ ፡ ነፃ ፡ ሆኖ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ከሱ ፡ በላይ ፡ ለመሆን ፡ የሚፈልገውን ፤ የመንግሥትን ፡ ሥልጣን ፡ በመደምሰስ ፡ ነበር ። ይህ ፡ የመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ እንደ ፡ እውነቱ ፡ ከሆነ ፡ በብሄሩ ፡ አካል ፡ ላይ ፡ ያለ ፡መዥገር፡ ነው … ስለሆነም ፡ የአረጀው ፡ የመንግሥት ፡ ስልጣን ፡ ንጹህ ፡ የመጨቆኛ ፡ ብቻ ፡ የነበሩት ፡ አካሎች ፡ መወገድ ፡ ነበረባቸው ፤ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ በላይ ፡ ለመቆም ፡ መብት ፡ አለኝ ፡ ከሚለው ፡ ሥልጣንም ፡ ህጋዊ ፡ ተግባሮች ፡ ወስዶ ፡ በሃላፊነት ፡ ለሚጠየቁ ፡ የኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ አገልጋዮች ፡ መሰጠት ፡ አለበት ።»

እነዚህ ፡ የማርክስ ፡ አስተያየቶች ፡ የዘመናዊ ፡ ሶሺ



ያል-ዴሞክራሲ ፡ አድርባዮች ፡ ምን ፡ ያህል ፡ እንዳልገባቸው — ምናልባትም ፡ በትክክል ፡ ለመናገር ፤ ምን ፡ ያህል ፡ ሊገባቸው ፡ እንዳልፈለጉ — በግልፅ ፡ የሚያሳየው ፡ ከሃዲው ፡ ቤርንስተይን ፡ የጻፈው « የሶሺያሊዝም ፡ ተቀዳሚ ፡ ሁኔታዎችና ፡ የሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ ተግባሮች » የተባለው ፡ ባለሄሮስትራያዊ ፡ ዝና ፡ መጽሐፍ ፡ ነው ። በተለይም ፡ ከዚህ ፡ በላይ ፡ በተጠቀሰው ፡ የማርክስ ፡ ጥቅስን ፡ በሚመለከት ፡ ቤርንስተይን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ጽፎአል ፤ « የፖለቲካ ፡ ይዘቱን ፡ በሚመለከተው ፡ በኩል » ይህ ፡ ፕሮግራም « በሁሉም ፡ ጥልቅ ፡ ባህርያቱ ፡ የሚታየው ፡ ከፕሩዶን ፡ ፌዴራሊዝም ፡ ጋር ፡ በጣም ፡ ተመሳሳይ ፡ መሆኑን ፡ ነው … ምንም ፡ እንኳ ፡ በሌሎች ፡ ነጥቦች ፡ ላይ ፡ ልዩነት ፡ ቢኖራቸውም ፡ ማርክስና 'ንዑስ ፡ ቡርዧዋው' ፕሩዶን (« ንዑስ ፡ ቡርዧዋ » የሚለውን ፡ ቃል ፡ ቤርንስተይን ፡ ያስቀመጠው ፡ በቅንፍ ፡ ውስጥ ፡ ነው ፤ ይኸውም ፡ የምፀት (irony) ትርጉምን ፡ ለመስጠት) በነዚህ ፡ ነጥቦች ፡ ላይ ፡ ያላቸው ፡ የአስተሳሰብ ፡ መስመር ፡ የተቻለውን ፡ ያህል ፡ የተቀራረበ ፡ ነው ።» እርግጥ ፡ ነው ፤ ብሎ ፡ ይቀጥላል ፡ ቤርንስተይን ፤ የማዘጋጃ ፡ ቤቶች ፡ አስፈላጊነት ፡ በማደግ ፡ ላይ ፡ ነው ፤ ነገር ፡ ግን « እኔን ፡ የሚያጠራጥረኝ ፡ ማርክስና ፡ ፕሩዶን ፡ እንደሚመለከቱት ፡ የዴሞክራሲ ፡ የመጀመሪያ ፡ ሥራ ፡ ዘመናዊው ፡ መንግሥትን ፡ መፈንገልና (auflösung) የነሱን ፡ ድርጅቶችንም ፡ ፍጹም ፡ መለወጥ (Umwandlung) የሚቻል ፡ መሆኑን ፤ ብሄራዊ ፡ ስብሰባ ፡ ከክፍለ ፡ ሀገር ፡ ወይም ፡ ከቀበሌ ፡ ስብሰባ ፡ ወኪሎች ፡ ማቋቋምን ፤ እነዚህም ፡ በበኩላቸው ፡ ከኮሙኖች ፡ ወኪሎች ፡ የተውጣጡ ፡ መሆናቸውን ፡ ነው ፤ በመጨረሻም ፤ የነበረው ፡ የብሄራዊ ፡ ውክልና ፡ ቅርፅ ፡ ይጠፋል ፡ ማለት ፡ ነው ።» (ቤርንስተይን ፤ « ተቀዳሚ ፡ ሁኔታዎች » ፤ የጀርመን ፡ እትም ፤ ገጽ ፡ የ፻፬ እና ፡ ፪፻፳ ፤ ፲፰፻፺፱ ዓ. ም.)





« ተባይ ፡ የሆነውን ፡ የመንግሥት ፡ ሥልጣን ፤ መደምሰስ » የሚለው ፡ የማርክስን ፡ ርዕየት ፡ በፕሩዶን ፡ ፌዴራሊዝም ፡ ጋር ፡ ማምታታት ፤ ይህ ፡ በጣም ፡ የማይቻል ፡ ነው! ቢሆንም ፡ ይህ ፡ በድንገት ፡ አይደለም ፤ ምክንያቱም ፡ ማርክስ ፡ እዚህ ፡ የሚናገረው ፡ በጭራሽ ፡ በዋህድነት ፡ (ሴንትራሊዝም) አንፃር ፡ ስለፌዴራሊዝም ፡ ሳይሆን ፤ ስለ አሮጌው ፤ በሁሉም ፡ ቡርዥዋ ፡ አገሮች ፡ ስላለው ፡ የቡርዥዋ ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ መስበር ፡ መሆኑን ፡ ለአድርባይው ፡ ወደ ፡ ጭንቅላቱ ፡ አይመጣም ።

ለአድርባይው ፡ ወደ ፡ ጭንቅላቱ ፡ የሚመጣለት ፡ በራሱ ፡ ዙርያ ፡ የሚያየውን ፤ በንኡስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ጮርቃነትና « የጠጋኝነት » እግድሳት (stagnation) ፡ አካባቢ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ እሱም « ማዘጋጃ ፡ ቤቶች » ብቻ ፡ ናቸው! አድርባዩ ፡ ስለ ወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት ፡ ማሰቡን ፡ እንኳ ፡ ትቶታል ።

ይህ ፡ በጣም ፡ ያስቃል ። ነገር ፡ ግን ፤ የሚያስደንቀው ፡ በዚህ ፡ ነጥብ ፡ ላይ ፡ ማንም ፡ አለመከራከሩን ፡ ነው ። ቤርንስተይንን ፡ ብዙዎቹ ፡ ወቅሰውት ፡ ነበር ፤ በተለይም ፡ በሩሲያ ፡ ሥነ ፡ ጽሑፍ ፡ ፕሌኻኖቭ ፤ በአውሮጳ ፡ ሥነ ፡ ጽሑፍ ፡ ካውትስኪይ ፤ ይሁን ፡ እንጂ ፡ አንዳቸውም ፡ ስለዚሁ ፡ ማርክስ ፡ በቤርንስተይን ፡ ስለመጣመሙ ፡ አንዳችም ፡ አልተናገሩም ።

አድርባይው ፡ እንደዚያ ፡ በአብዮታዊ ፡ መንፈስ ፡ ማሰብንና ፡ ስለአብዮት ፡ ማውጣት ፡ ማውረዱን ፡ ስለረሳ ፤ ማርክስን ፡ ሥርዓተ ፡ አልበኝነትን ፡ ከመሰረተው ፡ ከፕሩዶን ፡ ጋር ፡ በማምታታት ፤ « ፌዴራሊዝምን » ለማርክስ ፡ ይለጥፍበታል ። ኦርቶዶክሳዊ ፡ ማርክሲስቶችና ፡ የአብዮታዊው ፡ ማርክሲስት ፡ ቴዎሪ ፡ ተከላካዮች ፡ ሊባሉ ፡ የሚሹት ፡ ካውትስኪይና ፡ ፕሌኻኖቭ ፡ በዚህ ፡ ነጥብ ፡ ላይ ፡ ምንም ፡ አይናገሩም! በማርክሲዝምና ፡ በሥርዓተ ፡ አልበኝነት ፡ መካከል ፡ ስላለው ፡ ልዩነት ፤ ያለው ፡ የርዕየቶች ፡ ከፍተኛ ፡ ማጉደፍ ፡ ስሩ ፡ ያለው ፡ እዚህ ፡ ነው ፤ ይህ ፡ የሁለቱም ፡ የካውትስካውያንና ፡ የአድርባዮች ፡ ባህርይ ፡ ነው ፤ ወደዚህ ፡ ጉዳይ ፡ እንደገና ፡ በኋላ ፡ እንመለስበታለን ።



ማርክስ ፡ ስለኮሙን ፡ ልምድ ፡ ባለው ፡ ጥቅስ ፡ የፌዴራሊዝም ፡ ምልክት ፡ ፍጹም ፡ የለበትም ። ማርክስ ፡ ከፕሩዶን ፡ ጋር ፡ የተስማማበትን ፡ ነጥብ ፡ ለአድርባዩ ፡ ቤርንስተይን ፡ አልታየውም ። ማርክስ ፡ ከፕሩዶን ፡ ጋር ፡ ባልተስማማበት ፡ ነጥብ ፡ ላይ ፡ ግን ፡ ቤርንስተይን ፡ ስምምነቱ ፡ ይታየዋል ።

ማርክስ ፡ ከፕሩዶን ፡ ጋር ፡ በሚስማማበት ፤ ሁለቱም ፡ ዘመናዊው ፡ የመንግሥት ፡ መኪና « መሰበር » አለበት ፡ ስለሚሉ ፡ ነው ። በዚህ ፡ ማርክሲዝም ፡ ከሥርዓተ ፡ አልበኝነት (ከፕሩዶንም ፤ ከባኩኒንም) ጋር ፡ የሚስማሙበት ፡ ነጥብ ፡ አድርባዮችም ፡ ሆኑ ፡ ካውትስካውያን ፡ ሊያዩ ፡ አይፈልጉም ፤ ምክንያቱም ፡ ከማርክሲዝም ፡ ጋር ፡ የተለያዩበት ፡ ነጥብ ፡ ነውና ።

ማርክስ ፡ ከፕሩዶንም ፤ ከባኩኒንም ፤ ከሁለቱም ፡ ጋር ፡ የተለያየበት ፡ በፌዴራሊዝም ፡ ጥያቄ ፡ ላይ ፡ ነው ፤ (የወዝ ፡ አደሩ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ አይነሳም) ፌዴራሊዝም ፡ የሚመነጨው ፡ ከንዑስ ፡ ቡርዥዋው ፡ ሥርዓተ ፡ አልበኝነት ፡ ርዕየት ፡ ነው ። ማርክስ ፡ ሴንትራሊስት (ዋህዳዊ) ነበር ፡ ከላይ ፡ ባቀረብነው ፡ የአስተያየቱ ፡ ጥቅስ ፡ ውስጥ ፡ ምንም ፡ ከዋህድነት ፡ ያፈገፈገበት ፡ ቦታ ፡ የለም ። እነዚያ ፡ በጮርቃነት ፡ ተወጥረው ፡ በመንግሥት ፡ ላይ « የጣኦት ፡ አምልኮ ፡ ያላቸው ፡ ሰዎች ፡ ብቻ ፡ ናቸው ፤ የቡርዥዋ ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ መሰበርን ፡ እንደዋህድነት ፡ መሰበር ፡ የሚመለከቱ፡

አሁን ፡ ወዝ ፡ አደሩና ፡ ድሃ ፡ አርሶ ፡ አደሮች ፡ የመንግሥት ፡ ስልጣንን ፡ በእጃቸው ፡ ቢያደርጉ ፤ ራሳቸው ፡ በነፃ ፡ በኮሙኖች ፡ ቢደራጁና ፤ ካፒታልን ፡ ለመምታት ፡ የካፒታሊስቶችን ፡ ተቃውሞ ፡ ለመደምሰስና ፤ በግል ንብረት ፡ የነበሩትን ፡ የባቡር ፡ ሃዲዶችን ፤ ፋብሪካዎችን ፡ መሬትንና ፡ የመሳሰሉትን ፡ ለመላ ፡ ብሄሩ ፤ ለመላ ፡ ኅብረተሰቡ ፡ ለማስተላለፍ ፡ የመላ ፡ ኮሙኖችን ፡ ኃይል ፡ ቢያስተ

ባብሩ ፤ ይህ ፡ ዋህድነት ፡ አይደለምን? ይህ ፡ በጣም ፡ ትክክለኛ ፡ የሆነ ፡ ዴሞክራቲክ ፡ ዋህድነት ፤ እንድያውም ፡ ወዝ ፡ አደራዊ ፡ ዋህድነት ፡ አይደለምን?

የበጐ ፡ ፈቃድ ፡ ዋህድነት ፤ የኮሙኖች ፡ በፈቃድ ፡ በመተባበር ፡ ብሄርን ፡ መመስረት ፤ የወዝ ፡ አደራዊ ፡ ኮሙኖች ፡ ፈቅደው ፡ በመዋህድ ፡ የቡርዥዋ ፡ ገዥነትንና ፡ የቡርዥዋ ፡ የመንግሥት ፡ መኪናን ፡ መሰባበር ፡ የሚቻል ፡ መሆኑን ፡ ለቤርንስተይን ፡ በፍጹም ፡ አይታየውም ። እንደሁሉም ፡ ጮርቃዎች ፡ ቤርንስተይንም ፡ ዋህድነትን ፡ የሚመለከተው ፡ ከላይ ፡ በቢሮክራሲና ፡ በወታደራዊ ፡ ኃይል ፡ ብቻ ፡ ተመርኩዞ ፤ ከላይ ፡ ብቻ ፡ እንደሚጫንና ፡ እንደሚጠበቅ ፡ ነገር ፡ ነው ።

ማርክስ ፡ ርዕዮቶቹን ፡ እንደሚያጣምሙበት ፡ ቀድሞ ፡ የተገነዘበ ፡ ይመስል ፤ በግልፅ ፡ ያረጋገጠው ፤ ኮሙን ፡ ብሄራዊ ፡ አንድነትን ፡ ለማፍረስ ፤ ዋህዳዊ ፡ ሥልጣንን ፡ ለማስወገድ ፡ ፈልጎ ፡ ነበር ፡ የሚለው ፡ ክስ ፤ ሆን ፡ ተብሎ ፤ አውቆ ፡ የተደረገ ፡ ማጭበርበሪያ ፡ መሆኑን ፡ ነው ። ማርክስ ፡ አውቆ ፡ የተጠቀመበት ፡ አረፍተ ፡ ነገር « ብሄራዊ ፡ አንድነትን ፡ ማደራጀት »የሚል ፡ ነው ፤ ይኸውም ፡ ንቁ ፤ ዴሞክራቲክ ፤ ወዝ ፡ አደራዊ ፡ ዋህድነት ፡ በቡርዥዋ ፡ በወታደራዊና ፡ በቢሮክራሲ ፡ ዋህድነት ፡ አንፃር ፡ በማስቀመጥ ፡ ነው ።

ነገር ፡ ግን ... አውቆ ፡ ለመስማት ፡ ያልፈለገ ፡ ከማንኛውም ፡ ጆሮው ፡ ከማይሰማ ፡ ደንቆሮ ፡ የባሰ ፡ ነው ። ስለሆነም ፡ በተለይ ፡ የዛሬው ፡ ዘመን ፡ የሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ አድርባዮች ፡ ሊሰሙት ፡ የማይሹት ፡ ስለመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ መደምሰስና ፡ ስለተባይ ፡ መነቀል ፡ ነው ።

## ፫. የመዥገሩ ፡ መንግሥት ፡ መደምሰስ ።

ይህን ፡ ጥያቄ ፡ የሚመለከቱ ፡ የማርክስ ፡ ቃላት ፡ ጠቅሰን ፡ ነበር ፤ ሆኖም ፡ አሁን ፡ ማሟላት ፡ አለብን ።



«... አዲሱ ፡ በአሮጌውና ፡ እንድያውም ፡ ከበሰበሰው ፡ የኅብረተሰብ ፡ አኗኗር ፡ ጋር ፡ ባለው ፡ አንዳንድ ፡ መመሳሰል ፡ ምክንያት ፡ ማሳሳት ፡ የአዲስ ፡ ታሪካዊ ፡ ጥልቅ ፡ ኪነት ፡ አጋጣሚ ፡ ነው ። ስለሆነም ፡ ዘመናዊው ፡ የመንግሥት ፡ መኪናን ፡ የሰበረው ፡ (bricht — ሰበረ) ይህ ፡ አዲስ ፡ ኮሙንን ፡ የተመለከቱት ፡ እንደ ፡ መካከለኛው ፡ ዘመን ፡ ኮሙን ፡ ትንሳኤ... እንደ ፡ ትናንሽ ፡ መንግሥታት ፡ ፌዴሬሽን (እንደ ፡ ሞንተስክዬ ፤ ዢሮንዲስቶች[19]) እንደ ፡ ከልክ ፡ ካለፈ ፡ ዋህድነት ፡ ጋር ፡ ሲደረግ ፡ የነበረውን ፡ የአረጀ ፡ ትግል ፡ የተጋነነ ቅርፅ ፡ ነበር ።

... ኮሙናዊ ፡ ተቋም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ እየተመገበ ፤ የኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ነፃ ፡ እንቅስቃሴ ፡ ያገደውን ፡ ይህ ፡ መዥገር « መንግሥት » ሲመጠው ፡ የነበረውን ፡ ኃይል ፡ በሙሉ ፡ በኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ አካል ፡ ሊመልስ ፡ ይችል ፡ ነበር ። በዚህ ፡ አንድ ፡ ድርጊት ፡ የፈረንሳይ ፡ ትንሳኤ ፡ ወደፊት ፡ በተራመደ ፡ ነበር ።

... ኮሙናዊ ፡ ተቋም ፡ የገጠር ፡ አምራቾችን ፡ በእያንዳንዱ ፡ አካባቢ ፡ ባሉት ፡ ዋና ፡ ከተማዎች ፡ ህሊናዊ ፡ መሪነት ፡ ስር ፡ በማድረግ ፤ ብሎም ፡ በከተማው ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ አማካኝነት ፡ እውነተኛ ፡ የብሶታቸው ፡ ተቆርቋሪዎችን ፡ ባገኙ ፡ ነበር ። ራሱ ፡ የኮሙን ፡ መኖር ፡ ያስከተለው ፤ ግልፅ ፡ ነው ፤ በየቦታው ፡ ራስን ፡ በራስ ፡ ማስተዳደር ፡ ነው ፤ ይሁን ፡ እንጂ ፡ አሁን ፡ ትርፍ ፡ ነገር ፡ የሆነውን ፤ መንግሥታዊ ፡ ሥልጣንን ፡ በመቃወም ፡ አይደለም ።

« መዥገር » የነበረውን « የመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ መደምሰስ » ፤ የመንግሥት ፡ ሥልጣንን « መመንገል » ፤ « ማፈራረስ » ፤ « የመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ አሁን ፡ ትርፍ ፡







ነገር ፡ ነው » — እነዚህ ፡ ናቸው ፡ ማርክስ ፡ መንግሥትን ፡ በሚመለከት ፡ የፓሪስ ፡ ኮሙንን ፡ ሲመረምርና ፡ ሲተነትን ፡ የተጠቀመባቸው ፡ ሀረጎች ።

ይህ ፡ ሁሉ ፡ የተጻፈው ፡ ከግማሽ ፡ ምእት ፡ ዓመት ፡ በፊት ፡ ነው ፤ አሁን ፡ ግን ፡ ለሰፊው ፡ ሕዝብ ፡ እውቀት ፡ ያልተጣመመውን ፡ ማርክሲዝም ፡ ለመስጠት ፤ እንደ ነበረው ፡ ለማግኘት ፡ መቆፈርን ፡ የሚመስል ፡ ሥራ ፡መሥራት ፡ ሊኖርብን ፡ ነው ። ማርክስ ፡ በሕይወቱ ፡ ሳለ ፡ የተካሄደውን ፡ የመጨረሻ ፡ ታላቅ ፡ አብዮትን ፡ በመመርመር ፡ ያደረጋቸው ፡ መደምደምያዎች ፤ ልክ ፡ የሚቀጥለው ፡ ታላቅ ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ አብዮት ፡ ጊዜ ፡ ሲደርስ ፡ ተረስተዋል ።

> «... በኮሙን ፡ ላይ ፡ የተሰነዘሩት ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ፍቾችና ፤ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ጥቅም ፡ ያላቸው ፡ በኮሙን ፡ ላይ ፡ ማትኮራቸው ፡ የሚያረጋግጠው ፡ ኮሙኑ ፡ በከፍተኛ ፡ ደረጃ ፡ ግትር ፡ ያልሆነ ፡ የፖለቲካ ፡ ቅርፅ ፡ እንደነበር ፡ ነው ፤ ከዚያ ፡ በፊት ፡ የነበሩት ፡ የአገዛዝ ፡ ቅርፆች ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ በመሠረቱ ፡ ጨቋኞች ፡ ነበሩ ። ኮሙኑ ፡ በመሠረቱ ፡ <u>የወዝ ፡ አደር ፡ መደብ ፡ መንግሥት</u> ፡ ነበር ፤ አምራች ፡ መደብ ፡ ከበዝባዥ ፡ መደብ ፡ ጋር ፡ ያደረገው ፡ ትግል ፡ ውጤት ፡ ነበር ፤ ኮሙኑ ፡ የሰው ፡ ጉልበት ፡ የኤኮኖሚ ፡ ነፃነት ፡ ሊጐናፀፍበት ፡ ይችል ፡ የነበረ ፤ ግልፅ ፡ የሆነ ፡ ፖለቲካዊ ፡ ቅርፅ ፡ ነበር ።
>
> ያለዚህ ፡ የመጨረሻ ፡ ሁኔታ ፡ የኮሙኑ ፡ ተቋም ፡ የማይቻልና ፡ ማታለያ ፡ በሆነ ፡ ነበር ... »

ተምኔታውያን ፡ ሥራችን ፡ ብለው ፡ የተሰማሩበት ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ለውጥ ፡ ሊካሄድበት ፡ የሚችል ፡ ፖለቲካዊ ፡ ቅርፅን « ለመፈልሰፍ » ነበር ። ሥርዓተ-አልበኞች ፡ ፖለቲካዊ ፡ ቅርፅ ፡ የሚለውን ፡ ጥያቄ ፡ በጠቅላላው ፡ አይቀበሉትም ፡ ነበር ። የዘመናዊው ፡ ሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ አድርባዮች ፡ የቡርዥዋው ፡ የፖለቲካ ፡ ቅርፅን ፤ ፓርላማዊ ፡ ዴሞክራቲክ ፡ መንግሥትን ፡ መዘለል ፡ እንደሌለበት ፡ ወሰን ፡ ተቀብለውታል ፤ በዚህ « ቅርፅ » ፊት ፡ ሲሰግዱ ፡ ግምባራቸውን ፡ እየፈነካከቱ ። ስለዚህም ፡ ይኸንን ፡ ቅርፅ ፡ <u>ለማፈራረስ</u> ፡ የሚደረገው ፡ ማንኛውም ፡ ሙከራ ፡ ሥርዓተ-አልበኝነት ፡ ነው ፡ ብለው ፡ አውጀዋል ።



ማርክስ ፡ ከጠቅላላው ፡ የሶሺያሊዝም ፡ ታሪክና ፡ ከፖለቲካዊ ፡ ትግል ፡ የደመደመው ፡ መንግሥት ፡ ወደፊት ፡ የሚጠፋ ፡ መሆኑንና ፡ ሲጠፋም ፡ የሽግግር ፡ ቅርፁ (ከመንግሥት ፡ ወደ ፡ መንግሥት ፡ አልባነት) «ወዝ ፡ አደሩ ፡ እንደ ፡ ገዢ ፡ መደብ ፡ መደራጀት » እንዳለበት ፡ ነው ። ይሁን ፡ እንጂ ፤ የዚህ ፡ የወደፊት ፡ ደረጃ ፡ ፖለቲካዊ ፡ <u>ቅርጾችን ፡ ለመፈልሰፍ</u> ፡ ማርክስ ፡ አልቃጣም ። እሱ ፡ ራሱን ፡ የወሰነው ፡ የፈረንሳይን ፡ ታሪክ ፡ በጥንቃቄ ፡ በመመርመርና ፡ በመተንተን ፤ እንደዚሁም ፡ <u>፲፰፻፸፩</u> ዓ. ም. የአመራበትን ፡ መደምደምያ ፡ በመስጠት ፡ ነው ፤ ይኸውም ፡ ነገሩ ፡ የሚያመራው ፡ የቡርዥዋ ፡ የመንግሥት ፡ መኪናን ፡ <u>ለማፈራረስ</u> ፡ መሆኑን ፡ ነው ።

የወዝ ፡ አደሩ ፡ ሰፊ ፡ አብዮታዊ ፡ ንቅናቄ ፡ ሲፈነዳ ፤ ምንም ፡ እንኳ ፡ ይህ ፡ ንቅናቄ ፡ ግቡን ፡ ባይመታም ፤ ምንም ፡ እንኳ ፡ እድሜው ፡ አጭር ፡ ቢሆንና ፡ የማይካድ ፡ ደካማነት ፡ ቢኖረውም ፤ ይህ ፡ ንቅናቄ ፡ ምን ፡ ዓይነት ፡ ቅርጽ ፡ <u>እንደፈለሰፈ</u> ፡ ማርክስ ፡ ማጥናት ፡ ጀመረ ።

ኮሙን — በወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት « በመጨረሻ ፡ የተገለጸ » ፤ የሰው ፡ ጉልበት ፡ የኤኮኖሚ ፡ ነፃነት ፡ ሊቀዳጅበት ፡ የሚችል ፡ ቅርፅ ፡ ነው ።

ኮሙን — የቡርዥዋውን ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ በወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት ፡ <u>ለመሰባበር</u> ፡ የተደረገ ፡ የመጀመሪያ ፡ ሙከራ ፡ ነው ፤ እንደዚሁም « በመጨረሻ ፡ የተፈ





ለሰፊ » የተሰባበረውን ፡ የመንግሥት ፡ መኪናን ፡ ሊተካ ፡ የሚችልና ፡ ያለበትም ፡ የፖለቲካ ፡ ቅርፅ ፡ ነው ።

በሚቀጥለው ፡ የ ፲፱፻፭ ዓ. ም. እና ፡ የ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የሩሲያ ፡ አብዮቶች ፡ በአዲስ ፡ ሁናቴዎችና ፡ በአዲስ ፡ አኳኋኖች ፡ የኮሙኑን ፡ ተግባር ፡ እንዴት ፡ እንደቀጠሉትና ፡ የማርክስን ፡ አስደናቂ ፡ የሆነውን ፡ ታሪካዊ ፡ ትንተና ፡ እንዴት ፡ እንዳረጋገጡ ፡ እንመለከታለን ።

## ምዕራፍ ፡ IV.

## የቀጠለ ። የኤንግልስ ፡ ተጨማሪ ፡ ማብራሪያዎች ።

የኮሙንን ፡ ልምድ ፡ ጠቃሚነትን ፡ በሚመለከተው ፡ በኩል ፡ ማርክስ ፡ መሠረታዊ ፡ የሆኑትን ፡ ነገሮች ፡ ዘርዝሯል ። ኤንግልስም ፡ አሁንም ፤ አሁንም ፡ የማርክስ ፡ ትንተናና ፡ መደምደምያዎችን ፡ እያብራራ ፡ ይህንን ፡ አርእስት ፡ ደጋግሞ ፡ አንስቷል ። አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ከታላቅ ፡ ኃይልና ፡ ጉልህነት ፡ ጋር ፡ የጥያቄውን ፡ ሌሎች ፡ ዝርዝሮች ፡ አብራርቷል ፤ ስለዚህም ፡ እነዚህ ፡ ማብራሪያዎችን ፡ በቅርብ ፡ መመልከት ፡ ያስፈልጋል ።

### ፩ «የመኖሪያ ፡ ቤት ፡ ጥያቄ ። »

የመኖሪያ ፡ ቤትን ፡ ጥያቄ (፲፰፻፸፪ ዓ. ም.)[20] በሚመለከተው ፡ ሥራው ፡ ኤንግልስ ፡ የኮሙንን ፡ ልምድ ፡ በመገንዘብ ፤ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ደጋግሞ ፡ መንግሥትን ፡ በሚመለከት ፡ የአብዮት ፡ ተግባሮችን ፡ ገልጿል ። ልናጤነው ፡ የሚገባ ፡ ነገር ፡ ቢኖር ፤ በተጨበጠ ፡ አርእስት ፡ በግልፅ ፡ የሚታዩት ፤ በአንድ ፡ በኩል ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ መንግሥት ፡ ከአሁነኛው ፡ መንግሥት ፡ ጋር ፡ ያላቸው ፡ ተመሳሳይ ፡



ባህርያት ፡ በሁለቱም ፡ ሁኔታዎች ፡ ስለመንግሥት ፡ እንድንናገር ፡ መሠረት ፡ የሚሰጡን ፡ ባህርያት ፡ ሲሆኑ ፤ በሌላ ፡ በኩል ፡ ደግሞ ፡ የልዩነታቸው ፡ ባህርያት ፡ ወይንም ፡ የመንግሥት ፡ ወደ ፡ መደምሰስ ፡ ሽግግር ፡ ነው ።

«የመኖሪያ ፡ ቤት ፡ ጥያቄ ፡ የሚፈታው ፡ እንዴት ፡ ነው? በዘመናዊው ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ውስጥ ፡ ይህ ፡ ጥያቄ ፡ የሚፈታው ፡ ልክ ፡ እንደማንኛውም ፡ ሌላ ፡ የኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ጥያቄ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ በጥያቄና ፡ በማቅረብ ፡ በሚደረገው ፡ የደረጃ ፡ በደረጃ ፡ የኤኮኖሚ ፡ መስተካከል ፡ ነው ፤ ይሁንና ፡ ይህ ፡ መፍትሄ ፡ አሁንም ፡ አሁንም ፡ ጥያቄው ፡ ራሱ ፡ እንደገና ፡ እንዲነሳ ፡ ያደርጋል ፤ ስለዚህም ፡ ምንም ፡ መፍትሄ ፡ አይሰጥም ። የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ አብዮት ፡ ይህን ፡ ጥያቄ ፡ እንዴት ፡ እንደሚፈታው ፡ የሚመሰረተው ፡ በጊዜና ፡ ቦታ ፡ አኳኋን ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ ጥያቄው ፡ የተያያዘው ፡ ይበልጥ ፡ ላቅ ፡ ካሉ ፡ ጥያቄዎች ፡ ጋር ፡ ነው ፤ ከነዚህም ፡ ዋና ፡ መሠረታዊ ፡ ከሆኑት ፡ አንዱ ፡ በከተማና ፡ በገጠር ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ ተቃራኒ ፡ ሁኔታ ፡ መወገድ ፡ ነው ። የወደፊቱን ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ለማደራጀት ፡ ተምኔታዊ ፡ ሥርዓትን ፡ መፍጠር ፡ የኛ ፡ ተግባር ፡ ስላልሆነ ፤ ይህን ፡ ጥያቄ ፡ ከዚህ ፡ በበለጠ ፡ ጠልቆ ፡ ለማየት ፡መሞከር ፡ ትርፍ ፡ ነገር ፡ ይሆናል ። ይሁን ፡ እንጂ ፡ አንድ ፡ የማያጠራጥር ፡ ነገር ፡ አለ ፤ ይኸውም ፡ በትክክል ፡ ከተጠቀሙበት ፡ እውነተኛ ፡ የመኖሪያ ፡ ቤት ፡ እጥረትን ፡ በሙሉ ፡ ለማስወገድ ፡ የሚያስችል ፡ በትልልቅ ፡ ከተማዎች ፡ ውስጥ ፡ በቂ ፡ የመኖሪያ ፡ ቤቶች ፡ ብዛት ፡ አለ ። እርግጥ ፡ ነው ፤ ይህ ፡ ሊሆን ፡ የሚችለው ፡ ከዛሬው ፡ ባለቤቶቹ ፡ ቤቶችን ፡ በመውረስና ፡ በነዚህ ፡ ቤቶች ፡ ውስጥ ፡ ቤት ፡ የሌላቸውን ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፤ ወይም ፡ በዛሬው ፡ ቤታቸው ፡ ተጣ







በው ፡ የሚኖሩትን ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ በማዛወር ፡ ብቻ ፡ ነው ። ወዝ ፡ አደሩም ፡ ወዲያውኑ ፡ የፖለቲካ ፡ ሥልጣኑን ፡ እንደጨበጠ ፤ ያሁኑ ፡ መንግሥት ፡ የመኖሪያ ፡ ቤት ፡ ጉዳይና ፡ ተመሳሳይ ፡ ወረሳዎች ፡ በቀላሉ ፡ እንደሚያደርገው ፡ ሁሉ ፤ በኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ጥቅም ፡ ፍላጎት ፡ የተመረኮዘ ፡ ተመሳሳይ ፡ እርምጃ ፡ ለመውሰድ ፡ ቀላል ፡ ይሆንለታል » (የጀርመን ፡ እትም ፤ ፲፰፻፹፯ ዓ. ም. ፤ ገጽ ፡ ፳፪)

እዚህ ፡ ላይ ፡ የመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ ቅርፅ ፡ መለወጡ ፡ አልተነሳም ፤ የተግባሩ ፡ ይዘት ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ። መውረስና ፡ ቤትን ፡ መውሰድ ፡ በአሁኑ ፡ መንግሥት ፡ ትእዛዝም ፡ ይከናወናሉ ። የወዝ ፡ አደሩ ፡ መንግሥት ፡ ቢሆን፤ የጉዳዩ ፡ ፎርማል ፡ ጐን ፡ ሲታይ ፤ መኖሪያ ፡ ቤቶች ፡ እንዲወሰዱና ፡ ህንፃዎችም ፡ እንዲወረሱ « ትእዛዝ » ያስተላልፋል ። ይሁን ፡ እንጂ ፡ ከቡርዥዋው ፡ ጋር ፡ የተሳሰረው ፡ አሮጌው ፡ የሥራ ፡ አስፈጻሚ ፡ አውታር ፤ ቢሮክራሲው ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ መንግሥት ፡ ትእዛዞችን ፡ በሥራ ፡ ላይ ፡ ለማዋል ፡ እንደማይችል ፡ ግልፅ ፡ ነው ።

« ... እዚህ ፡ ላይ ፡ መጠቀስ ፡ ያለበት ፤ መላ ፡ የሥራ ፡ መሣሪያዎችን ፡ መያዝ ፤ ጠቅላላውን ፡ ኢንዱስትሪ ፡ በሠርቶ ፡ አደር ፡ ሕዝብ ፡ እጅ ፡ ማስገባት ፤ ፕሩዶናዊ « የመግዛት »ከሚለው ፡ ተግባር ፡ ቀጥታ ፡ ተቃራኒ ፡ መሆኑን ፡ ነው ። በዚህ ፡ በሁለተኛው ፡ ዓይነቱ ፡ ሁኔታ ፡ እያንዳንዱ ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ የመኖሪያ ፡ ቤቱ ፤ የእርሻ ፡ መሬት ፤ የሥራ ፡ መሣሪያዎች ፡ ባለቤት ፡ ይሆናል ። በመጀመሪያው ፡ ዓይነት ፡ ሁኔታ ፡ ግን « ሠርቶ ፡ አደሩ ፡ ሕዝብ » የህንፃዎች ፥ የፋብሪካዎችና ፡ የሥራ ፡ መሣሪያዎች ፡ ጠቅላላ ፡ ባለቤት ፡ ይሆናል ። ቢያንስ ፡ በሽግግሩ ፡ ጊዜ ፡ ግለሰቦች ፡ ወይም ፡ ማኅበራት ፡ የተወሰነ ፡ ክፍያ ፡ ሳያደርጉ ፡ በእነዚህ ፡



ህንፃዎች ፤ ፋብሪካዎችና ፡ ሌሎችም ፡ ለመጠቀም ፡ እንደሚችሉ ፡ ያጠራጥራል ። በዚህም ፡ ምክንያት ፡ የመሬት ፡ የግል ፡ ንብረትን ፡ መደምሰስ ፤ የመሬት ፡ ግብር ፡ መደምሰስ ፡ ማለት ፡ አይደለም ፤ በልዩ ፡ መንገድ ፡ ቢሆንም ፤ ወደ ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ንብረትነት ፡ መስጠት ፡ ይታሰባል ። ስለሆነም ፡ የመላው ፡ የሥራ ፡ መሣሪያዎች ፡ በሠርቶ ፡ አደሩ ፡ ሕዝብ ፡ እጅ ፡ መግባት ፤የመከራየትንና ፡ የማከራየትን ፡ ግንኙነቶች ፡ አያግድም » (ገጽ ፡ ፳፰)

በዚህ ፡ ትንትና ፡ ውስጥ ፡ የተነሳው ፡ ጥያቄ ፤ ይኸውም ፡ ስለ ፡ መንግሥት ፡ መክሰም ፡ የኤኮኖሚ ፡ መሠረቶች ፤ በሚቀጥለው ፡ ምዕራፍ ፡ እንመለስበታለን ። ኤንግልስ ፡ በጣም ፡ ተጠንቅቆ ፡ ሲገልፅ ፤ « ቢያንስ ፡ በሽግግሩ ፡ ጊዜ » የወዝ ፡ አደሩ ፡ መንግሥት ፡ የመኖሪያ ፡ ቤቶችን ፡ ያለ ፡ ክፍያ ፡ እንዲጠቀሙባቸው ፡ ለመፍቀድ « አስቸጋሪ » ይሆናል ፡ ይላል ። የመላ ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ንብረት ፡ የሆኑትን ፡ ቤቶች ፡ ቤተ ፡ ሰቦች ፡ በሚከራዩበት ፡ ጊዜ ፡ ኪራይ ፡ መከፈል ፡ አለበት ፤ የተወሰነ ፡ ቁጥጥርና ፡ ቤቶችን ፡ ለማደላደል ፡ የተወሰነ ፡ ቅደም ፡ ተከተል ፡ መኖር ፡ አለበት ። ይህ ፡ ሁሉ ፡ የተወሰነ ፡ የመንግሥትን ፡ ቅርፅ ፡ ይጠይቃል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ለዚህ ፡ ልዩ ፡ መብት ፡ ያለውን ፡ ቦታ ፡ የያዙ ፡ ባለሥልጣኖች ፡ ያሉበት ፡ ልዩ ፡ ወታደራዊና ፡ ቢሮክራሲያዊ ፡ አውታር ፡ በፍፁም ፡ አያስፈልገውም ። ቤቶች ፡ ከኪራይ ፡ ነፃ ፡ ሆነው ፡ ሊሰጡ ፡ ወደሚቻልበት ፡ ሁኔታ ፡ ለመሸጋገር ፡ የመንግሥት ፡ ፍፁም « መክሰምን » ይጠይቃል ።

ከኮሙን ፡ በኋላና ፡ በኮሙን ፡ ልምድ ፡ ተፅእኖ ፡ ምክንያት ፡ ብላንኪስቶች[21] ፡ ወደ ፡ ማርክሲዝም ፡ መሠረተ ፡ ሃሳብ ፡ አቋም ፡ ስለመሸጋገራቸው ፡ ሲናገር ፤ ኤንግልስ ፡ እግረ ፡ መንገዱን ፡ ይህን ፡ አቋም ፡ እንደሚከተለው ፡ ያብራራል ፤






« … የወዝ ፡ አደሩና ፡ የበላይ ፡ ገዥነቱ ፡ የፖለቲካ ፡ እርምጃ ፡ መደቦቹና ፡ ከነሱ ፡ ጋር ፡ አብሮም ፡ መንግሥት ፡ እንዲጠፉ ፡ እንደመሸጋገሪያ ፡ ያስፈልጋል … » (ገጽ ፡ ፶፫)

የፀጉር ፡ ፈለጣ ፡ ሒስ ፡ ሱሰኞች ፤ ወይም ፡ የቡርዥዋ « ማርክሲዝምን ፡ ደምሳሾች » በዚህ « የመንግሥት ፡ መደምሰስ » መቀበልንና ፤ ከላይ ፡ በ « አንቲ ፡ ዱሪንግ » እንደተጠቀሰው ፤ ይህን ፡ የሥርዓተ-አልበኞችን ፡ አስተያየት ፡ በመቃወም ፡ መካከል ፡ ምናልባት ፡ ቅራኔ ፡ ያለ ፡ ሊመስላቸው ፡ ይችላል ። አድርባዮች ፡ ኤንግልስንም ፡ ጭምር ፡ እንደ « ሥርዓተ-አልበኛ » ቢቆጥሩ ፡ አያስገርምም ፤ ምክንያቱም ፡ አሁን ፡ በሶሺያል-ሾቪኒስቶች ፡ ዘንድ ፡ በጣም ፡ በመስፋፋት ፡ ያለው ፡ ኢንተርናሽናሊስቶችን ፡ በሥርዓተ-አልበኝነት ፡ መክሰስ ፡ ነውና ።

ማርክሲዝም ፡ ሁልጊዜ ፡ ያስተማረው ፡ ከመደቦች ፡ መጥፋት ፡ ጋር ፡ መንግሥትም ፡ ጭምር ፡ አብሮ ፡ እንደሚጠፉ ፡ ነው ። « በአንቲ ፡ ዱሪንግ » ውስጥ ፡ ያለው « የመንግሥት ፡ መክሰም » የሚለው ፡ የታወቀ ፡ ክፍል ፡ ሥርዓተ-አልበኞችን ፡ የሚወነጅለው ፡ የመንግሥት ፡ መደምሰስን ፡ በመደገፋቸው ፡ ሳይሆን ፤ መንግሥት « በአንድ ፡ ሌሊት » ለመደምሰስ ፡ ይቻላል ፡ ብለው ፡ በመስበካቸው ፡ ነው ፡ እንጂ ።

አሁን ፡ ያንሰራራው « የሶሺያል-ዴሞክራሲ » መሠረተ ፡ ሐሳብ ፡ ማርክሲዝም ፡ የመንግሥትን ፡ መደምሰስ ፡ ጥያቄ ፡ በሚመለከተው ፡ በሥርዓተ-አልበኝነት ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ አስተያየት ፡ እንዴት ፡ እንዳጣመመው ፡ ለመመልከት ፤ ማርክስና ፡ ኤንግልስ ፡ ከሥርዓተ-አልበኝነት ፡ ጋር ፡ ያደረጉትን ፡ አንድ ፡ ክርክር ፡ ማስታወሱ ፡ በጣም ፡ ጠቃሚ ፡ ነው ።



## ፪. ከሥርዓተ ፡ አልበኞች ፡ ጋር ፡ ክርክር ።

ይህ ፡ ክርክር ፡ የተካሄደው ፡ በ ፲፰፻፸፫ ዓ. ም. ነው ። ማርክስና ፡ ኤንግልስ ፡ ፕሩዶናውያንን[22] ፤ « አውቶኖሚያንን » ወይንም « ፀረ-አውቶሪታርያኖችን » በመቃወም ፡ ወደ ፡ ኢጣልያው ፡ ሶሺያሊስት ፡ አመታዊ ፡ መጽሔት ፡ ጽሑፎች ፡ ልከዋል ፤ እነዚህ ፡ ጽሑፎች ፡ በጀርመንኛ « በNeue Zeit» »[23] ብቅ ፡ ያሉት ፡ በ፲፱፻፲፫ ዓ. ም. ብቻ ፡ ነው ።

« … የወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ የፖለቲካ ፡ ትግል ፡ አብዮታዊ ፡ ቅርፅ ፡ ከያዘ » ብሎ ፡ ይጽፋል ፡ ማርክስ ፡ ፖለቲካን ፡ በመቃወማቸው ፡ በሥርዓተ-አልበኞች ፡ ላይ ፡ ሲያፌዝ ፤ « ወዝ ፡ አደሮች ፡ በቡርዥዋ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ ቦታ ፡ የራሳቸውን ፡ አብዮታዊ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ ካቋቋሙ ፤ መርሆችን ፡ በመጣሳቸው ፡ ከፍተኛ ፡ ወንጀል ፡ ይፈጽማሉ ፤ ምክንያቱም ፡ የራሳቸውን ፡ ግርድፍ ፡ የቀን ፡ ቀን ፡ ፍላጎታቸውን ፡ ለማርካትና ፡ የቡርዥዋውን ፡ ተቃውሞ ፡ ለማጥፋት ፡ መሣርያቸውን ፡ ጥለው ፤ እጃቸውን ፡ አጣምረው ፡ በመቀመጥና ፡ መንግሥቱን ፡ በማስወገድ ፡ ፈንታ ፤ ወዝ ፡ አደሮች ፡ ለመንግሥቱ ፡ አብዮታዊና ፡ ሽግግራዊ ፡ ቅርፅን ፡ ይሰጡታል ።» («Neue Zeit ፤ ፲፱፻፲፫-፲፱፻፲፬ ዓ. ም. ፤ ፴፪ ፤ ቅፅ ፡ ፩ ፤ ገጽ ፡ ፵)[24]

የዚህ ፡ ዓይነት ፡ የመንግሥት « መወገድን » ብቻ ፡ ነው ፡ ማርክስ ፡ ሥርዓተ ፡ አልበኞችን ፡ በመቃወም ፡ የተዋጋው! መደቦች ፡ ሲጠፉ ፡ መንግሥትም ፡ እንደሚጠፋ ፤ ወይም ፡ መደቦች ፡ ሲደመሰሱ ፡ መንግሥትም ፡ የሚደመሰስ ፡ መሆኑን ፡ ማርክስ ፡ ምንግዜም ፡ አልተቃወመም ። ማርክስ ፡ የተቃወመው ፤ ወዝ ፡ አደሮች ፡ መሣሪያ ፡ ከመጠቀም ፤ ከተደራጀ ፡ አመፅ ፤ ማለትም « የቡርዥዋውን ፡ ተቃ





ውሞ ፡ ለመደምሰስ » የሚያስፈልገውን ፡ መንግሥት ፡
መተው ፡ አለባቸው ፡ የሚለውን ፡ ነው ።

ከሥርዓተ-አልበኝነት ፡ ጋር ፡ የሚደረገው ፡ ትግል ፡
እውነተኛ ፡ ትርጉም ፡ እንዳያጣምሙበት ፡ ለመከላከል ፤
ማርክስ ፡ አውቆ ፡ ለወዝ ፡ አደሩ ፡ የሚያስፈልገውን ፡
መንግሥት « አብዮታዊና ፡ ሽግግራዊ ፡ ቅርፅን » በትክ
ክል ፡ ጠቁሟል ። ለወዝ ፡ አደሩ ፡ መንግሥት ፡ የሚያስፈል
ገው ፡ ለጊዜው ፡ ብቻ ፡ ነው ። እኛ ፡ እንደ ፡ ዓላማ ፡ አድር
ገን ፡ መንግሥት ፡ መደምሰስ ፡ አለበት ፡ በሚለው ፡ ጥያቄ ፡
ላይ ፡ ከሥርዓተ-አልበኞች ፡ ጋር ፡ በጠቅላላው ፡ አንለያይም ።
እኛ ፡ የምንለው ፡ ይህ ፡ ዓላማ ፡ ግቡን ፡ እንዲመታ ፡ ለ
ጊዜው ፡ መሳሪያዎችን ፤ ቀሳቁሶችንና ፡ የመንግሥት ፡ ሥል
ጣን ፡ እርምጃዎችን ፡ በበዝባዦች ፡ ላይ ፡ መጠቀም ፡ አለ
ብን ፤ ይሽውም ፤ ልክ ፡ መደቦችን ፡ ለመደምሰስ ፡ የጭ
ቁኑ ፡ መደብ ፡ ጊዜያዊ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ እንደሚያስ
ፈልገው ፡ ሁሉ ፡ ነው ። ማርክስ ፡ በሥርዓተ-አልበኞች ፡
ላይ ፡ ጉዳዩን ፡ ሲያስቀምጥ ፡ የመረጠው ፡ በጣም ፡ የከረረ
ና ፡ በጣም ፡ ግልፅ ፡ የሆነ ፡ መንገድ ፡ ነው ፤ የካፒታሊስ
ቶችን ፡ ቀንበር ፡ ፈንግለው ፡ ወዝ ፡ አደሮች « መሳሪያቸው
ን ፡ ማስቀመጥ » አለባቸው ፡ ወይስ ፡ የካፒታሊስቶችን ፡
ተቃውሞ ፡ ለመደምሰስ ፡ በነሱ ፡ ላይ ፡ መጠቀም ፡ አለባቸ
ው? ይሁንና ፡ አንድ ፡ መደብ ፡ በሌላው ፡ ላይ ፡ የሚያደ
ርገው ፡ ቅደም ፡ ተከተሉን ፡ የያዘ ፡ የመሳሪያዎችን ፡ መጠቀ
ም ፡ የመንግሥት « ሽግግራዊ ፡ ቅርፅ » ካልሆነ ፡ ሌላ ፡
ምን ፡ ሊሆን ፡ ይችላል?

እስቲ ፡ እያንዳንዱ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራት ፡ ራሱን ፡ ይጠ
ይቅ ፤—ከሥርዓተ-አልበኞች ፡ ጋር ፡ ስለመንግሥት ፡
ሲከራከር ፡ እንዲህ ፡ ነበር ፡ ወይ ፡ ጥያቄ ፡ ያቀረበው?
የሁለተኛ ፡ ኢንተርናሽናል ፡ አብዛኛው ፡ የህጋዊ ፡ ሶሺ
ያሊስት ፡ ፓርቲዎች ፡ ጥያቄን ፡ ያቀረቡት ፡ እንዲህ ፡ ነበር ፡
ወይ?



ኤንግልስም ፡ እነዚህን ፡ ሃሳቦች ፡ በጣም ፡ ሰፋ ፡ አድር
ጎና ፡ ይበልጥ ፡ ግልጽ ፡ በሆነ ፡ አኳኋን ፡ ያስፋፋቸዋል ።
በመጀመሪያ ፡ ራሳቸውን « ፀረ-አውቶሪታሪያኖች » ብለው ፡
በሚጠሩት ፡ በፕሩዶናውያን ፡ ዝብርቅርቅ ፡ ሃሳቦች ፡ ማለት
ም ፡ ማንኛውም ፡ ሥልጣን ፤ ማንኛውም ፡ ታዛዥነት ፤
ማንኛውም ፡ ኃይል ፡በሚቃወሙት ፡ ላይ ፡ ያፌዝባቸዋል ።
ለመሆኑ ፡ ፋብሪካን ፤ የባቡር ፡ ሃዲድን ፤ በሰፊ ፡ ባህር ፡
ውስጥ ፡ የሚንሳፈፈውን ፡ መርከብ ፡ ብንወስድ ፤ ይላል ፡
ኤንግልስ ፤ ለመሆኑ ፡ በመኪናዎችና ፡ በተቀነባበረ ፡ የብዙ ፡
ሰዎች ፡ ትብብር ፡ ከተመሠረቱት ፡ ከፍተኛ ፡ ቴክኒካዊ ፡
ተቀዋሞች ፡ አንዱ ፡ እንኳ ፡ ቢሆን ፡ ያለ ፡ ታዛዥነት ፡ ወይ
ም ፡ ያለ ፡ ሥልጣንና ፡ ኃይል ፡ ሊሠራ ፡ እንደማይችል ፡
ግልፅ ፡ አይደለምን?

« ... በጣም ፡ የተደናበሩት ፡ ፀረ ፡ አውቶሪታሪ
ያኖችን ፡ በዚህ ፡ ትችት ፡ በምቃወምበት ፡ ጊዜ ፡ እነ
ሱ ፡ ሊሰጡኝ ፡ የሚችሉት ፡ መልስ ፡ ቢኖር ፡ የሚከተ
ለውን ፡ ብቻ ፡ ነው « አዎ! ይህ ፡ እውነት ፡ ነው ፤
ነገር ፡ ግን ፡ እዚህ ፡ ጉዳዩ ፡ ወኪሎቻችን ፡ ስለምንል
ክበት ፡ ስለ ፡ አውቶሪቲ ፡ ጥያቄ ፡ አይደለም ፤ ስለ ፡
ትእዛዝ ፡ ነው ፡ እንጂ !» እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ የሚያስቡት ፡
የአንድን ፡ ነገር ፡ ስሙን ፡ ብቻ ፡ በመለወጥ ፡ ነገሩን ፡
የሚለውጡ ፡ ይመስላቸዋል ... »[25]

አውቶሪቲና ፡ አውቶኖሚ ፡ የሚለዋወጡ ፡ ነገሮች ፡
መሆናቸውን ፤ የምንጠቀምባቸው ፡ መስክ ፡ ከልዩ ፡ ልዩ ፡
የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ እድገት ፡ ደረጃዎች ፡ ጋር ፡ የሚለዋወጥ ፡
መሆኑን ፤ እነዚህንም ፡ እንደ ፡ ፍጹም ፡ ነገር ፡ መውሰድ ፡
ስህተት ፡ መሆኑን ፡ አሳይቶ ፤ እንደዚሁም ፡ መኪናንና
ከፍተኛ ፡ ምርትን ፡ የምንጠቀምበት ፡ መስክ ፡ ከቀን ፡
ቀን ፡ በመስፋፋት ፡ ላይ ፡ መሆኑን ፡ በመጨመር ፤ ኤንግ





ልስ ፡ በአጠቃላይ ፡ ከአውቶሪቲ ፡ ውይይት ፡ ወደ ፡ መን
ግሥት ፡ ጥያቄ ፡ ያልፋል ።

« … አውቶኖሚስቶች » ብሎ ፡ ይጽፋል ፡ ኤንግ
ልስ « የወደፊቱ ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ድርጅት ፡ አውቶ
ሪቲን ፡ የሚፈቅደው ፡ የምርት ፡ ሁኔታዎች ፡ ስለሚ
ያስገድዱት ፡ በዚሁ ፡ አካባቢ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ ቢሉ ፡
ኖሮ ፡ ከነሱ ፡ ጋር ፡ ቋንቋ ፡ በተገኘ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡
እነሱ ፡ አውቶሪቲን ፡ አስፈላጊ ፡ የሚያደርጉትን ፡ ሁኔ
ታዎች ፡ በሙሉ ፡ ለማየት ፡ አይችሉምና ፡ ከቃሉ ፡ ጋር ፡
በጋለ ፡ ስሜት ፡ ይታገላሉ ።

ለምንድነው ፡ ፀረ-አውቶሪታሪያኖች ፡ የፖለቲካ ፡
አውቶሪቲን ፤ መንግሥትን ፡ በመቃወም ፡ በመጮህ ፡
ብቻ ፡ የማይወሰኑት? ሁሉም ፡ ሶሺያሊስቶች ፡ መንግ
ሥትና ፤ ከሱ ፡ ጋር ፡ አብሮም ፡ የፖለቲካ ፡ አውቶሪቲ ፡
በመጪው ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ አብዮት ፡ ምክንያት ፡ እንደ
ሚጠፉ ፡ ይስማማሉ ፤ ማለትም ፡ ማኅበራዊ ፡ ተግባሮ
ች ፡ ፖለቲካዊ ፡ ባህሪያቸውን ፡ ያጣሉ ፤ እና ፡ የኅብ
ረተ ፡ ሰቡን ፡ ጥቅም ፡ የሚጠብቁ ፡ ያስተዳደር ፡ ተግባ
ሮችን ፡ ብቻ ፡ ያከናውናሉ ። ነገር ፡ ግን ፡ ፀረ ፡ አውቶ
ሪታሪያኖች ፡ ፖለቲካዊ ፡ መንግሥት ፡ የፈጠራቸው ፡
የኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ግንኙነቶች ፡ ገና ፡ ከመፍረሳቸው ፡ በፊ
ት ፡ ፖለቲካዊ ፡ መንግሥት ፡ በአንድ ፡ ምት ፡ እንዲደ
መሰስ ፡ ይጠይቃሉ ። የኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ አብዮት ፡ የመጀ
መሪያ ፡ ተግባር ፡ አውቶሪቲን ፡ ማስወገድ ፡ መሆን ፡
አለበት ፡ ይላሉ ።

ለመሆኑ ፡ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ አብዮት ፡ አይተው ፡
ያውቃሉን? አብዮት ፡ ከተባለ ፡ ያለ ፡ ጥርጥር ፡ ከፍ
ተኛ ፡ የአውቶሪቲ ፡ ነገር ፡ ነው ። አብዮት ፡ የምልአተ ፡
ሕዝቡ ፡ አንድ ፡ ክፍል ፡ ከፍተኛ ፡ የአውቶሪቲ ፡ መሳሪያ
ዎችን ፤ ጠብመንጃን ፤ ሳንጃንና ፡ መድፍን ፡ በመጠ



ቀም ፡ የራሱን ፡ ፍላጎት ፡ በሌላው ፡ ክፍል ፡ ላይ ፡
የሚጭንበት ፡ ድርጊት ፡ ነው ። ስለሆነም ፡ ድል ፡
የመታው ፡ ፓርቲ ፡ ገዥነቱን ፡ የሚያስጠብቀው ፡
ባለው ፡ መሳሪያ ፡ አማካኝነት ፡ በአድሃሪዎች ፡ ላይ
በሚፈጥረው ፡ ፍርሃት ፡ ነው ። የፓሪስ ፡ ኮሙን ፡
የታጠቀ ፡ ሕዝብ ፡ በቡርዥዋው ፡ ላይ ፡ አውቶሪቲውን
ባይጠቀም ፡ ኖሮ ፡ ከአንድ ፡ ቀን ፡የበለጠ ፡ ሊቆይ ፡
ይችል ፡ ነበርን? እንድያውም ፡ በተቃራኒው ፡ ኮሙኑ ፡
በዚህ ፡ አውቶሪቲው ፡ በደምብ ፡ ባለመጠቀሙ ፡ መ
ውቀስ ፡ አይገባምን? ስለዚህም ፤ ከሁለቱ ፡ አንዱ ።
ወይንም ፡ ፀረ-አውቶሪታሪያኖች ፡ የሚናገሩትን ፡ አያው
ቁም ፤ በዚህ ፡ ሁኔታ ፡ ውዥንብር ፡ ይነዛሉ ። ወይንም ፡
ያውቃሉ ፤ በዚህም ፡ ሁኔታ ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ ጉዳይ ፡
ይክዳሉ ። በዚህም ፡ ሆነ ፡ በዛ ፡ የሚጠቅሙት ፡ አድ
ሃሪያንን ፡ ነው » (ገጽ ፡ ፴፱)[26]

በዚህ ፡ አስተያየት ፡ የተነሱት ፡ ጥያቄዎች ፡ መንግሥት ፡
በሚከስምበት ፡ ጊዜ ፡ በፖለቲካና ፡ በኤኮኖሚ ፡ መካከል ፡
ባለው ፡ ግንኙነት ፡ አንፃር ፡ መመርመር ፡ አለባቸው ።
(ስለመንግሥት ፡ መክሰም ፡ በሚቀጥለው ፡ ምዕራፍ ፡ እን
መለስበታለን ። የማኅበራዊ ፡ ተግባሮች ፡ ከፖለቲካ ፡ ወደ ፡
ግልጽ ፡ የአስተዳደር ፡ ተግባሮች ፡ መለወጥና « ፖለቲካዊ ፡
መንግሥት » ጥያቄዎች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ። ይህ ፡ የመጨ
ረሻው ፡ ቃል (« ፖለቲካዊ ፡ መንግሥት » — ተርጓሚው)
በተለይ ፡ አለመግባባት ፡ ሊፈጥር ፡ ይችላል ፤ የሚያመለ
ክተው ፡ የመንግሥት ፡ መክሰም ፡ ሂደትን ፡ ነው ፤ ሂደቱ ፡
የተወሰነ ፡ ደረጃ ፡ በሚደርስበት ፡ ጊዜ ፡ በመክሰም ፡ ላይ ፡
ያለ ፡ መንግሥት ፡ ፖለቲካዊ ፡ ያልሆነ ፡ መንግሥት ፡ ተብሎ ፡
ሊጠራ ፡ ይቻላል ።

በዚህ ፡ የኤንግልስ ፡ ክርክር ፡ በጣም ፡ ግሩሙ ፡ ነገር ፤
አሁንም ፡ በሥርዓተ-አልበኞች ፡ ላይ ፡ ጉዳዩን ፡ እንዴት ፡





እንደሚያቀርበው ፡ ነው ። የኤንግልስ ፡ ደቀ ፡ መዝሙሮች ፡ ለመሆን ፡ የሚሹት ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ በዚህ ፡ ጉዳይ ፡ ላይ ፡ ከ ፲፰፻፸፫ ዓ. ም. ጀምረው ፡ ከሥርዓተ-አልበኞች ፡ ጋር ፡ ሚሊዮን ፡ ጊዜ ፡ ተከራክረዋል ፤ ቢሆንም ፡ የተከራከሩት፡ማርክሲስቶች ፡ መከራከር ፡ እንደሚገባቸውና ፡ እንዳለባቸው ፡ ሆነው ፡ አይደለም ። ሥርዓተ-አልበኞች ፡ ስለመንግሥት ፡ መደምሰስ ፡ ያላቸው ፡ ሃሳብ ፡ የተምታታና ፡ ፀረ-አብዮታዊ ፡ ነው — ብሎ ፡ ነው ፡ ኤንግልስ ፡ ይህን ፡ ጥያቄ ፡ ያቀረበው ። ሥርዓተ-አልበኞች ፡ ለማየት ፡ የማይሹት ፡ በተለይ ፡ የአብዮት ፡ አነሳሱንና ፡ እድገቱን ፡ ሲሆን ፡ ከዚሁም ፡ ጋር ፡ አብሮ ፡ አመፅን ፤ አውቶሪቲን ፤ ሥልጣንን ፤ መንግሥትን ፡ በሚመለከት ፡ የተወሰኑ ፡ ተግባሮቹን ፡ ጭምር ፡ ነው ።

የተለመደው ፡ የዛሬዎቹ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ በሥርዓተ-አልበኞች ፡ ላይ ፡ የሚያደርጉት ፡ ሂስ ፡ ወደማይረባ ፡ የጮርቃ ፡ ወራዳነት ፡ አዘቅዝቋል « እኛ ፡ መንግሥትን ፡ እናውቃለን ፤ ሥርዓተ ፡ አልበኞች ፡ ግን ፡ አያውቁም!» እርግጥ ፡ ነው ፤ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ወራዳነት ፡ በሚያስቡና ፡ በአብዮተኛ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ ዘንድ ፡ ጥላቻን ፡ ሳይፈጥር ፡ አልቀረም ። ኤንግልስ ፡ የሚለው ፡ ሌላ ፡ ነው ፤ እሱ ፡ የሚያስገነዝበው ፤ ሶሺያሊስቶች ፡ በሙሉ ፡ የሚቀበሉት ፤ መንግሥት ፡ የሚጠፋው ፡ ከሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ ቀጥሎ ፡ እንደ ፡ ውጤት ፡ መሆኑን ፡ ነው ። ቀጥሎም ፡ በተለይ ፡ የሚያተኩረው ፡ በአብዮት ፡ ጥያቄ ፡ ላይ ፡ ነው ። ይህንን ፡ ጥያቄ ፡ ነው ፡ ብዙውን ፡ ጊዜ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች፡ በአድርባይነት ፡ የሚያልፉትና ፡ እንድያውም ፡ ሥርዓተ-አልበኞች « እንዲመረምሩት » የሚተውት ። ይህንን ፡ ጥያቄ ፡ በሚያነሳበት ፡ ጊዜ ፡ ኤንግልስ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ይጠይቃል ። ኮሙኑ ፡ በአብዮታዊው ፡ የመንግሥት ፡ ሥልጣኑ ፤ ማለትም ፡ እንደ ፡ ገዢ ፡ መደብ ፡ በታጠቀውና ፡



በተደራጀው ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ይበልጥ ፡ መጠቀም ፡ አልነበረበትምን?

ያንሠራራው ፡ ሕጋዊው ፡ ሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ በአብዮት ፡ ውስጥ ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ ለተጨበጡ ፡ ተግባሮች ፡ ጥያቄ ፡ ብዙውን ፡ ጊዜ ፡ የሚያልፈው ፤ ወይ ፡ እንድያው ፡ በጮርቃ ፡ ፌዝ ፡ ነው ፤ ወይ ፡ ሻል ፡ ባለው ፤ ማምለጫ « ጊዜው ፡ ያሳየናል » በማለት ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ ነው ፡ የዚህ ፡ ዓይነቱን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ በመቃወም ፡ ሥርዓተ-አልበኞች ፡ ሲናገሩ ፡ ለወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮታዊ ፡ ትምህርት ፡ የመስጠት ፡ ተግባሩን ፡ የከዳው ፡ ለማለት ፡ የቻሉት ። ኤንግልስ ፡ ያለፈውን ፡ የመጨረሻ ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ አብዮት ፡ ልምድ ፡ ላይ ፡ ያተኮረው ፡ በተለይ ፡ ባንክንና ፡ መንግሥትን ፡ በሚመለከት ፡ ረገድ ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ ምንና ፡ እንዴት ፡ ማድረግ ፡ እንዳለበት ፡ በጣም ፡ የተጨበጠ ፡ ጥናት ፡ ለማድረግ ፡ ነው ።

## ፫. ለቤቤል ፡ የተጻፈ ፡ ደብዳቤ ።

በማርክስና ፡ በኤንግልስ ፡ ስለመንግሥት ፡ ከተጻፉት ፡ ድርሰቶች ፡ ውስጥ ፤ እጅግ ፡ በጣም ፡ ግሩም ፡ ከሆኑት ፡ አንዱ ፤ ኤንግልስ ፡ ለቤቤል ፡ በመጋቢት ፡ ፲፰-፳፰ ፤ ፲፰፻፸፰ ዓ. ም. በላከው ፡ ደብዳቤ ፡ ውስጥ ፡ የሚከተለው ፡ ነው ። ይህ ፡ ደብዳቤ ፤ በቅንፍ ፡ ውስጥ ፡ እንገንዘበውና ፤ እኛ ፡ እንደምናውቀው ፡ ከሆነ ፡ ለመጀመሪያ ፡ ጊዜ ፡ የታተመው ፡ በቤቤል ፡ የራሱ ፡ የታሪክ ፡ ማስታወሻዎች (« ከሕይወቴ ፡ ታሪክ ») ሁለተኛው ፡ ቅፅ ፡ በ ፲፱፻፲፩ ዓ. ም. ነው ፤ ማለትም ፡ ደብዳቤው ፡ ተጽፎ ፡ ከተላከ ፡ ከሠላሳ ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡ በኋላ ፡ ነው ።

ኤንግልስ ፡ ለቤቤል ፡ ደብዳቤ ፡ የጻፈው ፤ ማርክስ ፡ በዝነኛው ፡ ለብራክ ፡[27] በጻፈው ፡ ደብዳቤ ፡ የተቸውን ፤





የኀታ ፡ ፕሮግራምን ፡ ረቂቅ ፡ በመተቸት ፡ ነው ። በተለይም ፡
የመንግሥትን ፡ ጥያቄ ፡ በሚመለከት ፡ ኤንግልስ ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፤

«ነፃው ፡ ሐዝባዊ ፡ መንግሥት ፡ ወደ ፡ ነፃ ፡ መን
ግሥት ፡ ተሸጋግሯል ። እነዚህ ፡ ቃላት ፡ በሰዋስዋ
ዊው ፡ ረገድ ፡ ሲወሰዱ ፡ ነፃ ፡ መንግሥት ፡ ማለት ፡
ከዜጋዎቹ ፡ ነፃ ፡ የሆነ ፡ መንግሥት ፡ ማለት ፡ ነው ፤
ይኸውም ፡ ፈላጭ ፡ ቆራጭ ፡ አገዛዝ ፡ ያለው ፡ መንግ
ሥት ፡ ማለት ፡ ነው ። በተለይ ፡ ከኮሙኑ ፡ በኋላ ፡ ስለ ፡
መንግሥት ፡ ያለው ፡ አሉቧልታ ፡ ውድቅ ፡ መሆን ፡ አለ
በት ፡ ምክንያቱም ፡ በቃሉ ፡ ትክክለኛ ፡ ፍች ፡ መሠረት ፡
ኮሙን ፡ መንግሥት ፡ አልነበረም ። ምንም ፡ እንኳ ፡
ቀደም ፡ ብሎ ፡ ማርክስ ፡ ፕሩዶንን ፡ በመቃወም ፡
በጻፈው ፡ መጽሐፉ ፤[28] በኋላም « በኮሙኒስት ፡ ማኒፌ
ስቶ » ውስጥ ፡ በግልፅ ፡ እንደተጠቀሰው ፡ የሶሺያሊ
ስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ሥርዓት ፡ ሲስፋፋ ፡ መንግሥት ፡
ራሱ ፡ ይከስማል (sich auflöst) ብሎ ፡ ይጠፋል ፡ ቢልም ፤
ሥርዓተ ፡ አልበኞች «በሕዝባዊ ፡ መንግሥት » ዓይና
ችንን ፡ ሊያወጡት ፡ ነው ። መንግሥት ፡ ለትግል ፤
ለአብዮት ፡ የምንጠቀምበት ፤ ጠላቶችን ፡ በኃይል ፡ የምን
ይዝበት ፡ የመሸጋገሪያ ፡ ተቋም ፡ ስለሆነ ፤ ስለ ፡ ነፃ ፡ ሕ
ዝባዊ ፡ መንግሥት ፡ መናገር ፡ የለየለት ፡ ሞኝነት ፡ ነው ።
ወዝ ፡ አደሩ ፡ መንግሥቱን ፡ እስከፈለገው ፡ ድረስ —
ለሚያስፈልገው ፡ ለነፃነት ፡ ብሎ ፡ አይደለም ፤ ጠላቶ
ቹን ፡ ለመያዝ ፡ እንጂ ፤ ስለ ፡ ነፃነት ፡ ለመናገር ፡ በሚቻ
ልበት ፡ ጊዜ ፡ መንግሥት ፡ እንደመንግሥት ፡ አይኖር
ምና ። ስለዚህም ፡ በሁሉም ፡ ቦታ ፡ መንግሥት ፡ የሚ
ለው ፡ ቃል ፡ የፈረንሳዩን ፡ ቃል « ኮሚዩንን » በደ
ምብ ፡ አድርጎ ፡ ሊተካ ፡ በሚችለው ፤ በጥሩው ፡ ጥንታ
ዊ ፡ የጀርመን ፡ ቃል « በኮሚዩኒቲ » (Gemeinwesen) ለመ



ተካት ፡ ሀሳብ ፡ ማቅረብ ፡ አለብን ።» (የጀርመን ፡ አሪ
ጅናል ፤ ገጽ ፡ ፫፻፳፩-፫፻፳፪)

ይህ ፡ ደብዳቤ ፡ የሚጠቅሰው ፤ ከጥቂት ፡ ሳምንታት ፡ በ
ኋላ ፡ ማርክስ ፡ በደብዳቤው ፡ የተቸውን (የማርክስ ፡ ደብ
ዳቤ ፡ የተጻፈው ፡ በግንቦት ፡ ፭ ፤ ፲፰፻፸፭ ዓ. ም. ነው)
የፓርቲውን ፡ ፕሮግራም ፡ መሆኑንና ፡ በዚያን ፡ ጊዜም ፡
ኤንግልስ ፡ ከማርክስ ፡ ጋር ፡ ለንደን ፡ ውስጥ ፡ ይኖር ፡ እንደ
ነበር ፡ ግልፅ ፡ መሆን ፡ አለበት ። ስለዚህም ፡ ኤንግልስ ፡
በመጨረሻው ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ « እኛ » ሲል ፡ ያለ ፡ ጥር
ጥር ፡ በራሱ ፡ ስምና ፡ በማርክስ ፡ ስም ፡ ለጀርመን ፡ የወዝ ፡
አደሮች ፡ ፓርቲ ፡ መሪ ፡ ሀሳብ ፡ የሚያቀርበው « መንግ
ሥት » የሚለው ፡ ቃል ፡ ከፕሮግራሙ ፡ እንዲፋቅና ፡ ኮሚ
ዩኒቲ ፡ በሚለው ፡ ቃል ፡ እንዲተካ ፡ ነው ።
ለአድርባዮች ፡ እንዲመች ፡ ሆኖ ፡ በተውገረገረው ፤
በአሁኑ ፡ ጊዜ ፡ « የማርክሲዝም » መሪዎች ፡ የዚህ ፡ ዓይ
ነቱ ፡ የፕሮግራም ፡ እርማት ፡ ሀሳብ ፡ ቢቀርብላቸው ፡
« ስለሥርዓተ-አልበኝነት » ምን ፡ ዓይነት ፡ ማጓራት ፡
ይነሳ ፡ ነበር!

ያጓሩ ። ይህ ፡ ከቡርዥዋው ፡ ምስጋና ፡ ያስገኝላቸዋል ።
እኛም ፡ ሥራችንን ፡ እንቀጥላለን ። የፓርቲአችንን ፡
ፕሮግራም ፡ በምናሻሽልበት ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ እውነቱ ፡ በጣም ፡
ለመቅረብ ፤ ከማርክሲዝም ፡ ጥምዘዛን ፡ በማስወገድ ፡ ማ
ርክሲዝምን ፡ ለመገንባት ፤ የወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ ለነጻ
ነቱ ፡ የሚያደርገውን ፡ ትግል ፡ ትክክል ፡ በሆነ ፡ መንገድ ፡
ለመምራት ፡ የኤንግልስና ፡ የማርክስ ፡ ምክር ፡ በማንኛው
ም ፡ ረገድ ፡ መቀበል ፡ አለብን ። በእርግጥ ፡ በቦልሼ
ቪኮች ፡ መካከል ፡ የኤንግልስንና ፡ የማርክስን ፡ ምክር ፡
የሚቃወም ፡ አይገኝም ። ምናልባት ፡ ሊነሳ ፡ የሚችለው ፡
ችግር ፡ በቃሉ ፡ ብቻ ፡ ነው ። በጀርመንኛ ፡ ቋንቋ « ኮሚ
ዩኒቲ » የሚል ፡ ትርጉም ፡ ያላቸው ፡ ሁለት ፡ ቃላት ፡ አሉ ፡






ከነዚህም ፡ ቃላት ፡ ኤንግልስ ፡ የመረጠው ፤ ነጠላ ፡ ኮሚዩኒቲን ፡ የሚያመለክተው ፡ ቃል ፡ ሳይሆን ፤ ጥምር ፡ ኮሚዩኒቲዎችን ፤ የኮሚዩኒቲዎች ፡ ሥርዓት ፡ የሚያመለክተው ፡ ቃልን ፡ ነው ። በሩሲያንኛ ፡ ቋንቋ ፡ እንደዚህ ፡ ዓይነት ፡ ቃል ፡ የለም ። ስለዚህ ፤ ምንም ፡ እንኳ ፡ ጉድለቶች ፡ ቢኖሩትም ፤ የፈረንሳይኛውን ፡ ቃል « ኮሚዩንን » መምረጥ ፡ ይኖርብናል ።

« ኮሚዩኑ ፤ (ኮሙን — ተርጓሚው) በቃሉ ፡ ትክክለኛ ፡ ፍች ፡ መሰረት ፡ መንግሥት ፡ አልነበረም » የሚለው ፡ የኤንግልስ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ በቴዎሪያዊ ፡ አንፃር ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ዋጋ ፡ ያለው ፡ ነው ። እላይ ፡ እንደተዘረዘረው ፡ ይህ ፡ አባባል ፡ ፍጹም ፡ ግልፅ ፡ ነው ። ኮሙን ፡ መጨቆን ፡ የነበረበት ፡ አብዛኛውን ፡ ሕዝብ ፡ ሳይሆን ፡ አነስተኛውን (በዝባዦችን) በመሆኑ — መንግሥት ፡ መሆኑን ፡ እያቆመ ፡ ነበር ። የቡርዥዋውን ፡ የመንግሥት ፡ መኪናን ፡ ሰብሮ ፡ ነበር ። በልዩው ፡ የመጨቆኛ ፡ ኃይል ፡ ቦታ ፡ ሕዝቡ ፡ ራሱ ፡ በመድረኩ ፡ ላይ ፡ ወጣ ። ይህ ፡ ሁሉ ፡ ከመንግሥት ፡ ትክክለኛ ፡ ፍች ፡ ማፈግፈግ ፡ ነው ። ኮሙን ፡ ጠንክሮ ፡ ቢገነባ ፡ ኖሮ ፤ በውስጡ ፡ ያሉት ፡ የመንግሥት ፡ ፈለጎች ፡ ራሳቸው « ይከስሙ » ነበር ። የመንግሥቱን ፡ ተቋሞች « ማጥፋት » ባላስፈለገው ፡ ነበር — ምንም ፡ የሚያደርጉት ፡ ስለሌለ ፡ መስራታቸውንም ፡ ያቆማሉና ።

« ሥርዓት-አልበኞች «በሕዝባዊ ፡ መንግሥት » ዓይናችንን ፡ ሊያወጡት ፡ ነው » ሲል ፡ ኤንግልስ ፡ በመጀመሪያ ፡ ደረጃ ፡ ባኩኒንንና ፡ እሱ ፡ በጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ ላይ ፡ ያደረሰውን ፡ ጥቃት ፡ በመገንዘብ ፡ ነው ። ኤንግልስ ፡ እነዚህ ፡ ጥቃቶች ፡ ትክክለኛ ፡ ናቸው ፡ ብሎ ፡ የሚቀበላቸው ፤ « ሕዝባዊ ፡ መንግሥት » እንደ « ነፃው ፡ ሕዝባዊ ፡ መንግሥት » ዋጋ ፡ የሌለው ፡ ሞኝነትና ፡ እንደዚሁም ፡ ከሶሺያሊዝም ፡ ማፈግፈግ ፡ ስለሆነ ፡ ነው ። ኤንግልስ ፡ የሚጥረው ፡ የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞ



ክራቶች ፡ ከሥርዓት-አልበኞች ፡ ጋር ፡ የሚያደርጉት ፡ ትግል ፡ ትክክለኛ ፡ መስመር ፡ ለማስያዝ ፤ ይህ ፡ ትግል ፡ በመሠረቱ ፡ ትክክለኛ ፡ ለማድረግ ፤ « መንግሥትን » በሚመለከት ፡ ትግሉ ፡ ከአድርባዮች ፡ አጉል ፡ እምነቶች ፡ ለማንፃት ፡ ነው ። ምን ፡ ያደርጋል! የኤንግልስ ፡ ደብዳቤ ፡ ለሰላሳ ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡ ጓዳ ፡ ውስጥ ፡ ተሸንቅሮ ፡ ነበር ። ቀጥለን ፡ እንደምናየው ፤ ይህ ፡ ደብዳቤ ፡ ከታተመ ፡ በኋላ ፡ እንኳ ፡ በውስጣዊ ፡ ይዘታቸው ፡ ኤንግልስ ፡ ያስጠነቀቃቸውን ፡ ስህተቶች ፡ ካውትስኪይ ፡ እኝኝ ፡ ብሎ ፡ ይደጋግማቸዋል ።

በነገራችን ፡ ላይ ፡ ቤቤል ፡ ለኤንግልስ ፡ በመስከረም ፡ ፳፩ ቀን ፡ ፲፰፻፸፭ ዓ. ም. በጻፈው ፡ የደብዳቤ ፡ መልስ ፡ ሲጽፍ ፡ በፕሮግራሙ ፡ ረቂቅ ፡ ላይ ፡ ከኤንግልስ ፡ ሀሳብ ፡ ጋር « ሙሉ ፡ በሙሉ ፡ እንደሚስማማ » እና ፡ ሊብክነኽት ፡ ለመካካስ ፡ በመዘጋጀቱ ፡ መገሰፁን ፡ ይናገራል ። (የጀርመን ፡ እትም ፤ የቤቤል ፡ ማስታወሻዎች ፤ ቅፅ ፡ ፪ ፤ ገጽ ፡ ፫፻፴፬) ቢሆንም ፡ የቤቤል « አላማችን » የሚለውን ፡ ጽሑፍ ፡ ብንወስድ ፡ በዚህ ፡ ጽሑፍ ፡ ውስጥ ፡ መንግሥትን ፡ በሚመለከት ፡ ያሉት ፡ አስተያየቶች ፡ ስህተተኛ ፡ ሆነው ፡ እናገኛቸዋለን ።

« በመደብ ፡ ገዥነት ፡ የተመሠረተ ፡ መንግሥት ፡ ወደ ፡ ሕዝባዊ ፡ መንግሥት ፡ መሸጋገር ፡ አለበት ።» («Unsere Ziele» ፤ የጀርመን ፡ እትም ፤ ፲፰፻፸፪ ዓ. ም. ፤ ገጽ ፡ ፲፬) ።

ይህ ፡ በቤቤል ፡ ጽሁፍ ፡ በ ፱ኛው (በዘጠነኛው!) እትም ፡ ታትሟል! መንግሥትን ፡ በሚመለከት ፡ ጉዳይ ፡ ያለ ፡ ማቋረጥ ፡ በተደጋገሙ ፡ የአድርባይ ፡ አስተያየቶች ፡ የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ በመዋጣቸው ፡ የሚያስደንቅ ፡ አይደለም ፤ በተለይ ፡ የኤንግልስ ፡ አብዮታዊ ፡





ትንተናዎች ፡ ጓዳ ፡ ውስጥ ፡ በተቀበሩበትና ፡ መላ ፡ የኑሮ ፡
ሁኔታዎች ፡ ለረጅም ፡ ጊዜ ፡ ከአብዮት «በተለዩበት » ጊዜ ።

## ፬. የኤርፉርቱ ፡ ፕሮግራም ፡ ረቂቅ ፡ ሂስ ።

መንግሥትን ፡ በሚመለከት ፡ የማርክሲዝምን ፡ ቴዎሪ ፡
በምንመረምርበት ፡ ጊዜ ፡ ኤንግልስ ፡ ለካውትስኪይ ፡ በሰኔ ፡
፳፱ ፡ ፲፰፻፺፩ ዓ. ም. የላከውን ፤ አሥር ፡ አመት ፡ ካለፈ ፡
በኋላ ፡ ብቻ ፡ በ «Neue Zeit» የታተመውን ፡ የኤርፉርቱን ፡
ፕሮግራም[29] ፡ ረቂቅ ፡ ሂስ ፡ መሳት ፡ የለበትም ፤ ምክንያ
ቱም ፡ ይህ ፡ ሂስ ፤ በተለይ ፡ በመሠረቱ ፡ የሚያተኩረው ፡
መንግሥታዊ ፡ መዋቅርን ፡ በሚመለከት ፡ በየሶሺያል-
ዴሞክራቶች ፡ አድርባይ ፡ ርዕየት ፡ ላይ ፡ ነውና ።

እግረ ፡ መንገዱን ፡ ኤንግልስ ፡ በኤኮኖሚ ፡ ጥያቄ ፡
ላይ ፡ ከፍተኛ ፡ ጠቀሜታ ፡ ያላቸውን ፡ ግሩም ፡ ግንዛቤ
ዎች ፡ አድርጓል ። ይህ ፡ የሚያሳየው ፡ ኤንግልስ ፡ በዘ
መናዊው ፡ ካፒታሊዝም ፡ የሚካሄዱትን ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡
ለውጦች ፡ ምን ፡ ያህል ፡ በንቃትና ፡ በአስተዋይነት ፡ ይከታ
ተል ፡ እንደነበርና ፡ እንደዚሁም ፡ እስከተወሰነ ፡ ደረጃ ፡
የአሁኑ ፤ የኢምፔሪያሊስት ፡ ዘመናችን ፡ ተግባሮችን ፡ አስ
ቀድሞ ፡ ማየት ፡ መቻሉን ፡ ነው ። ግንዛቤውም ፡ እነሆ —
በረቂቁ ፡ ፕሮግራም ፡ ውስጥ ፡ ስለተጠቀሰው ፡ የካፒታሊ
ዝም ፡ ባህርይ ፤ « ፕላን ፡ አልባነት » (Planlosigkeit) ስለ
ሚለው ፡ ቃል ፡ ኤንግልስ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ይጽፋል ፤

« ከአክስዮን ፡ ማኅበር ፡ ኩባንያዎች ፡ ሁሉንም ፡
የኢንዱስትሪ ፡ ቅርንጫፎችን ፡ በቁጥጥራቸው ፡ ሥር ፡
ወዳደረጉትና ፡ በሞኖፖሊ ፡ ወደያዙት ፡ ወደ ፡ ትሬስ
ቶች ፡ በሚሸጋገርበት ፡ ጊዜ ፡ የሚያከትመው ፡ የምርት ፡
የግል ፡ ንብረት ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፤ ፕላን ፡ አልባነትም ፡



ጭምር ፡ ነው ።» («Neue Zeit» ፤ ፳ኛው ፡ ዓመት ፤
ቅፅ ፡ ፩ ፤ ፲፱፻፩-፲፱፻፪ ዓ. ም. ፤ ገጽ ፡ ፰)

እዚህ ፡ ላይ ፡ በቴዎሪ ፡ አስተያየት ፡ ደረጃ ፡ እጅግ ፡
በጣም ፡ አስፈላጊ ፡ የሆን ፤ የካፒታሊዝም ፡ የመጨረሻ ፡
ደረጃ ፡ ስለሆነው — ስለኢምፔሪያሊዝም ፡ ማለትም ፡ ካ
ፒታሊዝም ፡ ወደሞኖፖሊ ፡ ካፒታሊዝም ፡ መሸጋገሩን ፡ እ
ናያለን ። በኋለኛው ፡ ላይ ፡ አፅንኦት ፡ ማድረግ ፡ ያስፈልጋል ፤
ምክንያቱም ፡ የሞኖፖሊ ፡ ካፒታሊዝም ፡ ወይም ፡ መንግ
ሥታዊ — ሞኖፖሊ ፡ ካፒታሊዝም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡
ካፒታሊዝም ፡ አይደለም ፤ እንድያውም « መንግሥታዊ ፡
ሶሺያሊዝም » ተብሎ ፡ ሊጠሩ ፡ ይቻላል ፤ እና ፡ የመሳሰሉ
ትን ፡ የሚል ፡ ስህተተኛ ፡ የቡርዥዋ ፡ የጥገና ፡ እምነት ፡
በጣም ፡ ተስፋፍቶ ፡ ይገኛልና ። ትሬስቶች ፤ እርግጥ ፡ ነው ፤
በፊትም ፡ አሁንም ፡ ወደፊትም ፡ የተሟላ ፡ ፕላን ፡ ሊሰጡ ፡
አይችሉም ። ቢሆንም ፡ ምን ፡ ያህል ፡ ፕላን ፡ ቢሰጡም ፤
ምን ፡ ያህል ፡ የካፒታሊስት ፡ ማግናቶች ፡ በብሄራዊ ፡ ወይ
ንም ፡ እንድያው ፡ በዓለም ፡ አቀፍ ፡ ደረጃ ፡ የምርት ፡ ብዛ
ትን ፡ በቅድሚያ ፡ ቢያሰላስሉም ፤ ምን ፡ ያህል ፡ በእቅድ ፡
ቢቆጣጠሩም ፤ ዞሮ ፡ ዞሮ ፡ የምንገኘው ፡ በካፒታሊዝም ፡
ሥር ፡ ነው ፤ ምንም ፡ እንኳ ፡ በአዲሱ ፡ ደረጃው ፡ ቢሆ
ንም ፤ አለጥርጥር ፡ በካፒታሊዝም ፡ ሥር ፡ ነው ። የዚ
ህ ፡ ዓይነት ፡ የካፒታሊዝም ፡ ለሶሺያሊዝም « ቅርብነት »
የወዝ ፡ አደሩን ፡ እውነተኛ ፡ ተወካዮች ፡ ለሶሺያሊስት ፡
አብዮት ፡ ቅርበት ፤ ምቹነት ፤ ቶሎ ፡ መከናወንና ፡ አጣ
ዳፊነት ፡ ማገልገል ፡ አለበት ፡ እንጂ ፡ ሁሉም ፡ ጠጋኞች ፡
ለማድረግ ፡ እንደሚሞክሩት ፡ የዚህ ፡ ዓይነት ፡ አብዮትን ፡
ማጉደፍያ ፤ ካፒታሊዝምን ፡ መወደሻ ፡ መሆን ፡ የለበትም ።

ይሁንና ፡ ወደ ፡ መንግሥት ፡ ጥያቄ ፡ እንመለስ ። ኤንግ
ልስ ፡ በደብዳቤው ፡ ውስጥ ፡ በተለይ ፡ ሶስት ፡ በጣም ፡ ጠ
ቃሚ ፡ ሀሳቦችን ፡ ይሰጣል ። አንደኛው — በሪፑብሊክ ፡





ጥያቄ ፡ ላይ ፤ ሁለተኛው — የብሄር ፡ ጥያቄ ፡ ከመንግ
ሥቱ ፡ መዋቅር ፡ ጋር ፡ ስላለው ፡ ግንኙነት ፤ ሶስተኛው —
በየቦታው ፡ ራስን ፡ በራስ ፡ የማስተዳደር ፡ መብትን ፡
በሚመለከት ።

ሪፑብሊኩን ፡ በሚመለከት ፡ ጥያቄ ፡ ኤንግልስ ፡ የኤ
ርፉርቱን ፡ ፕሮግራም ፡ ረቂቅ ፡ ሲተች ፤ የሂሱ ፡ ዋና ፡ ማእ
ከላዊ ፡ ነጥብ ፡ ያደርገዋል ። እኛም ፡ የኤርፉርት ፡ ፕርግ
ራም ፡ ለዓለም ፡ አቀፍ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ ያለውን ፡
አቢይነት ፡ በምናስተውስበት ፡ ጊዜ ፤ ለሁለተኛው ፡ ኢንተ
ርናሽናል ፡ ሞዴል ፡ መሆኑን ፡ በምናይበት ፡ ጊዜ ፤ ያለ
አንዳች ፡ ማጋነን ፤ ኤንግልስ ፡ የመላውን ፡ ሁለተኛ ፡ ኢንተ
ርናሽናል ፡ አድርባይነት ፡ ነቅፏል ፡ ለማለት ፡ ይቻላል ።

« የረቂቁ ፡ የፖለቲካ ፡ ጥያቄ — ይላል ፡ ኤንግ
ልስ — ከፍተኛ ፡ ደካማነት ፡ አለው ። በተለይም ፡ በረ
ቂቁ ፡ ውስጥ ፡ ቀጥታ ፡ መጠቀስ ፡ የነበረበት ፡ የለም
(ስርዝ ፡ የኤንግልስ) ።»

ቀጥሎም ፡ የጀርመን ፡ ሕገ ፡ መንግሥት ፡ በጣም ፡ አድ
ሀሪ ፡ ከሆነው ፡ የ ፲፰፻፺፩ ዓ. ም. ሕገ ፡ መንግሥት ፡ ግልባ
ጭ ፡ መሆኑን ፤ ዊልኼልም ፡ ሊብክነኽት ፡ እንዳለውም ፡
ሬይኽስታግ* «የፊላጭ ፡ ቆራጭ ፡ አገዛዝ ፡ የበለስ ፡ ቅጠ
ል » ብቻ ፡ እንደሆነ ፤ የንዑስ ፡ መንግሥታትንና ፡ የን
ዑስ ፡ የጀርመን ፡ መንግሥታትን ፡ ኅብረት ፡ ህልውና ፡
በሚደነግገው ፡ ሕገ ፡ መንግሥት ፡ መሠረት « ሁሉን
ም ፡ የምርት ፡ መገልገያ ፡ መሳሪያዎች ፡ ወደ ፡ ሕዝብ ፡ ንብ
ረት ፡ ለማዛወር » መመኘት « ግልፅ ፡ ሞኝነት » እንደሆ
ነ ፡ ግልፅ ፡ ያደርገዋል ።

---

* ሬይኽስታግ — የጀርመን ፡ ፓርላሜንት ። (ተርጓሚው)



ኤንግልስ ፡ በጀርመን ፡ የሪፑብሊክ ፡ ጥያቄ ፡ በፕሮ
ግራሙ ፡ ውስጥ ፡ በሕግ ፡ ለማስገባት ፡ ፈፅሞ ፡ የማይ
ቻል ፡ መሆኑን ፡ በደምብ ፡ በመገንዘብ « ይህንን ፡ አር
እስት ፡ መንካት ፡ አደገኛ ፡ ነው » ይላል ። ይሁን ፡ እን
ጂ ፡ ኤንግልስ ፡ ይህንኑ « ሁሉንም ፡ ሰው » ያረ
ካውን ፡ ግልፅ ፡ ግንዛቤ ፡ እንዲሁ — እንዳለ ፡ መቀ
በሉንም ፡ አልፈቀደም ። ኤንግልስ ፡ ይቀጥልና « በዚ
ህም ፡ ሆነ ፡ በዛ ፤ ዞሮ ፡ ዞሮ ፡ ነገሩ ፡ መነሳት ፡ አለበት ።
ይህ ፡ ምን ፡ ያህል ፡ አስፈላጊ ፡ እንደሆነ ፤ በተለይ ፡
በአሁኑ ፡ ጊዜ ፡ በሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ ሥነ ፡ ጽሁ
ፍ ፡ አብዛኛው ፡ ክፍል ፡ በመንሰራራት ፡ ላይ (einreißende)
ያለው ፡ አድርባይነት ፡ ያሳያል ። ፍጹም ፡ ልዩ ፡ የሆነ ፡
የፀረ-ሶሺያሊስቱ ፡ ሕግ[30] ፡ መታደሱን ፡ በመፍራት ፤
ወይንም ፡ በሕጉ ፡ ዘመን ፡ የወጡትን ፡ አስቸኳይ ፡ መግለ
ጫዎች ፡ ሁኔታ ፡ ሁሉ ፡ በማስታወስ ፤ አሁን ፡ የሚፈል
ጉት ፡ ፓርቲው ፡በጀርመን ፡ ውስጥ ፡ ባለው ፡ ያሁኑ ፡
ሕጋዊ ፡ ሥርዓት ፡ የፓርቲውን ፡ ጥያቄዎች ፡ በሙሉ ፡
በሰላማዊ ፡ መንገድ ፡ ለማሟላት ፡ ይቻላል ፡ ብሎ ፡
ፓርቲው ፡ እንዲቀበል ፡ ነው... »

የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ ፀረ-ሶሺያሊስቱ ፡
ሕግ ፡ ይታደሳል ፡ ብለው ፡ ፈርተው ፡ የመጣደፋቸውን ፡
መሠረታዊ ፡ ሀቅ ፡ ኤንግልስ ፡ በአፅንኦት ፡ በመጥቀስ ፤ ያለ
አንዳች ፡ ማመንታትም ፡ ይህ ፡ አድርባይነት ፡ ነው ፡ ብሎ ፡
ይጠራዋል ፤ ስለሆነም ፡ በጀርመን ፡ ውስጥ ፡ ሪፑብሊክና ፡
ነፃነት ፡ ስለሌለ « የሰላማዊ » መንገድ ፡ ህልም ፡ ፍጹም ፡
ዋጋ ፡ ቢስ ፡ መሆኑን ፡ ገልጧል ። ኤንግልስ ፡ እጆቹን ፡
ላለማሰር ፡ በጣም ፡ ተጠንቅቆ ፡ ነበር ። በሪፑብሊካዊ ፡
ወይም ፡ በጣም ፡ ነጻ ፡ በሆኑ ፡ አገሮች ፡ በሰላም ፡ ወደ ፡
ሶሺያሊዝም ፡ ለመገስገስ « ለማሰብ » (« ለማሰብ »ብቻ!)





እንደሚቻል ፡ ኤንግልስ ፡ ይቀበላል ፡ በጀርመን ፡ ግን ፡ ይላል ፡ ኤንግልስ ፡ ደጋግሞ ፤

« በጀርመን ፡ መንግሥቱ ፡ በጣም ፡ ኃይለኛ ፡ ለመሆን ፡ በተቃረበበት ፤ የሬይኽስታግና ፡ ሌሎች ፡ የውክልና ፡ አካሎች ፡ ሁሉ ፡ እውነተኛ ፡ ሥልጣን ፡ በተነፈጉበት ፤ በዚሁም ፡ ላይ ፡ ይህን ፡ ለማድረግ ፡ አስፈላጊ ፡ ባልነበረበት ፡ ጊዜ — ይህን ፡ መሳይ ፡ በጀርመን ፡ መስበካቸው ፡ ከፈላጭ ፡ ቆራጭ ፡ አገዛዝ ፡ ላይ ፡ የበለስን ፡ ቅጠል ፡ ገፍፎ ፡ ራስን ፡ ለራቁትነቱ ፡ መጋረጃ ፡ እንደማድረግ ፡ ይቆጠራል ። »

ይህን ፡ ምክር « በዝንጋታ » የያዙት ፡ አብዛኞቹ ፡ የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ ፓርቲ ፡ አፊሺያል ፡ መሪዎች ፡ በእርግጥ ፡ የፈላጭ ፡ ቆራጭ ፡ አገዛዝ ፡ መጋረጃ ፡ መሆናቸውን ፡ አረጋግጠዋል ።

«... የዚህ ፡ ዓይነት ፡ መመሪያዎች ፤ ዞሮ ፡ ዞሮ ፡ የአንድን ፡ ፓርቲ ፡ መንገድ ፡ ሊያስቱ ፡ ይችላሉ ። አስቀድመው ፡ አጠቃላይና ፡ አብስትራክት ፡ የሆኑ ፡ የፖለቲካ ፡ ጥያቄዎችን ፡ ይደቅናሉ ፤ ስለዚህም ፡ በእያንዳንዱ ፡ የታላቅ ፡ ድርጊት ፡ ወቅት ፤ በእያንዳንዱ ፡ የፖለቲካዊ ፡ ቀውስ ፡ የሚያጎርጡትን ፡ የወቅቱን ፡ አጣዳፊ ፡ ተጨባጭ ፡ ጥያቄዎችን ፡ ይሸፍናሉ ። በትንንቁ ፡ ወሳኙ ፡ ጊዜ ፡ ፓርቲው ፡ በድንገት ፡ አቢይ ፡ ከሆኑ ፡ ሌላ ፡ አንገብጋቢ ፡ ጥያቄዎችን ፡ ምንጊዜም ፡ ቢሆን ፡ አንስቶ ፡ ሰላልተወያየባቸው ፡ በፓርቲው ፡ ውስጥ ፡ ውዥንብር ፡ ከማስፈንና ፡ አንድነቱን ፡ ከማጣት ፡ በስተቀር ፡ ሌላ ፡ ምን ፡ ሊገኝ ፡ ይችላል?...

ይህ ፡ለጊዜያዊ ፡ ጥቅሞች ፡ ተብሎ ፡ የወቅቱን ፡ አቢይና ፡ መሠረታዊ ፡ አስተያየቶችን ፡ መርሳት ፤ ይህ ፡



ወደፊት ፡ የሚከተለውን ፡ ባለመመርመር ፡ ለጊዜያዊ ፡ መሳካት ፡ መታገልና ፡ መፍጨርጨር ፤ ይህ ፡ የወደፊቱን ፡ እንቅስቃሴ ፡ ለዛሬው ፡ መስዋእት ፡ ማድረግ — ምናልባት ፡ ይህ ፡ የሚደረገው « በቅንነት » ምክንያት ፡ ተነስቶ ፡ ሊሆን ፡ ይችላል ። ቢሆንም ፡ ይህ ፡ አድርባይነት ፡ ነው ፤ አድርባይነት ፡ ከመሆንም ፡ የሚያድነው ፡ የለም ፤ « ቅን »አድርባይነት ፡ ደግሞ ፡ ከሁሉም ፡ ሌሎች ፡ አድርባይነቶች ፡ የባሰ ፡ አደገኛ ፡ ነው...

አንድ ፡ የማያጠራጥር ፡ ነገር ፡ ቢኖር ፡ የኛ ፡ ፓርቲና ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ ሥልጣን ፡ ላይ ፡ ሊወጡ ፡ የሚችሉት ፡ በዴሞክራሲያዊ ፡ ሪፑብሊክ ፡ ቅርፅ ፡ ብቻ ፡ መሆኑን ፡ ነው ። ይህ ፡ ታላቁ ፡ የፈረንሳይ ፡ አብዮት ፡ አስቀድሞ ፡ እንዳሳየው ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ የበላይ ፡ ገዢነት ፡ ልዩ ፡ ቅርፅ ፡ ነው ።»

ኤንግልስ ፡ እዚህ ፡ ላይ ፡ በተለይ ፡ በጣም ፡ ጉልህ ፡ በሆነ ፡ አኳኋን ፡ በመደጋገም ፡ የሚገልፀው ፡ በሁሉም ፡ የማርክስ ፡ ሥራዎች ፡ ውስጥ ፡ የሚተመውን ፡ መሠረታዊ ፡ ሀሳብን ፡ ነው ፤ ማለትም ፡ ዴሞክራሲያዊ ፡ ሪፑብሊክ ፡ ለወዝ ፡ አደሩ ፡ የበላይ ፡ ገዢነት ፡ የቀረበ ፡ መንገድ ፡ መሆኑን ፡ ነው ። ምክንያቱም ፡ የዚህ ፡ ዓይነት ፡ ሪፑብሊክ ፡ የካፒታልን ፡ የበላይነት ፡ ቅንጣት ፡ ታህል ፡ ሳያስወግድ ፤ ከዚህም ፡ የተነሳ ፡ የሰፊውን ፡ ሕዝብ ፡ መበዝበዝንና ፡ የመደብ ፡ ትግልን ፡ ሳያጠፋ ፤ ትግሉ ፡ የግድ ፡ እንዲስፋፋ ፤ እንዲፋፋም ፡ እንዲፈነዳና ፡ እንዲከር ፡ ያደርጋል ፤ የሰፊውን ፡ ጭቁን ፡ ሕዝብ ፡ መሠረታዊ ፡ ፍላጎት ፡ ለማሟላት ፡ የሚቻልበት ፡ መንገድ ፡ ከተገኘ ፡ ይህ ፡ መንገድ ፡ እውነት ፡ ግቡን ፡ የሚመታው ፡ ሊታለፍ ፡ በማይቻለው ፡ በወዝ ፡ አደሩ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ ብቻ ፡ ነውና ፤ ሰፊው ፡ ጭቁን ፡ ሕዝብ ፡ በወዝ ፡ አደሩ ፡ ሲመራ ፡ ነው ። እነዚህ ፡ ቃላት ፡ ለመላው ፡ ሁለተኛ ፡ ኢንተርናሽናል





« የተረሱ » የማርክሲዝም « ቃላት » ናቸው ። የነዚህ ፡ ቃላት ፡ መረሳት ፡ በሜንሼቪኮች[5] ፡ ፓርቲ ፡ ታሪክ ፡ በ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የሩሲያ ፡ አብዮት ፡ መጀመሪያ ፡ ግማሽ ፡ ዓመት ፡ ላይ ፡ በተለይ ፡ በጣም ፡ ግልፅ ፡ ሆኖ ፡ ታይቷል ።

ከምልአተ ፡ ሕዝቡ ፡ ብሄራዊ ፡ ውህደት ፡ ጋር ፡ በማያያዝ ፡ ስለ ፡ ፌዴራል ፡ ሪፑብሊክ ፡ ጉዳይ ፡ ኤንግልስ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ይጽፋል ፤

« በዛሬይቱ ፡ ጀርመን ፡ ቦታ ፡ ምን ፡ ይተካ? » (በአድኃሪ ፡ ዘውዳዊ ፡ ሕገ ፡ መንግሥትና ፡ እንደዚሁም ፡ የዚህ ፡ ያህል ፡ አድኃሪ ፡ በሆነው ፡ በንዑስ ፡ መንግሥታት ፡ መከፋፈል ፤ ይህ ፡ መከፋፈል « የፕሩሲያዊነትን » ልዩ ፡ ጠባዮች ፡ ወደ ፡ ጠቅላላ ፡ ጀርመን ፡ እንደማሟሟት ፡ ፈንታ « ፕሩሲያዊነትን » ዘለአለማዊ ፡ ያደርጋል ።) « በእኔ ፡ አስተያየት ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ መጠቀም ፡ የሚችለው ፡ ቅርፅ ፡ አንድንና ፡ የማይከፋፈለውን ፡ ሪፑብሊክ ፡ ነው ። ምንም ፡ እንኳ ፡ በምሥራቅ ፡ ክፍለ ፡ ግዛት ፡ እንቅፋት ፡ እየሆነ ፡ በመሄድ ፡ ላይ ፡ ቢሆንም ፡ በሰፊው ፡ የአሜሪካ ፡ ግዛት ፡ የፌዴራል ፡ ሪፑብሊክ ፡ አሁንም ፡ በአጠቃላይ ፡ አስፈላጊ ፡ ነው ። ምንም ፡ እንኳ ፡ በአንድ ፡ ፓርላማ ፡ ውስጥ ፡ ቢሆኑም ፡ ሶስት ፡ ዓይነት ፡ የሕግ ፡ አውጪ ፡ ሥርዓት ፡ ጎን ፡ ለጎን ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ባሉባት ፤ በሁለት ፡ ደሴቶችዋ ፡ ውስጥ ፡ አራት ፡ ብሄሮች ፡ በሰፈሩበት ፡ እንግሊዝ ፡ ፌዴራል ፡ ሪፑብሊክ ፡ አንድ ፡ እርምጃ ፡ ወደፊት ፡ በሆነ ፡ ነበር ። በትንሽዋ ፡ ስዊስ ፡ ግን ፡ ፌዴራል ፡ ሪፑብሊክ ፡ እንቅፋት ፡ ከሆነ ፡ ቆይቷል ፤ ምክንያቱም ፡ ስዊስ ፡ በአውሮፓ ፡ የመንግሥታት ፡ ሥርዓት ፡ ተሳትፎ ፡ የሌላት ፡ አባል ፡ መሆንዋን ፡ ስለተቀበለችው ፡ ነው ። ጀርመን ፡ በስዊስ ፡ ሞዴል ፡ ፌዴራል ፡ ብትሆን ፡ አንድ ፡ ታላቅ ፡ የኋልዮሽ ፡



እርምጃ ፡ በሆነ ፡ ነበር ። የተባበረውን ፡ መንግሥት ፡ ፍጹም ፡ ከተወሀደ ፡ መንግሥት ፡ ሁለት ፡ ነጥቦች ፡ ይለዩታል ፤ እነሱም ፡ አንደኛ — የተባበረውን ፡ መንግሥት ፡ አባል ፡ የሆነው ፡ እያንዳንዱ ፡ ንዑስ ፡ መንግሥት ፤ የየግሉ ፡ የሆነ ፡ የፍትህ ፡ ብሄርና ፡ የወንጀለኛ ፡ መቅጫ ፡ ሕግ ፡ አውጪና ፡ አስፈጻሚ ፡ የፍርድ ፡ ሥርዓቶች ፡ አሉት ፤ ሁለተኛ — በሕዝባዊው ፡ ምክር ፡ ቤት ፡ ጎን ፡ እያንዳንዱ ፡ ትልቅም ፡ ሆነ ፡ ትንሽ ፡ የንዑስ ፡ አባል ፡ መንግሥት ፡ የሚመርጥበት ፡ ፌዴራል ፡ ምክር ፡ ቤት ፡ አለው ።» በጀርመን ፡ የተባበረ ፡ መንግሥት ፡ ፍፁም ፡ ወደተዋሀደ ፡ መንግሥት ፡ የሚመራ ፡ መሸጋገሪያ ፡ መንገድ ፡ ነው ፤ ስለሆነም ፡ የ ፲፰፻፵፰ እና ፡ የ ፲፰፻፵፱ ዓ. ም. « ከላይ ፡ የተደረገው ፡ አብዮት » መቀልበስ ፡የለበትም, ፡ እንድያውም « እንቅስቃሴ ፡ ከታች » እንዲታከልበት ፡ መደረግ ፡ አለበት ፡ እንጂ ።»

ኤንግልስ ፡ የመንግሥትን ፡ ቅርፆች ፡ በሚመለከት ፡ የግድየለሽነት ፡ አስተያየት ፡ አልነበረውም ፤ እንድያውም ፡ የአንፃሩ ፤ በበለጠ ፡ ጥልቀት ፡ ለመተንተን ፡ የሚሞክረው ፡ በተለይ ፡ የመሸጋገሪያ ፡ ቅርፆችን ፡ ሲሆን ፤ ከእያንዳንዱ ፡ ጉዳይ ፡ የተጨበጡ ፡ ታሪካዊ ፡ ጠባዮች ፡ በመነሳትም ፡ የመሸጋገሪያው ፡ ቅርፅ ፡ ከምን ፡ ወደ ፡ ምን ፡ እንደሚያልፍ ፡ ይጠቁማል ።

ጉዳዩን ፡ ከወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብና ፡ ከወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት ፡ አቋም ፡ በመመልከት ፤ ኤንግልስም ፡ እንደማርክስ ፡ የሚደግፈው ፡ ዴሞክራሲያዊ ፡ ዋህድነትን ፤ አንድና ፡ የማይከፋፈለውን ፡ ሪፑብሊክ ፡ ነው ። ፌዴራል ፡ ሪፑብሊክን ፡ የሚመለከተው ፡ ወይ ፡ እንደልዩና ፡ እንደ ፡ የእድገት ፡ እንቅፋት ፤ ወይ ፡ ከዘውዳዊ ፡ አገዛዝ ፡ ወደ ፡ የዋህድነት ፡ ሪፑብሊክ ፡ እንደ ፡ መሸጋገሪያ ፡ ቅርፅ ፤ በተለያዩ ፡ ልዩ ፡ ሁኔታዎች ፡ እንደ « አንድ ፡ እርምጃ ፡ ወደፊት » ነው ።





ከእነዚህ ፡ ልዩ ፡ ሁኔታዎች ፡ ውስጥም ፤ ብሄራዊ ፡ ጥያቄን ፡ በተቀዳሚ ፡ ያቀርባል ።

ኤንግልስም ፡ እንደ ፡ ማርክስ ፡ የንዑስ ፡ መንግሥታትን ፡ አድኅሪነትና ፡ ይህንም ፡ አድኅሪነት ፡ ለመሸፋፈን ፡ በአንዳንድ ፡ የተጨበጡ ፡ ሁኔታዎች ፡ የብሄር ፡ ጥያቄ ፡ መጠቀምን ፡ ያለአንዳች ፡ ምህረት ፡ ወቀሳ ፡ አደረገ ፡ እንጂ ፤ የትም ፡ ቦታ ፡ የብሄርን ፡ ጥያቄ ፡ ወደጐን ፡ የመተውና ፡ የመክዳት ፡ አንዳችም ፡ ምልክት ፡ እንኳ ፡ የለበትም ። ይህ ፡ ነጥብ « ከራሳቸው » ንዑስ ፡ መንግሥታት ፡ ጠባብ ፡ ብሄረተኝነት ፡ ከትክክለኛ ፡ ሕጋዊ ፡ ተቃውሞ ፡ ተነስተው ፡ የሆላንድና ፡ የፖላንድ ፡ ማርክሳውያን ፡ ብዙውን ፡ ጊዜ ፡ ስህተት ፡ ላይ ፡ የሚወድቁበት ፡ ነው ።

በእንግሊዝ ፡ ምንም ፡ እንኳን ፡ የጂኦግራፊያዊ ፡ ሁኔታዎች ፤ አንድ ፡ የወል ፡ ቋንቋና ፡ የብዙ ፡ ምእት ፡ ዓመታት ፡ ታሪክ ፡ መኖር ፤ የሀገሪቱን ፡ የተለያዩ ፡ ትንንሽ ፡ ክፍሎች ፡ የብሄር ፡ ጥያቄ « መጨረሻ ፡ ያበጁለት » ቢመስልም ፤ እዚህም ፡ ቢሆን ፡ እንኳን ፡ ኤንግልስ ፡ ግልፅ ፡ የሆነውን ፡ ሀቅ ፡ የብሄር ፡ ጥያቄ ፡ ጊዜው ፡ ያለፈበት ፡ ያከተመ ፡ ነገር ፡ እንዳልነበረ ፡ ያውቃል ፤ ስለሆነም ፡ የፌዴራላዊ ፡ ሪፑብሊክ ፡ መመሥረት ፡ አንድ « እርምጃ ፡ ወደፊት » እንደሚሆን ፡ አረጋግጧል ። እርግጥ ፡ ነው ፤ እዚህ ፡ ላይ ፡ ኤንግልስ ፡ የፌዴራል ፡ ሪፑብሊክ ፡ ጉድለቶች ፡ ሂስ ፡ ሳያደርግ ፡ ለመተው ፤ ወይም ፡ ለተዋሀደውና ፡ ለማእከላዊው ፡ ዴሞክራሲያዊ ፡ ሪፑብሊክ ፡ በጣም ፡ ቁርጠኛ ፡ ፕሮፓጋንዳና ፡ ትግል ፡ ላለማድረግ ፡ የቃጣበት ፡ አንድም ፡ ምልክት ፡ የለም ።

ነገር ፡ ግን ፤ ኤንግልስ ፡ ዴሞክራሲያዊ ፡ ቀሀድነት ፡ የሚተረጉመው ፤ የቡርዥዋና ፡ የንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ አይዲኦሎጂስቶች ፡ በመጨረሻዎቹም ፡ ውስጥ ፡ ሥርዓተ ፡ አልበኞችም ፡ እንደሚጠቀሙበት ፡ በቢሮክራሲያዊ ፡ መንገድ ፡ አይደለም ። ለኤንግልስ ፡ ቀሀድነት ፤ የመንግሥት ፡ አ






ንድነት « በኮሙኖችና » በክፍለ ፡ ግዛቶች ፡ በፈቃደኛነት ፡ መጠበቅን ፡ የመሰለ ፡ ሰፊ ፡ በየቦታው ፡ ራስን ፡ በራስ ፡ ማስተዳደርን ፤ እንደዚሁም ፡ ቢሮክራሲያዊ ፡ ድርጅቶችንና ፡ ማንኛውም ፡ ከላይ « ማዘዝን »ፍጹም ፡ ማውደም ፡ የሚለውን ፡ ሀሳብ ፡ ቅንጣት ፡ ያህል ፡ አይቃወምም ።

ኤንግልስ ፡ ማርክሲዝም ፡ በመንግሥት ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ ፕሮግራማዊ ፡ ርዕየትን ፡ በማስፋፋት ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ይጽፋል ፤ « ... እንግዲህ ፡ የተዋሀደ ፡ ሪፑብሊክ ፤ ይሁን ፡ እንጂ ፡ በ ፲፯፻፺፪ ዓ. ም. ያለንጉሥ ፡ እንደተመሠረተው ፡ ንጉሣዊ ፡ ግዛት ፤ እንደ ዛሬው ፡ የፈረንሳይ ፡ ሪፑብሊክ ፡ ዓይነት ፡ አይደለም ። ከ ፲፯፻፺፪ ዓ. ም. ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ፲፯፻፺፰ ዓ. ም. ድረስ ፡ እያንዳንዱ ፡ የፈረንሳይ ፡ ክፍል ፤ እያንዳንዱ ፡ ኮሙን (Gemeinde) የአሜሪካንን ፡ ራስን ፡ በራስ ፡ የፍጹም ፡ ማስተዳደር ፡ ሞዴል ፡ እንደተጠቀሙ ፡ ሁሉ ፤ እኛም ፡ ሊኖረን ፡ የሚገባው ፡ የዚህ ፡ ዓይነቱ ፡ ነው ። ራስን ፡ በራስ ፡ ማስተዳደር ፡ እንዴት ፡ መደራጀት ፡ እንደሚገባና ፡ እንዴት ፡ ያለቢሮክራሲ ፡ መሥራት ፡ እንደምንችል ፡ አሜሪካና ፡ የመጀመሪያው ፡ የፈረንሳይ ፡ ሪፑብሊክ ፡ አሳይተውናል ፤ አሁንም ፡ ቢሆን ፡ በካናዳ ፤ በአውስትራሊያና ፡ በሌሎች ፡ የእንግሊዝ ፡ ቅኝ ፡ ግዛቶች ፡ እየታየ ፡ ነው ። የዚህ ፡ ዓይነቱ ፡ ክፍለ ፡ ሀገራዊ (የአካባቢ)ና ፡ የጋርዮሽ ፡ ራስን ፡ በራስ ፡ ማስተዳደር ፤ ለምሳሌ ፡ ከስዊሱ ፡ ፌዴራላዊነት ፡ ይበልጥ ፡ ነፃ ፡ የሆነ ፡ ነው ። እውነት ፡ ነው ፤ በስዊስ ፡ ፌዴራሊዝም ፡ ሥር ፡ ካንቶን ፡ ከቡንዱ « (ማለት ፡ ከአጠቃላይ ፡ ፌዴራላዊ ፡ መንግሥቱ) » ይበልጥ ፡ በጣም ፡ ነፃ ፡ ነው ፤ እንደዚሁም ፡ ደግሞ ፡ ከአውራጃ (በዚርክ)ና ፡ ከኮሙን ፡ ጋር ፡ ሲነፃፀርም ፡ ነፃ ፡ ነው ። የካንቶናውያን ፡ አገዛዞች ፡ የአውራጃ ፡ ገገሮዎችንና ፡ ሹሞችን ፡

ይሾማሉ ፤ ይህ ፡ በእንግሊዘኛ ፡ ቋንቋ ፡ ተናጋሪዎች ፡ አገሮች ፡ አይታወቅም ፤ እኛም ፡ ለወደፊቱ ፡ እንደ ፡ ፕሩሲያውን ፡ ላንድሬቶችና ፡ ረጂሩንግስራቶች « (ከ ሚሺነሮችን ፤ የአካባቢ ፡ ፖሊስ ፡ አለቆችን ፡ አገረ ፡ ገዢዎችንና ፡ በጠቅላላው ፡ ከላይ ፡ የተሾሙትን ፡ ባለሥ ልጣኖች ፡ በሙሉ) » በማያዳግም ፡ ፍፁም ፡ ማው ደም ፡ አለብን ። » በዚህም ፡ ምክንያት ፡ ራስን ፡ በራስ ፡ ማስተዳደርን ፡ በሚመለከተው ፡ ነጥብ ፡ ላይ ፡ ኤንግ ልስ ፡ የሚቀጠለውን ፡ ሐሳብ ፡ ያቀርባል — « በጠቅ ላላ ፡ ሁሉ ፡ አቀፍ ፡ ምርጫ ፡ በተመረጡ ፡ ባለሥልጣ ኖች ፡ አማካኝነት ፡ ለክፍለ ፡ ሀገሮች » (ጠቅላይ ፡ ግዛ ት ፡ ወይም ፡ አካባቢ) « ለአውራጃዎችና ፡ ለኮሙ ኖች ፡ ሙሉ ፡ ራስን ፡ በራስ ፡ ማስተዳደር ፤ በመንግ ሥቱ ፡ የተሾሙትን ፡ የአካባቢና ፡ የክፍለ ፡ ሀገር ፡ ባለሥልጣኖችን ፡ በሙሉ ፡ ማባረር ።»

በኬሬንስኪይና ፡ በሌሎች « ሶሺያሊስት » ሚኒስት ሮች ፡ አገዛዝ ፡ ታፍኖ ፡ በነበረው « ፕራቭዳ »[31] (ቁ. ፷፰ ፤ ግንቦት ፡ ፳፰ ፤ ፲፱፻፲፯) አጋጣሚ ፡ አግኝቼ ፡ በዚህ ፡ ነጥብ ፡ ላይ — የታወቀ ፡ ነው ፡ በዚህ ፡ ነጥብ ፡ ላይ ፡ ብቻ ፡ ሳይ ሆን — የኛ ፡ የአስመሳይ ፡ አብዮታዊ ፤ የአስመሳይ ፡ ዴሞ ክራሲ ፡ አስመሳይ ፡ ሶሺያሊስታዊ ፡ ተወካዮች ፡ ከዴሞክ ራሲያዊነት ፡ ቁልጭ ፡ ባለ ፡ አሳፋሪነት ፡ ወደኋላ ፡ ማፈ ግፈጋቸውን ፡ አመልክቼ ፡ ነበር ። ግልፅ ፡ ነው ፤ ራሳቸው ን ፡ ከኢምፔሪያሊስት ፡ ቡርዧዋ ፡ ጋር « ያስተባበሩ » ሰዎች ፡ ለዚህ ፡ ዓይነት ፡ ሂስ ፡ ጆሮ ፡ የላቸውም ።

ኤንግልስ ፡ በተጨበጡ ፡ ሀቆች ፡ ላይ ፡ በመመስረት ፤ በተለይም ፡ በንዑስ ፡ ቡርዧዋ ፡ ዴሞክራቶች ፡ መካከል ፡ በጣም ፡ የአንሠራራውን ፤ ፌዴራላዊ ፡ ሪፑብሊክ ፡ ማለት ፡ ከተዋሀደ ፡ ሪፑብሊክ ፡ ይበልጥ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ነፃነት ፡ ያለው ፡ ማለት ፡ ነው ፡ የማ[illegible] ፡ [illegible] እምነት ፤



በጣም ፡ ትክክለኛ ፡ በሆነ ፡ ምሳሌ ፡ ላይ ፡ ተመርኩዞ ፡ ትክ ክል ፡ እንዳልሆነ ፡ ማረጋገጡን ፡ እዚህ ፡ መጥቀሱ ፡ በጣም ፡ አስፈላጊ ፡ ነው ። ይህ ፡ ስህተት ፡ ነውና ። በኤንግልስ ፡ የተጠቀሱት ፡ የ ፲፯፻፺፪-፲፯፻፺፰ ዓ. ም. የተዋሀደው ፡ የፈረ ንሳይ ፡ ሪፑብሊክና ፡ የስዊዘርላንዱ ፡ ፌዴራል ፡ ሪፑብሊክ ፡ ሀቆች ፡ ይህን ፡ ፋርሽ ፡ ያደርጉታልና ። ከፌዴራል ፡ ሪፑብ ሊክ ፡ ይልቅ ፡ እውነተኛ ፡ ዴሞክራሲያዊ ፡ የተዋሀደው ፡ ሪፑብሊክ ፡ ነው ፡ ይበልጥ ፡ ነፃነት ፡ የሰጠው ። በሌላ ፡ አነጋገር ፤ በታሪክ ፡ ከታወቁት ፡ የቀበሌ ፤ የአካባቢና ፡ የ ሌሎችም ፡ ነፃነቶች ፡ ከፍተኛ ፡ የሆነውን ፡ የሰጠው ፡ የተዋ ሀደው ፡ እንጂ ፡ ፌዴራላዊ ፡ ሪፑብሊክ ፡ አይደለም ።

በዚህ ፡ ሀቅ ፡ ላይ ፤ በእርግጥም ፡ በጠቅላላው ፡ ስለፌዴ ራላዊና ፡ ስለተዋሀደ ፡ ሪፑብሊክ ፤ ስለ ፡ አካባቢ ፡ ራስን ፡ በራስ ፡ የማስተዳደር ፡ ጥያቄ ፡ በፓርቲአችን ፡ ፕሮፓጋ ንዳና ፡ ቅስቀሳ ፡ በፊትም ፡ ሆነ ፡ አሁን ፡ በበቂ ፡ አልታሰ በበትም ።

## ፫. ማርክስ ፡ ለጻፈው « የእርስ ፡ በርስ ፡ ጦርነት ፡ በፈረንሳይ » በ ፲፰፻፺፩ ዓ. ም. የተሰጠ ፡ መቅድም ።

ኤንግልስ « የእርስ ፡ በርስ ፡ ጦርነት ፡ በፈረንሳይ » ለተባለው ፡ ጽሑፍ ፡ ሶስተኛ ፡ እትም ፡ በጻፈው ፡ መቅድ ም ፡ ላይ — ይህ ፡ መቅድም ፡ የተጻፈው ፡ በመጋቢት ፡ ፲፰ ፤ ፲፰፻፺፩ ዓ. ም. ሲሆን ፤ ለመጀመሪያ ፡ ጊዜ ፡ የታተመ ው ፡ በ «Neue Zeit» ነበር ። — መንግሥትን ፡ በሚመለ ከት ፡ ባሉት ፡ ጥያቄዎች ፡ ላይ ፡ ከሰጣቸው ፡ ጠቃሚ ፡አስተ ያየቶች ፡ ሌላ ፤ በተጨማሪ ፡ የኮሙንን ፡ ትምህርቶች ፡ ድርሞ ፡ በሚያስደንቅ ፡ ሁኔታ ፡ ግልፅ ፡ አድርጎ ፡ አቅ ርቦታል ።[32] ይህ ፡ መደምደሚያ ፡ ደራሲውን ፡ ከኮሙን ፡ በሚለየው ፡ የሃያ ፡ ዓመታት ፡ ጊዜ ፡ ጠቅላላ ፡ ልምድ ፡ በጣ

ም ፡ ጠልቆ ፡ በመሞላቱና ፣ በተለይም ፡ በጀርመን ፡ በተስ ፋፋው « በመንግሥት ፡ መለኮታዊ ፡ እምነት » ላይ ፡ የተሰነዘረ ፡ በመሆኑ ፣ ለተመለከትነው ፡ ጥያቄ ፡ ይህ ፡ ትክ ክል ፡ የማርክሲዝም ፡ የመጨረሻ ፡ ቃል ፡ ተብሎ ፡ ሊጠራ ፡ ይቻላል ።

ኤንግልስ ፡ እንደሚያስገነዝበው ፡ በፈረንሳይ ፡ ከእያንዳንዱ ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ ታጥቀ ው ፡ ስለነበሩ ፡ « በመንግሥቱ ፡ ቁንጮ ፡ ለነበሩት ፡ ቡ ርዧዋዎች ፡ መሣሪያቸውን ፡ መቀማት ፡ የመጀመሪያው ፡ ተቀዳሚ ፡ እርምጃ ፡ ነበር ። ስለሆነም ፡ በወዝ ፡ አደሮ ች ፡ ድል ፡ የመታ ፡ ማንኛውም ፡ አብዮት ፣ የሚያስከ ትለው ፡ በወዝ ፡ አደሮች ፡ መሸነፍ ፡ የሚያልቅ ፡ አዲ ስ ፡ ትግል ፡ ነበር ። »

ይህ ፡ የቡርዧዋ ፡ አብዮቶች ፡ ውጤት ፡ አጭር ፡ ቢሆ ንም ፡ በጣም ፡ ጉልህ ፡ የሆነ ፡ ነው ። የነገሩ ፡ ውስጠ ፡ ነገ ር — መንግሥት ፡ ጥያቄ ፡ ላይም ፣ ከብዙዎቹ ፡ ነገሮች ፡ ሌላ (ጭቁኑ ፡ መደብ ፡ መሣሪያ ፡ አለው ፡ ወይ?) የሚለው — እዚህ ፡ ላይ ፡ በግሩም ፡ ሁኔታ ፡ ተጠቅሷል ። በተለይም ፡ ይ ህንን ፡ ውስጠ ፡ ነገር ፡ በቡርዧዋ ፡ ርዕዮተ ፡ ዓለም ፡ ተፅ እኖ ፡ ሥር ፡ ያሉ ፡ ፕሮፌሰሮችና ፡ የንዑስ ፡ ቡርዧዋ ፡ ዴሞክራቶች ፡ አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ ችላ ፡ ይሉታል ። በ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የሩሲያ ፡ አብዮት ፡ የቡርዧዋ ፡ አብዮትን፡ ምሥጢር ፡ የመግለጽን ፡ ክብር (የካቬኝያክ ፡ ክብር) « በሜ ንሼቪኩና » « በማርክሳዊ ፡ ነኝ » ባዩ ፡ በጸረተሊ ፡ ላይ ፡ ወደቀ ። ጸረተሊ ፡ በሰኔ ፡ ፲፩ « ታሪካዊ » ንግግሩ ፡ ቡ ርዧዋዎቹ ፡ የፔትሮግራድን ፡ ሠራተኞች ፡ ትጥቅ ፡ ለማ ስፈታት ፡ መቁረጣቸው ፡ ለፈፌ ፣ አንቧረቀ ፣ እርግጥ ፡ ነው ፣ ውሳኔውን ፡ ያቀረበው ፡ እንደራሱ ፡ የግል ፡ ውሳኔ፡ አድርጎና ፣ በጠቅላላው « ለመንግሥቱ » አስፈላጊ ፡ እን ደሆነ ፡ አ[illegible]ው![33]



የሰኔው ፲፩ የጸረተሊ ፡ ታሪካዊ ፡ ንግግር ፣ በእርግጥ ፡ ለማንኛው ፡ የ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. አብዮት ፡ የታሪክ ፡ ጸሐፊ ፡ በአቶ ፡ ጸረተሊ ፡ የሚመራው ፡ የሶሺያሊስት-አብዮታ ውያንና ፡ የሜንሼቪኮች ፡ ቡድን ፡ እንዴት ፡ አብዮታዊ ውን ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ በመቃወም ፡ ወደ ፡ ቡርዧዋው ፡ እንደከዱ ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ጉልህ ፡ ከሆኑ ፡ ማስረጃዎች ፡ እን ደ ፡ አንዱን ፡ ሊጠቀሙበት ፡ ይችላሉ ።

ሌላው ፡ ኤንግልስ ፡ እግረ ፡ መንገዱን ፡ የሰጠው ፡ አስተ ያየት ፡ ከመንግሥት ፡ ጥያቄ ፡ ጋር ፡ የተያያዘ ፡ ሲሆን ፡ሃይ ማኖትን ፡ ይመለከታል ። የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ እየበሰበሰና ፡ ይበልጥ ፡ አድርባይ ፡ እየሆነ ፡ በሄደ ፡ መጠን « ሃይማኖት ፡ የግል ፡ ጉዳይ ፡ ሆኖ ፡ መታወጅ ፡ አለበት » የሚለው ፡ የታወቀ ፡ አስተሳሰብ ፡ አሁንም ፣ አሁንም ፡በጮ ርቃነት ፡ የተጣመመ ፡ ትርጉም ፡ ለመስጠት ፡ መንሸራተ ታቸው ፡ በደንብ ፡ የታወቀ ፡ ነው ። በተለይም ፡ ይህ ፡ አስ ተሳሰብ ፡ ነው ፡ ለአብዮታዊው ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ፓርቲም ፡ እንኳን ፡ ሳይቀር ፡ የሃይማኖት ፡ ጥያቄ ፡ የግል ፡ ጉዳይ ፡ ነው ፡ በማለት ፡ ለማጣመም ፡ የተሞከረው!! ይህን ፡ የወ ዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮታዊ ፡ ፕሮግራም ፡ ፍጹም ፡ መካድን ፡ ነው ፡ ኤንግልስ ፡ በጥብቅ ፡ የተቃወመው ። ኤንግልስ ፡ በ ፲፰፻፺፩ ዓ. ም. በጣም ፡ ደካማ ፡ የአድርባይነት ፡ ጅምሮ ችን ፡ በማጤኑ ፡ በጥንቃቄ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ይገልፃል ፣

« በኮሙን ፡ ውስጥ ፡ የተቀመጡት ፡ ወዝ ፡ አደ ሮች ፡ ብቻ ፡ ወይንም ፡ የታወቁ ፡ የወዝ ፡ አደሮች ፡ ተወ ካዮች ፡ ብቻ ፡ ስለነበሩ ፣ የኮሙኑ ፡ ውሳኔዎች ፡ ወዝ ፡ አደራዊ ፡ ቁርጠኛ ፡ ባህርይ ፡ ያዙ ። ምክንያቱም ፡ እነ ዚህ ፡ ውሳኔዎች ፡ ሪፑብሊካዊ ፡ ቡርዧዋው ፡ ከፍር ሀት ፡ የተነሳ ፡ ብቻ ፡ ማሳለፍ ፡ ያቃተውን ፡ ለውጦች ፡ አውጀዋል ፣ ለወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ ነፃ ፡ እንቅስቃሴ ፡ አስፈላጊ ፡ መሠረቶች ፡ አገናፅፈዋል ። መንግሥትን ፡

በሚመለከት ፡ ረገድ ፡ ሃይማኖት ፡ ፍጹም ፡ የግል ፡ ጉዳይ ፡ ነው ፡ የሚለውን ፡ መርህ ፡ በተግባር ፡ ላይ ፡ ማዋል ፡ ይህ ፡ ነው ። ኮሙኑ ፡ ቀጥታ ፡ ለወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ ጥቅም ፡ የሚውሉና ፡ በከፊል ፡ አሮጌውን ፡ ሥርዓት ፡ ማኅበር ፡ አጥልቀው ፡ የሚቆርጡ ፡ አዋጆችን ፡ አውጇዋል ። »

ኤንግልስ « መንግሥትን ፡ በሚመለከት ፡ ረገድ » የሚሉትን ፡ ቃላት ፡ ሆን ፡ ብሎ ፡ በስርዝ ፡ የሚያጠብቀው ፡ ፓርቲውን ፡ በሚመለከት ፡ ረገድ ፡ ሃይማኖት ፡ የግል ፡ጉዳይ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ባወጀው ፤ በዚህም ፡ የተነሳ ፡ የአብዮታዊው ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ፓርቲን ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ወራዳ ፡ እስከ ፡ ሆነው ፡ የጮርቃነት « ነፃ ፡ አስተሳሰብ » ደረጃ ፡ ድረስ ፡ ዝቅ ፡ ባደረገው ፤ የልዩ ፡ ልዩ ፡ እምነትን ፡ ሁኔታ ፡ ለመፍቀድ ፡ ዝግጁ ፡ ለሆነው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሕዝብን ፡ የሚያደነዝዘው ፡ የሃይማኖት ፡ አፍዮምን (opium) በመቃወም ፡ የሚታገለውን ፡ ፓርቲን ፡ በሚያወግዘው ፡ በጀርመን ፡ አድርባይነት ፡ ላይ ፡ የተሰነዘረ ፡ ቀጥተኛ ፡ ተግሳፅ ፡ ነው ።

የወደፊት ፡ የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ ታሪክ ፡ ጸሐፊ ፤ የ ፲፱፻፲፬ ዓ. ም. አሳፋሪ ፡ ክስረታቸው ፡ ሥሮች ፡ ለማግኘት ፡ በሚፈልግበት ፡ ጊዜ ፤ በሩን ፡ ለአድርባይነት ፡ በሰፊው ፡ ከከፈቱት ፤ በፓርቲው ፡ ርዕዮተ ፡ ዓለም ፡ መሪ ፡ ከካውትስኪይ ፡ የክህደት ፡ ጽሑፎች ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ የፓርቲው ፡ የ፲፱፻፲፫ ዓ. ም. «Los-von-Kirche-Bewegung»[34] (« ከ ቤተ ፡ ክርስትያን ፡ ተለዩ » በሚለው ፡ እንቅስቃሴ ፡ ላይ) አቋሙ ፡ ድረስ ፤ በዚህ ፡ ጥያቄ ፡ ላይ ፡ ብዙ ፡ ጠቃሚ ፡ ማስረጃዎች ፡ ሊያገኝ ፡ ይችላል ።

አሁንም ፡ ደግሞ ፤ ከኮሙኑ ፡ ሃያ ፡ ዓመታት ፡ በኋላ ፡ ኤንግልስ ፡ ለታጋይ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ የኮሙኑን ፡ ትምህርቶች ፡ እንዴት ፡ እንዳጠቃለለ ፡ እንመልከት ።

ኤንግልስ ፡ ከፍተኛ ፡ አስፈላጊነት ፡ ያየባቸው ፡ ትምህርቶች ፡ [illegible] ፤



« … ያ ፡ ናፖሌዎን ፡ በ ፲፯፻፺፰ ዓ. ም. የመሠረተውና ፡ ከዚያን ፡ ጊዜ ፡ ጀምሮ ፡ እያንዳንዱ ፡ አዲስ ፡ አገዛዝ ፡ እንደ ፡ አስፈላጊ ፡ መሣሪያ ፡ የሚወርሰውና ፡ በጠላቶቹ ፡ ላይ ፡ የሚጠቀምበት ፤ በተለይ ፡ የቀድሞው ፡ ማዕከላዊ ፡ መንግሥት ፡ የመጨቆኛ ፡ ሥልጣን ፤ የጦር ፡ ኃይል ፤ ፖለቲካዊ ፡ ፖሊስና ፡ ቢሮክራሲ ፤ በተለይ ፡ ይህ ፡ ኃይል ፡ ነበር ፡ ልክ ፡ በፓሪስ ፡ እንደወደቀው ፡ ሁሉ ፤ በየቦታው ፡ በፈረንሳይ ፡ መውደቅ ፡ የነበረበት ።

ገና ፡ ከመጀመሪያው ፡ ጀምሮ ፡ ኮሙኑ ፡ ማመን ፡ የተገደደበት ፤ የወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ አንዴ ፡ ሥልጣን ፡ ላይ ፡ ከወጣ ፡ በድሮው ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ መገልገልን ፡ መቀጠል ፡ እንደማይችል ፤ አሁን ፡ አሁን ፡ የተገኘውን ፡ የበላይነት ፡ እንደገና ፡ ላለማጣት ፡ ይህ ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ መደብ ፤ በአንድ ፡ በኩል ፡ በፊት ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ይጠቀሙበት ፡ የነበረውን ፡ አሮጌውን ፡ የጭቆና ፡ መኪና ፡ ማስወገድ ፡ እንዳለበትና ፤ በሌላ ፡ በኩል ፡ ደግሞ ፡ ራሱን ፡ ከራሱ ፡ ተወካዮችና ፡ ባለሥልጣኖች ፡ ለመከላከል ፤ ሁሉም ፡ አንድም ፡ ሳይቀር ፡ በተፈለገ ፡ ጊዜ ፡ ሊሻሩ ፡ እንደሚችሉ ፡ ማወጅ ፡ ነበረበት … »

ኤንግልስ ፡ አሁንም ፡ አሁንም ፡ በአፅንኦት ፡ የሚጠቅሰው ፡ በዘውድ ፡ አገዛዝ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፤ እንደዚሁም ፡ በዴሞክራሲያዊ ፡ ሪፑብሊክ ፡ ጭምር ፡ መንግሥት ፡ እንደ ሆነ ፡ እንደሚቀር ፤ ማለትም ፡ መሠረታዊ ፡ የመለያ ፡ ባህርያቱን ፡ እንደማይለቅ — ይኸውም ፡ ባለሥልጣኖች ፤ « የኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ አገልጋዮች » እና ፡ የኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ አካሎች ፡ ወደ ፡ በኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ላይ ፡ ጌትነት ፡ እንደሚሸጋገሩ ፡ ነው ።

« … ይህ ፡ የመንግሥትና ፡ የአካሎቹ ፡ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ አገልጋይነት ፡ ወደ ፡ በኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ላይ ፡ ጌትነት ፡ መሸጋገርን ፡ ለማጥፋት — ሽግግሩ ፡ የሁሉም ፡ የቀድሞ ፡ መንግሥታት ፡ የማይቀር ፡ ጠባይ ፡ በመሆኑ — ኮሙኑ ፡ ሁለት ፡ ስህተት ፡ የሌለባቸው ፡ ዘዴዎችን ፡ ተጠቅሟል ። በመጀመሪያ ፡ ደረጃ — ሁሉም ፡ ሥልጣኖች — የአስተዳደርን ፤ የፍርድን ፤ የትምህርትን — የተሞላው ፡ በአጠቃላይ ፡ ምርጫ ፡ በተመረጡ ፡ ሰዎች ፡ ሲሆን ፤ እነዚህ ፡ የተመረጡት ፡ ሰዎች ፡ በመራጮቹ ፡ ውሳኔ ፡ በማናቸውም ፡ ጊዜ ፡ ሊሻሩ ፡ እንደሚችሉ ፡ ደንግጓል ። በሁለተኛ ፡ ደረጃ — ከፍተኛም ፡ ሆኑ ፡ አነስተኛ ፡ ባለሥልጣኖች ፡ በሙሉ ፡ የሚከፈላቸው ፡ ደመወዝ ፡ ሌሎች ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ የሚያገኙትን ፡ ደመወዝ ፡ ያህል ፡ ብቻ ፡ ነበር ። በኮሙኑ ፡ የተከፈለው ፡ ከፍተኛ ፡ ደመወዝ ፡ ፮ ሺህ ፡ ፍራንክ* ፡ ነበር ። በዚህ ፡ ዓይነት ፡ መንገድ ፡ ለቦታ ፡ ሽሚያና ፡ ለግል ፡ ጥቅም ፡ እድገት ፡ ማነፍነፍ ፡ጠንካራ ፡ የሆነ ፡ እንቅፋት ፡ ተበጀለት ። እንዲያውም ፡ ይህ ፡ የውክልና ፡ አካሎች ፡ ተወካዮችን ፡ በማያፈናፍኑ ፡ ትእዛዞች ፡ ከሚያስሩት ፡ ሌላ ፤ በኮሙን ፡ የተጨመሩ ፡ ናቸው ። »

ኤንግልስ ፡ እዚህ ፡ ላይ ፡ ጠቃሚ ፡ ወደሆነው ፡ የመለያያ ፡ ወሰን ፤ ማለትም ፡ ትክክለኛ ፡ ዴሞክራሲ ፤ በአንድ ፡

---

* በመጠኑ ፡ ይህ ፡ በግምት ፡ ፳፬ መቶ ፡ ሩብል ፡ ይሆናል ። በአሁኑ ፡ ምንዛሪ ፡ ፮ ሺህ ፡ ሩብል ፡ ያህል ፡ ነው ። ለጠቅላላው ፡ መንግሥት ፡ በከፍተኛ ፡ እስከ ፡ ፮ ሺህ ፡ ሩብል ፡ ሳይሰጡ — ይህ ፡ በቂ ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፤ ለምሳሌ ፡ ለከተማ ፡ ምክር ፡ ቤቶች ፡ ፱ ሺህ ፡ ሩብል ፡ ደመወዝ ፡ የሚገመግሙ ፡ ቦልሸቪኮች ፡ ፍጹም ፡ ይቅር ፡ የማይባሉ ፡ ናቸው ።





በኩል ፡ ወደ ፡ ሶሺያሊዝም ፡ የሚሸጋገርበትን ፤ በሌላ ፡ በኩል ፡ ደግሞ ፡ ሶሺያሊዝም ፡ የሚጠይቅበትን ፡ ተመልክቷል ። ምክንያቱም ፡ መንግሥት ፡ እንዲደመሰስ ፡ የመንግሥት ፡ አገልግሎት ፡ ተግባሮችን ፡ አብዛኛው ፡ ሰፊ ፡ምልአተ ፡ ሕዝብ ፤ በኋላም ፡ መላው ፡ ሕዝብ ፡ ገብቶት ፡ ሊፈጽማቸው ፡ ወደሚችላቸው ፡ ቀላል ፡ የመቆጣጠርና ፡ የሂሳብ ፡ አያያዝ ፡ ሥራዎች ፡ መለወጥ ፡ ያስፈልጋል ። ለግል ፡ ሙያ ፡ እድገት ፡ ማነፍነፍ ፡ ፍጹም ፡ እንዲጠፋ ፤ በሕዝባዊ ፡ አገልግሎት ፡ ውስጥ « የተከበረ » ሹመት ፤ ምንም ፡ እንኳ ፡ ገቢ ፡ ባያስገኝም ፤ በሁሉም ፡ ነፃ ፡ ካፒታሊስት ፡ አገሮች ፡ ሁልጊዜ ፡ እንደሚደረገው ፡ ከፍተኛ ፡ ገቢ ፡ ወደሚያስገኙ ፤ በባንኮችና ፡ አክስዮን ፡ ኩባንያዎች ፡ ሥልጣኖች ፡ ለመውጣት ፡ እንደ ፡ ድልድይ ፡ ሆነው ፡ እንዳያገለግሉ ፡ መደረግ ፡ አለበት ።

ይሁን ፡ እንጂ ፡ አንዳንድ ፡ ማርክሳውያን ፤ ለምሳሌ ፡ የብሔሮችን ፡ የራስ ፡ እድል ፡ በራስ ፡ የመወሰን ፡ መብት ፡ ጥያቄ ፡ በሚመለከት ፤ ይህ ፡ በካፒታሊዝም ፡ ሥር ፡ አይቻልም ፤ በሶሺያሊዝም ፡ ሥርማ ፡ ትርፍ ፡ ነገር ፡ ነው ፡ ብለው ፡ በመከራከር ፡ ሲሳሳቱ ፤ ኤንግልስ ፡ ግን ፡ እንደዚህ ፡ ዓይነቱን ፡ ስህተት ፡ አልፈጸመም ። ይህ ፡ ግሩም ፡ የሚመስለው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ስህተተኛ ፡ የሆነ ፡ አስተያየት ፡ በማንኛውም ፡ ዴሞክራሲያዊ ፡ ተቋም ፡ አንፃር ፤ ከመካከለኛ ፡ የባለሥልጣኖች ፡ ደመወዝ ፡ ጭምር ፤ ሊደገም ፡ ይቻል ፡ ይሆናል ። ምክንያቱም ፡ በካፒታሊዝም ፡ ሥር ፡ ፍጹም ፡ ትክክለኛ ፡ ዴሞክራሲ ፡ አይቻልምና ፤ በሶሺያሊዝም ፡ ሥር ፡ ደግሞ ፡ ማንኛውም ፡ ዴሞክራሲ ፡ ይከስማል ።

ይህ ፡ ልክ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ጠቅላላ ፡ ፀጉሩ ፡ በአንድ ፡ ፀጉር ፡ ቢቀንስ ፡ መላጣ ፡ ሊሆን ፡ ይችላል ፡ እንደሚለው ፡ የቀድሞ ፡ ቀልድ ፡ ተመሳሳይ ፡ የሆነ ፡ ሶፊዝም ፡ ነው ።

ዴሞክራሲን ፡ እስከ ፡ መጨረሻ ፡ ደረጃ ፡ ለማሳደግ ፤ የዚህን ፡ እድገት ፡ ቅርፆች ፡ ለማግኘት ፤ የተገኙትንም ፡

በተግባር ፡ ለመፈተን ፤ ወዘተ ፤ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ለኅብረተ ፡
ሰባዊ ፡ አብዮት ፡ የሚደረገው ፡ ትግል ፡ ከመሠረታዊ ፡
ተግባሮች ፡ አንዱ ፡ ነው ። በተነጥላ ፡ የተወሰደ ፡ ምንም ፡
ዓይነት ፡ ዴሞክራሲ ፡ ሶሺያሊዝምን ፡ ሊያወጣ ፡ አይችል
ም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በገቢር ፡ ላይ ፡ ሲሆን ፡ ዴሞክራሲ « በነ
ጣላ ፡ አይወሰድም » ፤ ከሌሎች ፡ ነገሮች ፡ ጋር « በዘኅ
ብረት ፡ ይወሰዳል » እንጂ ፤ በኤኮኖሚ ፡ ኑሮም ፡ እንዲሁ ፡
ተፅእኖ ፡ ይፈጥራል ፤ የኤኮኖሚውን ፡ እድገት ፡ ያፋጥ
ናል ፤ በተራው ፡ የኤኮኖሚው ፡ እድገት ፡ ተፅእኖ ፡ ይታይ
በታል ፡ እንዲህ ፡ እያለም ፡ ይቀጥላል ። ይህ ፡ የህያው ፡ ታሪ
ክ ፡ ዲያሌክቲክ ፡ ነው ።

ኤንግልስ ፡ ይቀጥላል ፤

« ... ይህ ፡ የቀድሞውን ፡ የመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡
ማንኮታኰት (Sprengung) እና ፡ እርሱም ፡ በአዲስና ፡ እው
ነተኛ ፡ ዴሞክራሲያዊ ፡ በሆነ ፡ የመንግሥት ፡ ሥልጣ
ን ፡ መተካት ፡ « በእርስ ፡ በርሱ ፡ ጦርነት » ሶስተኛ ፡
ክፍል ፡ በሰፊው ፡ ተብራርቶ ፡ ተገልጿል ። ይሁን ፡ እን
ጂ ፡ የመተካቱ ፡ አንዳንድ ፡ ጠባዮችን ፡ እንደገና ፡ መመል
ከት ፡ አስፈላጊ ፡ ነበር ፤ ምክንያቱም ፡ በጀርመን ፡
በተለይ ፡ በመንግሥት ፡ ላይ ፡ ያለው ፡ መለኮታዊ ፡
እምነት ፡ በቡርዥዋውና ፡ እንድያውም ፡ በብዙዎቹ ፡
ወዝ ፡ አደሮችም ፡ እንኳን ፡ ሳይቀር ፡ ከፍልስፍና ፡
ወደ ፡ አጠቃላይ ፡ ንቃተ ፡ ህሊና ፡ አልፏልና ። እንደ ፡
ፍልስፍናው ፡ ፅንሰ ፡ ሀሳብ ፡ መንግሥት « የሀሳብ ፡
ህልውና » ማለት ፡ነው ፤ ወይም ፡ ወደፍልስፍና ፡ ቃላ
ት ፡ ሲተረጐም ፡ በመሬት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ግዛ
ት ፡ ማለት ፡ ነው ፤ መንግሥት ፡ ማለት ፡ እንግዲህ ፡
ዘለዓለማዊ ፡ እውነትና ፡ ፍትህ ፡ የሰፈኑበት ፡ ወይም ፡
የሚሰፍኑበት ፡ ሁኔታ ፡ ማለት ፡ ነው ። ከዚህም ፡ የሚ
ከተለው ፡ በመንግሥትና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የተያያዘው ፡



ሁሉ ፡ መለኮታዊ ፡ አክብሮት ፡ ነው ። መለኮታዊ ፡ አክ
ብሮት ፡ ሥሩ ፡ ያለው ፡ ሰዎች ፡ ከሕፃንነት ፡ ጀምረው ፡
ማሰብ ፡ እንደለመዱት ፤ የጠቅላላ ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡ ፡
የጋራ ፡ ጉዳዮችና ፡ ጥቅሞች ፡ ሊከናወኑና ፡ ሊጠበቁ ፡
የሚችሉት ፡ በሌላ ፡ ሳይሆን ፡ በድሮው ፡ ዘዴ ፤ ማ
ለትም ፡ በመንግሥቱና ፡ ከፍተኛ ፡ ደመወዝ ፡ በሚዝ
ቁት ፡የመንግሥቱ ፡ ባለሥልጣኖች ፡ በኩል ፡ ብቻ ፡
ነው ፡ ብለው ፡ ስለሚገምቱ ፡ ነው ። ሰዎች ፡ በትው
ልድ ፡ የተያያዘ ፡ የዘውድ ፡ አገዛዝ ፡ እምነትን ፡ አስ
ወግደው ፡ የዴሞክራቲክ ፡ ሪፑብሊክ ፡ ደጋፊዎች ፡
ሲሆኑ ፡ ተወዳዳሪ ፡ የሌለው ፡ ደፋር ፡ እርምጃ ፡ የወ
ሰዱ ፡ ይመስላቸዋል ። እንደእውነቱ ፡ ከሆነ ፡ ግን ፡ መ
ንግሥት ፡ አንዱ ፡ መደብ ፡ ሌላውን ፡ መደብ ፡ የሚጨ
ቁንበት ፡ መኪና ፡ እንጂ ፡ ሌላ ፡ ሊሆን ፡ አይችልም ።
በእርግጥም ፡ ይህ ፡ በዴሞክራቲክ ፡ ሪፑብሊክም ፡ ቢሆ
ን ፡ ከዘውድ ፡ አገዛዝ ፡ ቅንጣት ፡ ታህል ፡ አያንስም ።
ወዝ ፡ አደሩ ፡ የመደብ ፡ የበላይነት ፡ ድልን ፡ በትግሉ ፡
ከተቀዳጀ ፡ በኋላ ፡ የሚወርሰው ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አለ ፡ ቢባ
ል ፡ መንግሥት ፡ ነው ። ድል ፡ የመታው ፡ ወዝ ፡ አደር ፤
ልክ ፡ እንደኮሙኑ ፡ ሁኖ ፡ የዚህ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አስ
ከፊ ፡ ጐኖችን ፡ በተቻለ ፡ ፍጥነት ፡ ቈርጦ ፡ ለመጣል ፡
ይገደዳል ። ይህም ፡ በአዲስና ፡ በነፃ ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡
ሁኔታዎች ፡ ያደገው ፡ ትውልድ ፡ ራሱ ፡ ጠቅላላውን ፡
የመንግሥቱን ፡ ቅራቅንቦ ፡ አሽቀንጥሮ ፡ ለመጣል ፡
እስኪችል ፡ ድረስ ፡ ነው ። »

ኤንግልስ ፡ የዘውድ ፡ አገዛዝ ፡ በሪፑብሊክ ፡ በሚተ
ካበት ፡ ጊዜ ፡ በአጠቃላይ ፡ የመንግሥትን ፡ ጥያቄ ፡ በሚመለ
ከት ፡ የሶሺያሊዝም ፡ መሠረታዊ ፡ ሀሳቦችን ፡ እንዳይረሱ ፡
ጀርመኖችን ፡ አስጠንቅቋል ። የኤንግልስ ፡ ማስጠንቀቂ
ያዎች « በጥምር » ተግባራቸው ፡ በመንግሥት ፡ ላይ ፡ መለ





ኮታዊ ፡ እምነታቸውንና ፡ መለኮታዊ ፡ አክብሮታቸውን ፡ ለገለፁ ፡ ለነጸረተሊዎችና ፡ ቼርኖቮች ፡ ዛሬ ፡ እንደትክክለኛ ፡ ሆነው ፡ ይነበባሉ!

ሁለት ፡ ተጨማሪ ፡ አስተያየቶች ፤

፩. በዴሞክራሲያዊ ፡ ሪፑብሊክም ፡ ቢሆን ፡ ከዘውድ ፡ አገዛዝ « ቅንጣት ፡ ታህል ፡ በማያንስ » ሁኔታ ፡ መንግሥት « አንዱ ፡ መደብ ፡ ሌላውን ፡ የሚጨቁንበት ፡ መኪና » ሆኖ ፡ ይቀራል ፡ የሚለው ፡ የኤንግልስ ፡ አስተያየት ፤ በምንም ፡ ዓይነት ፡ መንገድ ፡ ቢሆን ፤ አንዳንድ ፡ ሥርዓተ ፡ አልበኞች « እንደሚያስተምሩት » የጭቆናው ፡ ዓይነት ፡ ቅርፅ ፡ ለወዝ ፡ አደሩ ፡ ምንም ፡ ልዩነት ፡ አልነበረውም፡ ማለት ፡ አይደለም ። ሰፊ ፤ ነፃና ፡ ይበልጥ ፡ ግልፅ ፡ የሆነ ፡ የመደብ ፡ ትግልና ፡ የመደብ ፡ ጭቆና ፡ ቅርፅ ፡ ለወዝ ፡ አደሩ ፡ በአጠቃላይ ፡ መደቦችን ፡ ለማጥፋት ፡ በሚያደርገው ፡ ትግሉ ፡ በሰፊው ፡ ይረዳዋል ።

፪. ለምንድነው ፡ አዲሱ ፡ ትውልድ ፡ ብቻ ፡ ጠቅላላውን ፡ የመንግሥቱን ፡ ቅራቅንቦ ፡ አሽቀንጥሮ ፡ ለመጣል ፡ የሚችለው? — ይህ ፡ ጥያቄ ፡ አሁን ፡ ቀጥለን ፡ ከምንመለከተው ፡ የዴሞክራሲ ፡ መወጣት ፡ ጋር ፡ የተያያዘ ፡ ነው ።

### ፫. ኤንግልስ ፡ ስለየዴሞክራሲ ፡ መወጣት ።

ኤንግልስ ፡ በዚህ ፡ አርእስት ፡ ላይ ፡ አስተያየቱን ፡ ለመግለጽ ፡ የተነሳው « ሶሺያል-ዴሞክራት » የሚለው ፡ ቃል ፡ በሳይንሳዊ ፡ መንገድ ፡ ሲታይ ፡ ስህተት ፡ መሆኑን ፡ ስለተገነዘበ ፡ ነው ።

ኤንግልስ ፡ በ ፲፰፻፸ ኛዎቹ ፡ ዓ. ም. በልዩ ፡ ልዩ ፡ ርእሶች ፤ በብዛትም « በዓለም ፡ አቀፍ » ጥያቄዎች ፡ ላይ («Internationales aus dem «Volksstaat») ለጻፋቸው ፡ ጽሑፍ ፤ በጥር ፡ ፫ ፤ ፲፰፻፺፬ ዓ. ም. ፤ ማለትም ፡ ከመሞቱ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ተኩል ፡ በፊት ፤ በጻፈው ፡ መግቢያ ፡ እንዳለው ፡ በሁሉም ፡ ጽሑፎቹ ፡ ውስጥ ፡ የተጠቀመው « ኮሙኒስት » የሚለው ፡ ቃል ፡ እንጂ « ሶሺያል-ዴሞክራት » የሚለውን ፡ አይደለም ፤ ምክንያቱም ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ፕሩዶናውያን ፡[22] በፈረንሳይና ፡ ላሳልያኖች ፡[36] በጀርመን ፡ ራሳቸውን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ ብለው ፡ ይጠሩ ፡ ስለነበር ፡ ነው ።

« ... ስለዚህም ፡ ለማርክስና ፡ ለኔ » ይላል ፡ ኤንግልስ ፡ በመቀጠል « የኛን ፡ በጣም ፡ የተለየ ፡ ርዕዮተ ፡ ዓለም ፡ ባሕርይ ፡ ለማመልከት ፡ ይህን ፡ መሳይ ፡ ብዙ ፡ ትርጉም ፡ ያለውን ፡ ቃል ፡ መጠቀም ፡ ፍጹም ፡ አልተቻለንም ፡ ነበር ። ዛሬ ፡ ብዙ ፡ ነገሮች ፡ ተለውጠዋል ፤ ይህ (« ሶሺያል-ዴሞክራት ») የሚለው ፡ ቃል ፤ ምንም ፡ እንኳ ፡ አሁንም ፡ ቢሆን ፡ የኤኮኖሚ ፡ ፕሮግራሙ ፡ በአጠቃላይ ፡ እንድያው ፡ የሶሺያሊስት ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፤ ቀጥታ ፡ የኮሙኒስት ፡ ለሆነ ፤ የጠቅላላ ፡ መንግሥት ፡ መደምሰስ ፤ ማለት ፡ የዴሞክራሲም ፡ ማለፍ ፡ ፖለቲካዊ ፡ የመጨረሻ ፡ ዓላማው ፡ ለሆነ ፡ ፓርቲ — ትክክለኛ (unpassend) ባይሆንም ፡ ምናልባት ፡ ሊያገለግል ፡ ይችላል ። ሆኖም ፡ የእውነተኛ (ስርዝ ፡ የኤንግልስ) የፖለቲካ ፡ ፓርቲዎች ፡ ስሞች ፡ በጠቅላላው ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ ቢሆን ፡ ተስማሚ ፡ አይደሉም ፤ ምክንያቱም ፡ ፓርቲዎች ፡ ያድጋሉ ፤ ስሞች ፡ ግን ፡ እንዳሉ ፡ ይቀራሉ ። »

ዲያሌክቲካዊው ፡ ኤንግልስ ፡ እስከ ፡ እለተ ፡ ሞቱ ፡ ድረስ ፡ ለዲያሌክቲክስ ፡ እውነተኛ ፡ ሆኖ ፡ ኖሯል ። ማርክስና ፡ እኔ — ይላል ፡ ኤንግልስ — ለፓርቲው ፡ ግሩም ፡ ድንቅና ፡ በሳይንሳዊ ፡ መንገድ ፡ ትክክለኛ ፡ የሆነ ፡ ስም ፡ ነበረን ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እውነተኛ ፡ ፓርቲ ፤ ማለትም ፡ የሰ







ፊው ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ፓርቲ ፡ አልነበረም ። ዛሬ (በ ፲፱ ኛው ፡ ምእት ፡ ዓመት ፡ መጨረሻ) እውነተኛ ፡ ፓርቲ ፡ አለ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ስሙ ፡ በሳይንሳዊ ፡ መንገድ ፡ ትክክል ፡ አይደለም ። ፓርቲው ፡ በማደግ ፡ ላይ ፡ ከሆነ ፤ ስሙ ፡ በሳይንሳዊ ፡ መንገድ ፡ ትክክል ፡ አለመሆኑን ፡ ከፓርቲው ፡ እስካልተደበቀ ፡ ድረስና ፡ የፓርቲውን ፡ ትክክለኛ ፡ የእድገት ፡ አቅጣጫ ፡ እስካላደናቀፈ ፡ ድረስ « ያስኬዳል » ግድ ፡ የለም!

ምናልባት ፡ አንዱ ፡ ቀልደኛ ፡ እኛን ፡ ቦልሼቪኮችን ፡ በኤንግልሱ ፡ መንገድ ፡ በመጠቀም ፡ ሊያፅናናን ፡ ይሞክር ፡ ይሆናል ፤ እውነተኛ ፡ የሆነ ፡ ፓርቲ ፡ አለን ፤ በሚያስደንቅ ፡ ሁኔታም ፡ እያደገ ፡ ነው ፤ « ቦልሼቪክን » የመሰለ ፡ ትርጉም ፡ የሌለውና ፡ ጐደሎ ፡ ቃልም « ያስኬዳል » ፤ ይህ ፡ ቃል ፡ ምንም ፡ ነገር ፡ አይገልጽም ፤ ፍጹም ፡ አጋጣሚ ፡ ከሆነው ፡ ነገር ፡ በ ፲፱፻፫ ዓ. ም. በብሩሴልስ - ሎንደን ፡ በተደረገው ፡ ጉባዔ ፡ አብዛኞቻችን ፡[37] ነበርን ፡ እንጂ … ምናልባትም ፡ አሁን ፡ የፓርቲአችን ፡ በሪፑብሊካኖችና ፡ በንኡስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ጮርቃ « አብዮታውያን » ዴሞክራቶች ፡ በሐምሌና ፡ በነሀሴ ፡ መሳደድ ፡ የተነሳ « ቦልሼቪክ » የሚለው ፡ ቃል ፡ እንደዚያ ፡ የመላውን ፡ ሕዝብ ፡ አክብሮት ፡ ባገኘበት ፤ ምናልባትም ፡ አሁን ፡ ይህ ፡ ማሳደድ ፡ ፓርቲአችን ፡ በእውነተኛ ፡ እድገቱ ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ታሪካዊ ፡ እርምጃ ፡ መደረጉን ፡ በተጨማሪ ፡ በሚመሰክርበት ፤ ምናልባት ፡ አሁን ፡ እኔም ፡ ብሆን ፡ በሚያዝያ ፡ ወር ፡ የፓርቲአችን ፡ ስም ፡ እንዲለወጥ ፡ ብዬ ፡ ያቀረብኩትን ፡ ሃሳብ ፡ ወደኋላ ፡ ለመጐተት ፡ ባቅማማሁኝ ፡ ነበር ። ሆኖም ፡ ምናልባት « ማስታረቂያ » ለጓዶቼ ፡ አቀርብ ፡ ነበር ፤ ይኸውም ፡ የኮሙኒስት ፡ ፓርቲ ፡ ተብለን ፡ እንድንጠራና ፤ በቅንፍ ፡ ውስጥ ፡ ቦልሼቪክ ፡ የሚለውን ፡ ቃል ፡ ማስቀመጥ …

ይሁን ፡ እንጂ ፡ የፓርቲው ፡ ስም ፡ ጥያቄ ፡ አብዮታዊው ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ በመንግሥት ፡ ጥያቄ ፡ ላይ ፡ ካለ



ው ፡ አቋም ፡ ጋር ፡ የማይወዳደር ፡ አነስ ፡ ያለ ፡ ጥያቄ ፡ ነው ።

ዘወትር ፡ በመንግሥት ፡ ጥያቄ ፡ ላይ ፡ ክርክር ፡ ሲደረግ ፡ ሁልጊዜ ፡ የሚፈፀመው ፡ ስህተት ፡ በዛ ፡ ኤንግልስ ፡ ማስጠንቀቂያ ፡ በሰጠበትና ፤ እኛም ፡ እግረ ፡ መንገዳችን ፡ ከፍ ፡ ብለን ፡ በጠቀስነው ፡ ላይ ፡ ነው ። ይኸውም ፤ የመንግሥት ፡ መደምሰስ ፡ ማለት ፡ የዴሞክራሲ ፡ መደምሰስ ፡ ማለት፡ መሆኑን ፤ የመንግሥት ፡ መክሰም ፡ ማለት ፡ የዴሞክራሲ ፡ መክሰም ፡ ማለት ፡ መሆኑን ፡ ሁልጊዜ ፡ ስለሚረሳ ፡ ነው ።

በመጀመሪያ ፡ ገፅታው ፡ ሲታይ ፡ ይህ ፡ አባባል ፡ በጣም ፡ እንግዳና ፡ የማይገባ ፡ ይመስላል ፤ በእርግጥም ፡ አንዳንዱ ፡ ሰው ፡ ጥቂቶቹ ፡ ለአብዛኞቹ ፡ መታዘዝ ፡ አለባቸው ፡ የሚለው ፡ መርህ ፡ የማይጠበቅበት ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ሥርዓት ፡ መምጣቱ ፡ ነው? ብሎ ፡ ይጠራጠር ፡ ይሆናል ፤ ምክንያቱም ፡ ዴሞክራሲ ፡ ማለት ፡ ይህ ፡ መርህ ፡ ማወቅ ፡ ማለት ፡ ነውና ።

አይደለም ። ዴሞክራሲ ፡ ማለት ፡ ጥቂቶቹ ፡ ለአብዛኞቹ ፡ መታዘዝ ፡ አለባቸው ፡ ከሚለው ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ ዓይነት ፡ አይደለም ። ዴሞክራሲ ፡ ማለት ፡ የጥቂቶቹ ፡ ለአብዛኞቹ ፡ መታዘዝ ፡ የሚያውቅ ፡ መንግሥት ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ማለትም ፡ አንዱ ፡ መደብ ፡ በሌላው ፡ መደብ ፡ ላይ ፤ አንዱ ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ክፍል ፡ በሌላው ፡ ክፍል ፡ ላይ ፡ የተቀነባበረ ፡ ጭቆና ፡ ለመጠቀም ፡ የሚያገለግል ፡ ድርጅት ፡ ማለት ፡ ነው ።

እኛ ፡ የግባችን ፡ የመጨረሻ ፡ ዋና ፡ ዓላማ ፡ መንግሥትን ፤ ማለትም ፡ ሁሉንም ፡ የተደራጀና ፡ የተቀነባበረ ፡ ጭቆናን ፤ ሁሉንም ፡ በህዝብ ፡ ላይ ፡ የሚጠቀሙት ፡ ጭቆናን ፡ በአጠቃላይ ፡ ለማጥፋት ፡ ነው ። ጥቂቶቹ ፡ ለአብዛኞቹ ፡ የመታዘዝን ፡ መርህ ፡ የማይጠብቅበት ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ሥርዓት ፡ ይመጣል ፡ ብለን ፡ አንጠብቅም ። ይሁን ፡ እንጂ ፡ ለሶሺያሊዝም ፡ ስንጥር ፡ ይህ ፡ ወደኮሙኒዝም ፡

እንደሚያድግ ፡ እናምናለን ፤ ከዚህም ፡ የተነሳ ፡ በሰዎች ፡ ላይ ፡ የሚደረገው ፡ ጭቆና ፡ በአጠቃላይ ፡ አስፈላጊነቱ ፡ ይጠፋል ፤ አንድ ፡ ሰው ፡ በሌላው ፤ አንዱ ፡ የኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ክፍል ፡ በሌላው ፡ ክፍል ፡ መታዘዝም ፡ ይቀራል ፤ ምክንያቱም ፡ ሰዎች ፡ ያለ ፡ ኃይልና ፡ ያለ ፡ ትእዛዝ ፡ መሠረታዊ ፡ የሆኑ ፡ የኑሮ ፡ ሁኔታዎችን ፡ አክብረው ፡ መጠበቅን ፡ ስለሚለምዱ ፡ ነው ።

ይህንን ፡ መሠረታዊ ፡ ልምድን ፡ በአፅንኦት ፡ ለመጥቀስ ፡ ነው ፡ ኤንግልስ « በአዲስና ፡ በነፃ ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ሁኔታዎች ፡ ስላደገው ፤ የመንግሥቱን » — የማንኛውንም ፡ ዓይነት ፡ መንግሥትነት ፤ የዴሞክራሲያዊ ፡ ሪፑብሊክ ፡ መንግሥትም ፡ ጭምር — « ጠቅላላ ፡ ቅራቅንቦ ፡ አሽቀንጥሮ ፡ ስለሚጥለው »ስለአዲሱ ፡ ትውልድ ፡ የሚናገረው ።

ይህንን ፡ ለማስረዳት ፡ የመንግሥትን ፡ መክሰም ፡ ኤኮኖሚያዊ ፡ መሠረቶችን ፡ ጥያቄ ፡ መመርመር ፡ አስፈላጊ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ V.

## የመንግሥት ፡ መክሰም ፡ ኤኮኖሚያዊ ፡ መሠረቶች ።

ለዚህ ፡ ጥያቄ ፡ በጣም ፡ ጥልቅ ፡ የሆነ ፡ ገለፃ ፡ የሰጠው « በጎታ ፡ ፕሮግራም ፡ ሂሱ » ማርክስ ፡ ነው ። (ግንቦት ፭ ፤ ፲፰፻፸፭ ዓ. ም. ለብራኬ ፡ የተላከው ፡ ደብዳቤ ፤ በ ፲፰፻፺፩ ዓ. ም. በ «Neue Zeit» IX ፤ ቁ. ፩ ከመጸፉ ፡ በፊት ፡ የትም ፡ አልታተመም ፡ ነበር ። በሩሲያንኛ ፡ ቋንቋ ፡ በልዩ ፡ እትም ፡ ወጥቷል ።) በዚህ ፡ ግሩም ፡ ድርሰት ፡ ውስጥ ፡ ያለው ፡ የላሳልያዊነት ፡ ሂስ ፡ ክርክር ፡ ክፍል ፡ ጠቃሚውን ፡ ክፍል ፤ ማለት ፡ በኮሙኒዝም ፡ እድገትና ፡ በመንግሥት ፡ መክሰም ፡ መካከል ፡ ያለውን ፡ የግንኙነት ፡ ትንተና ፡ ሸፍኖታል ።



### ፩. ጥያቄውን ፡ ማርክስ ፡ እንዳቀረበው ።

ግንቦት ፡ ፭ ፤ ፲፰፻፸፭ ዓ. ም. ማርክስ ፡ ለብራኬ ፡ የላከው ፡ ደብዳቤና ፡ ከላይ ፡ ያየነው ፡ መጋቢት ፡ ፳፰ ፤ ፲፰፻፸፭ ዓ. ም. ኤንግልስ ፡ ለቤቤል ፡ ከጻፈው ፡ ደብዳቤ ፡ ጋር ፡ ላይ ፡ ላዩን ፡ ብናነፃፅራቸው ፡ ማርክስ ፡ ከኤንግልስ ፡ ይበልጥ ፡ ላቅ ፡ ባለ « የመንግሥት ፡ ዋነኛ » ሊመስል ፡ ይችላል ። እንደዚሁም ፡ በሁለቱ ፡ ጸሐፊዎች ፡ መካከል ፡ በመንግሥት ፡ ጥያቄ ፡ ላይ ፡ ያለው ፡ የአስተያየት ፡ ልዩነትም ፡ በጣም ፡ ጉልህ ፡ መስሎ ፡ ሊታይ ፡ ይችላል ።

ኤንግልስ ፡ ለቤቤል ፡ ሲጽፍ ፡ ስለመንግሥት ፡ ያለው ፡ አሉባልታ ፡ በሙሉ ፡ እንዲጣል ፤ መንግሥት ፡ የሚለው ፡ ቃል ፡ ጭራሹም ፡ ከፕሮግራሙ ፡ እንዲፋቅና « ኮሚዩኒቲ » በሚል ፡ ቃል ፡ እንዲተካ ፡ ሀሳብ ፡ አቀረበ ። በቃሉ ፡ ትክክለኛ ፡ ፍች ፡ መሠረት ፡ ኮሙኑ ፡ መንግሥት ፡ እንዳልነበረ ፡ እንኳ ፡ ኤንግልስ ፡ አስታውቋል ። ማርክስም ፡ በበኩሉ « ስለወደፊቱ ፡ የኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ መንግሥት » ተናግሯል ፤ ይኸውም ፡ በኮሙኒስት ፡ ሥርዓትም ፡ እንኳን ፡ ቢሆን ፡ መንግሥት ፡ አስፈላጊ ፡ ነው ፡ ያለ ፡ ይመስላል ።

ሆኖም ፡ የዚህ ፡ ዓይነቱ ፡ አስተያየት ፡ በመሠረቱ ፡ ስህተተኛ ፡ ነው ። ጠልቀን ፡ ብንመረምር ፡ ግን ፡ ማርክስና ፡ ኤንግልስ ፡ በመንግሥትና ፡ በመንግሥት ፡ መክሰም ፡ ላይ ፡ ያላቸው ፡ አስተያየቶች ፡ ፍጹም ፡ አንድ ፡ ናቸው ፤ ከላይ ፡ የተጠቀሰው ፡ የማርክስ ፡ ጥቅስ ፡ የሚመለከተው ፡ በመክሰም ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ መንግሥት ፡ ነው ።

እርግጥ ፡ ነው ፡ የወደፊቱን « የመክሰም » ጊዜን ፡ ለመወሰን ፡ ጥያቄ ፡ ሊነሳ ፡ አይቻልም ፤ ምክንያቱም ፡ ይህ ፡ ረጅም ፡ ሂደት ፡ እንደሚሆን ፡ የታወቀ ፡ ነውና ። በማርክስና ፡ በኤንግልስ ፡ መካከል ፡ ልዩነት ፡ አለ ፡ ቢባል ፡ በተለያዩ ፡ ርእሶች ፡ ላይ ፡ በመሥራታቸውና ፡ በተለያዩ ፡

ዓላማዎች ፡ ስለጸፉ ፡ ነው ። ኤንግልስ ፡ ከፊቱ ፡ ያስቀመ ጠው ፡ ተግባር ፡ መንግሥትን ፡ በሚመለከት ፡ በጊዜው ፡ የነበረውን ፡ የማይረባ ፡ አጉል ፡ እምነት ፡ በሙሉ ፡ ለቤ ቤል ፤ (ባላነሰ ፡ መጠን ፡ የሀሳቡ ፡ ተካፋይ ፡ ለሆነው ፡ ላሳሌም ) ግልፅ ፤ ጥልቅና ፡ ሰፊ ፡ በሆነ ፡ አኳኋን ፡ ማሳየ ትን ፡ ነበር ። ማርክስ ፡ ግን ፡ እግረ ፡ መንገዱን ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ <u>ይህን</u> ፡ ጥያቄ ፡ የሚነካው ፤ ያተኮረው ፡ በሌላ ፡ ርእስ — በኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ እድገት ፡ ላይ ፡ ነበር ።

ጠቅላላ ፡ የማርክስ ፡ ቴዎሪ ፤ ፍጹም ፡ ባልተዛነፈ ፤ በጣም ፡ በተሟላ ፤ በተመረመረና ፡ ይዘተ ፡ ብዙ ፡ በሆነው ፡ ቅርፁ ፡ የሚያተኩረው ፡ የእድገትን ፡ ቴዎሪ ፡ በዘመናዊ ው ፡ ካፒታሊዝም ፡ ላይ ፡ መጠቀም ፡ ነው ። እርግጥ ፡ ነው ፤ በማርክስ ፡ ፊት ፡ የተደቀነው ፡ ጥያቄ ፡ ይህን ፡ ቴዎሪ ፡ በሁለቱም ፤ <u>በሚመጣው</u> ፡ የካፒታሊዝም ፡ ድቀት ፡ <u>በወ ደፊቱ</u> ፡ ኮሙኒዝም ፡ <u>የወደፊት</u> ፡ እድገት ፡ በሥራ ፡ ላይ ፡ ማዋልን ፡ ነበር ።

ይሁንና ፡ በምን ፡ <u>ጭብጥ ፡ ሀቆች</u> ፡ ላይ ፡ ተመሥርቶ ፡ ነው ፡ የወደፊቱን ፡ ኮሙኒዝም ፡ የወደፊት ፡ እድገት ፡ ጥያ ቄ ፡ ማቅረብ ፡ የሚቻለው?

በመሠረቱ ፡ <u>ምንጩ</u> ፡ ካፒታሊዝም ፡ ሆኖ ፡ በታሪክ ፡ ከካፒታሊዝም ፡ ያድጋል ፤ የሚመሠረተውም ፡ ካፒታሊ ዝም ፡ <u>በወለደው</u> ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ኃይል ፡ የተግባር ፡ ውጤት ፡ ላይ ፡ ነው ። ማርክስ ፡ ሊታወቅ ፡ በማይቻለው ን ፡ በባዶ ፡ የግምት ፡ ሥራ ፡ መላ ፡ ለመምታትም ፡ ሆነ ፡ ተምኔታዊነትን ፡ ለመድረስ ፡ የመሞከሩ ፡ ምንም ፡ ምልክት ፡ የለም ። አንድ ፡ የስነ ፡ ፍጥረት ፡ ተመራማሪ ፤ ለምሳሌ ፤ አዲስ ፡ የባዮሎጂያዊ ፡ ፍጥረት ፡ አመጣጡ ፡ እንዴት ፤ በምን ፡ መንገድ ፡ እንደነበርና ፡ በምን ፡ ዓይነት ፡ የተወ ሰነ ፡ አቅጣጫ ፡ እንደሚለዋወጥ ፡ ካወቀ ፡ የእድገቱን ፡ ጥያቄ ፡ ለመመርመር ፡ እንደሚችለው ፡ ሁሉ ፡ ማርክስም ፡



የኮሙኒዝም ፡ ጥያቄ ፡ የመረመረው ፡ በተመሳሳይ ፡ መንገድ ፡ ነው ።

ከሁሉ ፡ አስቀድሞ ፡ ማርክስ ፡ የጎታ ፡ ፕሮግራም ፡ ያመጣውን ፡ በመንግሥትና ፡ በኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ መካከል ፡ ያለውን ፡ ጥያቄ ፡ ውዥንብርን ፡ ወደ ፡ ጎን ፡ ይጥላል ። እንዲህ ፡ ሲልም ፡ ይጽፋል ፤

«... ዘመናዊው ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፤ በሁሉም ፡ በሠለ ጠኑት ፡ አገሮች ፤ በዛም ፡ አነሰ ፡ ከመካከለኛው ፡ ዘመን ፡ ቅይጥነት ፡ ነፃ ፡ በሆኑ ፤ በዛም ፡ አነሰ ፡ በእያንዳንዱ ፡ አገር ፡ የተለየ ፡ ታሪካዊ ፡ እድገት ፡ ምክንያት ፡ መጠ ነኛ ፡ ለውጥ ፡ በተካሄደባቸው ፤ በዛም ፡ አነሰ ፡ ባደ ጉት ፡ አገሮች ፡ ያደጉ ፡ የካፒታሊስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ነው ። በሌላ ፡ በኩል « ዘመናዊው ፡ መንግሥት » ከመንግ ሥታዊ ፡ ድምበር ፡ ጋር ፡ ይለዋወጣል ። የፕሩስ - ጀር መን ፡ ንጉሣዊ ፡ ግዛት ፡ በስዊዘርላንድ ፡ ካለው ፡ የተ ለየ ፡ ነው ፤ እንደዚሁም ፡ በተባበሩት ፡ የአሜሪካ ፡ ክ ፍለ ፡ ግዛቶች ፡ ያለው ፡ በእንግሊዝ ፡ ካለው ፡ የተለየ ፡ ነው ። ስለዚህም « የአሁኑ ፡ መንግሥት » ልበ ፡ ወለድ ፡ ነው ።

ይሁን ፡ እንጂ ፡ በተለያዩ ፡ የሰለጠኑ ፡ አገሮች ፡ ያሉት ፡ የተለያዩ ፡ መንግሥታት ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ በቅር ፃቸው ፡ በብዙ ፡ ቢለያዩም ፡ ሁሉም ፡ አንድ ፡ የጋራ ፡ ባህርይ ፡ አላቸው ፤ ይኸውም ፡ የሚመሠረቱት ፤ በ ዛም ፡ አነሰ ፤ ባደገ ፡ ካፒታሊስታዊ ፤ ዘመናዊ ፡ በሆነ ፡ የቡርዥዋ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ነው ። ስለዚህም ፡ የተወሰ ኑ ፡ ዋና ፡ ዋናዎቹ ፡ የጋራ ፡ ጠባዮች ፡ አሏቸው ። በዚህ ፡ ረገድ « የአሁኑ ፡ መንግሥት » ከጠፊው ፡ የዛሬ ፡ የ ቡርዥዋ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ከሚመሠረተው ፡ ከወደፊቱ ፡ መንግሥት ፡ ጋር ፡ በማነፃፀር ፡ ለመናገር ፡ ይቻላል ።

ከዛም ፤ መንግሥት ፡ በኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡





ምን ፡ ዓይነት ፡ ሽግግርን ፡ ያልፋል? የሚለው ፡ ጥያቄ ፡ ይነሳል ። በሌላ ፡ አነጋገር ፤ የአሁኑን ፡ የመንግሥት ፡ ተግባሮች ፡ የሚመስሉ ፡ ምን ፡ ዓይነት ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ተግባሮች ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ይቀራሉ? ለዚህ ፡ ጥያቄ ፡ መልስ ፡ መስጠት ፡ የሚቻለው ፡ ሳይንሳዊ ፡ በሆነ ፡ መንገድ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ ስለሆነም « ሕዝብ » የሚለው ፡ ቃል « መንግሥት » ከሚለው ፡ ቃል ፡ ጋር ፡ ሺህ ፡ ጊዜ ፡ ቢያወሳስቡት ፡ ወደ ፡ መፍትሄው ፡ ትንጣት ፡ ታህል ፡ ሊያስጠጋው ፡ አይችልም ። »

በዚህ ፡ አኳኋን ፡ ስለ « ሕዝባዊ ፡ መንግሥት » ያለው ፡ ሁሉንም ፡ ንግግር ፡ መሳለቂያ ፡ ካደረገ ፡ በኋላ ፤ ማርክስ ፡ ጥያቄውን ፡ እንዳለ ፡ ያቀርብና ፡ ለጥያቄው ፡ ሳይንሳዊ ፡ መልስ ፡ ለማግኘት ፡ የሚቻለው ፡ ጥብቅ ፡ ሆነው ፡ በተመሠረቱ ፡ ሳይንሳዊ ፡ ጭብጥ ፡ ሀቆች ፡ ላይ ፡ በመመርኮዝ ፡ ብቻ ፡ እንደሆነ ፡ ያስጠነቅቃል ።

አንድ ፡ በጠቅላላው ፡ የእድገት ፡ ቴዎሪ ፤ በአጠቃላይም ፡ ሳይንስ ፤ ይበልጥ ፡ የተረጋገጠ ፡ ሀቅ ፡ አለ — ይህን ፡ ሀቅ ፡ ተምኔታውያን ፡ ረስተውታል ፤ የዛሬዎቹ ፡ አድርባዮች ፡ ሶሺያሊስት ፡ አብዮትን ፡ በመፍራት ፡ ትተውታል — ይህም ፡ በታሪክ ፡ ከካፒታሊዝም ፡ ወደ ፡ ኮሙኒዝም ፡ ለማለፍ ፡ ያለ ፡ ጥርጥር ፡ የተለየ ፡ የሽግግር ፡ ደረጃ ፡ ወይም ፡ ጊዜ ፡ መኖር ፡ እንዳለበት ፡ ነው ።

## ፪. ከካፒታሊዝም ፡ ወደ ፡ ኮሙኒዝም ፡ ሽግግር ።

ማርክስ ፡ በመቀጠል ፤ « ... በካፒታሊስትና ፡ በኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰቦች ፡ መካከል ፡ አንዱ ፡ ወደ ፡ ሌላው ፡ የሚሸጋገርበት ፡ አብዮታዊ ፡ የሽግግር ፡ ጊዜ ፡ አለ ። ይህን ፡ የሚያንፀባርቅ ፡ ደግሞ ፡ ፖለቲ



ካዊ ፡ የሽግግር ፡ ጊዜ ፡ ደግ[illegible] ፡ የዚህ ፡ ጊዜ፡ መንግሥት ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮታዊ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ ብቻ ፡ እንጂ ፡ ሌላ ፡ ሊሆን ፡ አይችልም ።... »

ይህ ፡ የማርክስ ፡ መደምደምያ ፡ የሚመሠረተው ፡ በዘመናዊው ፡ ካፒታሊስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ውስጥ ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ በተጫወተው ፡ ሚና ፤ የዚህን ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ እድገት ፡ በሚመለከቱ ፡ ጭብጥ ፡ ሐቆችና ፤ በወዝ ፡ አደሩና ፡ በቡርዥዋው ፡ መካከል ፡ ባሉት ፡ የማይታረቁ ፡ ተፃራሪ ፡ ጥቅሞች ፡ ትንተናዎች ፡ ላይ ፡ ነው ።

ካሁን ፡ በፊት ፡ ጥያቄው ፡ የቀረበው ፡ በሚከተለው ፡ አኳኋን ፡ ነበር ፤ ወዝ ፡ አደሩ ፡ ነፃነቱን ፡ እንዲጐናፀፍ ፡ ቡርዥዋውን ፡ ገልብጦ ፡ የፖለቲካ ፡ ሥልጣኑን ፡ መጨበጥና ፡ የራሱን ፡ አብዮታዊ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ መመሥረት ፡ አለበት ፡ ነበር ።

አሁን ፡ ግን ፡ ጥያቄው ፡ የቀረበው ፡ ትንሽ ፡ ለየት ፡ ባለ ፡ አኳኋን ፡ ነው — ወደኮሙኒዝም ፡ በማደግ ፡ ላይ ፡ ካለው ፡ ከካፒታሊስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ወደ ፡ ኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ለመሸጋገር ፡ ያለ « ፖለቲካዊ ፡ የሽግግር ፡ ጊዜ » አይቻልም ፤ በዚህም ፡ ጊዜ ፡ መንግሥቱ ፡ ሊሆን ፡ የሚችለው ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮታዊ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት፡ ብቻ ፡ ነው ።

ይሁንና ፡ ይህ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ ከዴሞክራሲ ፡ ጋር ፡ ያለው ፡ ዝምድና ፡ ምንድን ፡ ነው?

« የኮሙኒስት ፡ ማኒፌስቶ » « ወዝ ፡ አደሩን ፡ እስከ ፡ ገዢ ፡ መደብ ፡ ደረጃ ፡ ድረስ ፡ ከፍ ፡ ማድረግ » እና « ዴሞክራሲን ፡ መጐናፀፍ » የሚሉትን ፡ ሁለት ፡ ፅንሰ ፡ ሀሳቦችን ፡ እንድያው ፡ ጐን ፡ ለጐን ፡ እንዳስቀመጣቸው ፡ ተመልክተናል ። ከላይ ፡ በተዘረዘረው ፡ ሁሉ ፡ መሠረት ፡ ከካፒታሊዝም ፡ ወደ ፡ ኮሙኒዝም ፡ ባለው ፡ የሽግግር ፡ ጊዜ ፡ ዴሞክራሲ ፡ እንዴት ፡ እንደሚለወጥ ፡ ይበልጥ ፡ በትክክል ፡ ለመወሰን ፡ ይቻላል ።

በካፒታሊስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፤ እጅግ ፡ በጣም ፡ አመቺ ፡ በሆኑ ፡ ሁኔታዎች ፡ በማደግ ፡ ላይ ፡ ከሆነ ፤ በዴሞክራሲያዊው ፡ ሪፑብሊክ ፡ በዛም ፡ አነሰ ፡ ሙሉ ፡ ዴሞክራሲ ፡ አለን ። ይሁን ፡ እንጂ ፤ ይህ ፡ ዴሞክራሲ ፡ በካፒታሊስታዊ ፡ ብዝበዛ ፡ ጠባብ ፡ አጥሮች ፡ የተገደበ ፡ ነው ፤ ስለዚህም ፡ በመሠረቱ ፡ ሁልጊዜ ፡ ዴሞክራሲ ፡ ለጥቂቶች ፤ ሀብት ፡ ላላቸው ፡ መደቦች ፡ ብቻ ፤ ለሃብታሞች ፡ ብቻ ፡ ሆኖ ፡ ይቀራል ። በካፒታሊስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ነፃነት ፡ ሁልጊዜ ፡ በጥንት ፡ የግሪክ ፡ ሪፑብሊኮች ፡ እንደነበረው ፡ ዓይነት ፤ ነፃነት ፡ ለባሪያ ፡ ጌቶች ፡ ሆኖ ፡ ይቀራል ። በካፒታሊስት ፡ የብዝበዛ ፡ ሁኔታዎች ፡ ምክንያት ፡ የዘመኑ ፡ ቅጥር ፡ ባሪያዎች ፡ በእጦትና ፡ በችግር ፡ በጣም ፡ በመደቈሳቸው « ለዴሞክራሲ ፡ ግድ ፡ የላቸውም » ፤ « ለፖለቲካ ፡ ግድ ፡ የላቸውም » ፤ በተለመደው ፡ የሁኔታዎች ፡ ሰላማዊ ፡ እድገት ፡ አብዛኛው ፡ ሕዝብ ፡ በኅብረተ ፡ ሰብአዊ ፡ የፖለቲካ ፡ ህይወት ፡ እንዳይካፈል ፡ ይወገዳል ።

የዚህ ፡ አስተያየት ፡ ትክክለኛነት ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ግልፅ ፡ በሆነ ፡ ሁኔታ ፡ በጀርመን ፡ ሊረጋገጥ ፡ ይችላል ፤ ምክንያቱም ፡ በዚህ ፡ መንግሥት ፡ ውስጥ ፡ ደምብ ፡ በወጣለት ፡ ህጋዊነት ፡ በሚያስገርም ፡ አኳኋን ፡ ለረጅም ፡ ጊዜ ፡ ሳይናወፅ ፤ ለግማሽ ፡ ምእት ፡ ዓመት ፡ ያህል (ከ ፲፰፻፸፰ እስከ ፡ ፲፱፻፲፬ ዓ. ም.) ችሎ ፡ ቆይቷል ። በዚህ ፡ ጊዜ ፡ ውስጥም ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ ከሌሎች ፡ አገሮች ፡ በበለጠ « ህጋዊነትን ፡ ለመጠቀም » ችለዋል ፤ በዓለም ፡ የትም ፡ ከተደረገው ፡ በበለጠም ፤ አብዛኛውን ፡ የወዝ ፡ አደሮች ፡ ክፍል ፡ ወደ ፡ ፖለቲካ ፡ ፓርቲ ፡ አደራጅተዋል ።

እስከ ፡ አሁን ፡ በካፒታሊስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ከታዩት ፡ ይህ ፡ በፖለቲካ ፡ የነቃና ፡ ትጉህ ፡ የቅጥር ፡ ባሪያ ፡ ከፍተኛ ፡ ብዛቱ ፡ ምን ፡ ያህል ፡ ይሆናል? ከአሥራ ፡ አምስት ፡ ሚሊዮን ፡ ቅጥር ፡ ሠራተኞች ፡ አንዱ ፡ ሚሊዮን ፡ የሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ ፓርቲ ፡ አባል ፡ ነው! ከአሥራ ፡ አምስት ፡ ሚሊዮን ፡ ሶስቱ ፡ በሠራተኞች [illegible] ተደራጅተዋል!



ዴሞክራሲ ፡ በጣት ፡ ለሚቆጠሩ ፡ ጥቂቶች ፤ ዴሞክራሲ ፡ ለሀብታሞች — ይህ ፡ ነው ፡ የካፒታሊስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ዴሞክራሲ ። የካፒታሊስታዊ ፡ ዴሞክራሲን ፡ አሠራር ፡ ጠጋ ፡ ብለን ፡ ብንመለከት ፤ በሁሉም « በጠቃቅን » — ጠቃቅን ፡ በሚመስሉ ፤ — የምርጫ ፡ መብት ፡ ዝርዝሮች (የነዋሪነት ፡ ደረጃን ፤ ሴቶች ፡ ማግለልን ፤ ወዘተ) ፤ በውክልና ፡ ተቋሞች ፡ ዘዴ ፤ በመሰብሰብ ፡ መብት ፡ ላይ ፡ የሚደረጉት ፡ ጉልህ ፡ እንቅፋቶች (ሕዝባዊ ፡ ሕንፃዎች « ለለማኞች » አይደሉም!) ፤ እለታዊ ፡ ጋዜጣዎች ፡ ፍጹም ፡ ካፒታሊስታዊ ፡ በሆነ ፡ መንገድ ፡ ማዘጋጀት ፤ ወዘተ ፤ ወዘተ ፤ በዴሞክራሲ ፡ ላይ ፡ ገደብ ፡ በገደብ ፡ ላይ ፡ ሲግተለተል ፡ እናያለን ። እነዚህ ፡ ለድሆች ፡ የሚደረጉ ፡ ገደቦች ፤ አድልዎዎች ፤ ማግለሎችና ፡ እንቅፋቶች ፡ ቀላል ፡ ይመስላሉ ፤ በተለይም ፡ ራሱ ፡ ጭንቅን ፡ በፍጹም ፡ ባልቀመሰና ፡ የጭቁን ፡ መደቦችን ፡ ጠቅላላ ፡ ኑሮ ፡ ጠጋ ፡ ብሎ ፡ በፍጹም ፡ አይቶ ፡ በማያውቀው ፡ ሰው ፡ ዓይን (ከመቶ ፡ ዘጠና ፡ ዘጠኙ ፡ እጅ ፡ ካልሆነ ፤ ከአሥሩ ፡ ዘጠኙ ፡ እጅ ፡ የሚሆኑት ፡ የቡርዥዋ ፡ ጸሐፊዎችና ፡ የፖለቲካ ፡ ሰዎች ፡ የዚህ ፡ ዓይነቱ ፡ ናቸው) ፤ ስለሆነም ፡ በድምሩ ፡ ሲወሰድ ፡ እነዚህ ፡ ገደቦች ፡ ድሀውን ፡ ከፖለቲካ ፤ በዴሞክራሲ ፡ ውስጥ ፡ ነቃ ፡ ብሎ ፡ ከመካፈል ፡ ያገልላሉ ፤ ይገፈትራሉም ።

ማርክስ ፡ ይህንን ፡ የካፒታሊስት ፡ ዴሞክራሲ ፡ ውስጠ ፡ ነገር ፡ በደምብ ፡ ስለተረዳ ፤ የኮሙንን ፡ ልምድ ፡ ሲተነትን ፤ ለጭቁኖች ፡ በጥቂት ፡ ዓመታት ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ከጨቋኙ ፡ መደብ ፡ የትኞቹ ፡ ተወካዮች ፡ በፓርላማ ፡ እንደሚወክሏቸውና ፡ እንደሚጨቁኗቸው ፡ ለመወሰን ፡ ይፈቀድላቸዋል! ብሏል ።[38]

ነገር ፡ ግን ፡ በዚህ ፡ በማይቀር ፡ ጠባብ ፡በሆነውና ፡ ድሀውን ፡ በድብቅ ፡ አሽቀንጥሮ ፡ በሚቀጥለው ፤ ስለዚህም ፡

ሁለመናው ፡ በሸርና ፡ በውሸት ፡ በተጥለቀለቀው ፡ በካፒታሊስት ፡ ዴሞክራሲ ፤ ሊበራል ፡ ፕሮፌሰሮችና ፡ የንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ አድርባዮች ፡ ሊያሳምኑን ፡ እንደሚፈልጉት ፤ እድገቱ ፡ ቀላል ፤ ቀጥታና ፡ ትክክል ፡ በሆነ ፡ መንገድ ፡ አይሄድም ፤ « ይበልጥ ፡ ትልቅና ፡ ሙሉ ፡ ወደሆነ ፡ ዴሞክራሲ » አይወስድም ። የለም ። እድገቱ ፤ ማለት ፡ ወደኮሙኒዝም ፡ የሚካሄደው ፡ እድገት ፡ በወዝ ፡ አደሩ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ አማካይነት ፡ እንጂ ፤ በሌላ ፡ መንገድ ፡ አይቻልም ፤ ምክንያቱም ፡ የበዝባዦች ፡ ካፒታሊስቶች ፡ ተቃውሞን ፡ ለመሰባበር ፡ ሌላ ፡ ማንም ፡ አይችልም ፤ ሌላ ፡ አማራጭ ፡ መንገድም ፡ የለም ።

ስለሆነም ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ ማለትም ፡ ጨቋኞችን ፡ ለመደቆስ ፤ የጭቁኖች ፡ ግምባር ፡ ቀደም ፡ እንደ ፡ ገዢ ፡ መደብ ፡ የተደራጀበት ፡ ድርጅት ፤ ዴሞክራሲን ፡ በማስፋፋት ፡ ብቻ ፡ ሊወሰን ፡ አይችልም ። ከዴሞክራሲ ፡ ታላቅ ፡ መስፋፋት ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ ላይ ፤ ለመጀመሪያ ፡ ጊዜ ፡ ዴሞክራሲ ፡ ለድሆች ፤ ዴሞክራሲ ፡ ለሕዝብ ፡ ሰጥቶ ፤ ለባለሀብቶች ፡ በመንፈግ ፤ የወዝ ፡ አደሩ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ በጨቋኞች ፡ በበዝባዦች ፤ በካፒታሊስቶች ፡ ነፃነት ፡ ላይ ፡ ተከታታይ ፡ ገደቦችን ፡ ያበጃል ። የሰውን ፡ ዘር ፡ ከቅጥር ፡ ባርነት ፡ ነፃ ፡ ለማውጣት ፡ እነዚህን ፡ መደቆስ ፡ አለብን ፤ የእነርሱን ፡ ተቃውሞ ፡ በኃይል ፡ መደምሰስ ፡ አለበት ፤ — ግልፅ ፡ ነው ፤ ጭቆና ፡ ባለበት ፤ አመፅ ፡ ባለበት ፡ ነፃነት ፡ የለም ፤ ዴሞክራሲ ፡ የለም ።

ኤንግልስ ፡ ለቤቤል ፡ በጻፈው ፡ ደብዳቤ ፡ ይህንን ፤ አንባቢ ፡ እንደሚያስታውሰው ፤ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ግሩም ፡ በሆነ ፡ ሁኔታ ፡ ገልፆታል ፤ « ወዝ ፡ አደሩ ፡ መንግሥትን ፡ የሚፈልገው ፡ ለነፃነት ፡ ፍላጎት ፡ ሳይሆን ፡ ጠላትን ፡ ለመደምሰስ ፡ ነው ፤ ስለ ፡ ነፃነት ፡ ለመናገር ፡ በሚቻልበት ፡ ጊዜ ፡ መንግሥት ፡ አይኖርም ።»





ዴሞክራሲ ፡ ለአብዛኛው ፡ ሰፊ ፡ ሕዝብ ፡ [illegible] ፡ ሕዝቡን ፡ የበዘበዙትን ፤ የጨቆኑትን ፡ በኃይል ፡ መደቆስ ፤ ማለትም ፡ ከዴሞክራሲ ፡ ማግለል — ይህ ፡ ነው ፡ ከካፒታሊዝም ፡ ወደ ፡ ኮሙኒዝም ፡ ባለው ፡ የሽግግር ፡ ጊዜ ፡ ዴሞክራሲ ፡ የሚያደርገው ፡ ለውጥ ።

በኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ የካፒታሊስቶች ፡ ተቃውሞ ፡ በተደመሰሰበት ፡ ጊዜ ፤ ካፒታሊስቶች ፡ በጠፉበት ፡ ጊዜ ፤ መደቦች ፡ በሌሉበት ፡ ጊዜ (ማለትም ፡ በኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ አባሎች ፡ መካከል ፡ በጋራ ፡ የምርት ፡ መገልገያዎች ፡ ላይ ፡ በአላቸው ፡ ግንኙነት ፡ አንፃር ፡ ልዩነት ፡ በሌለበት ፡ ጊዜ) ፤ ያን ፡ ጊዜ ፡ ብቻ ፡ ነው « መንግሥት ፡ የሚጠፋውና ፡ ስለነፃነትም ፡ ለመናገር ፡ የሚቻለው » ። ያን ፡ ጊዜ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እውነተኛ ፡ ሙሉ ፡ ዴሞክራሲ ፡ ያለ ፡ ምንም ፡ ዓይነት ፡ ገደብ ፡ የሚቻለውና ፡ በተግባርም ፡ የሚውለው ። ሰዎች ፡ ከካፒታሊስታዊ ፡ ባርነት ፤ ይህ ፡ ነው ፡ ከማይባል ፡ የካፒታሊስት ፡ ብዝበዛ ፡ ፍርሀቶች ፤ አረመኔነት ፤ ከንቱነትና ፡ ውርደት ፡ ነፃ ፡ ሲወጡ ፤ ቀስ ፡ በቀስም ፡ መሠረታዊ ፡ የሆኑትን ፤ ለምእት ፡ ዓመታት ፡ የታወቁትን ፤ ለብዙ ፡ ሺህ ፡ ዓመታት ፡ በሁሉም ፡ ፊና ፡ ሲደጋገሙ ፡ የኖሩትን ፡ አብሮ ፡ የመኖር ፡ ሕጎችን ፡ አክብረው ፡ መጠበቅን ፡ ሲለምዱ ፤ እነዚህን ፡ ሕጎች ፡ ያለ ፡ ኃይል ፤ ያለ ፡ አስገዳጅነት ፤ ያለ ፡ ትእዛዝ ፤ ያለ ፡ ልዩው ፡ አውታር — መንግሥት ፡ ተብሎ ፡ ከሚጠራው ፡ ማስገደጃ ፡ ድርጅት ፤ ያለሱ — አክብረው ፡ ሲጠብቁ ፤ ይህ ፡ ሀቅ ፡ ሲረጋገጥ ፤ ያን ፡ ጊዜ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ ዴሞክራሲ ፡ መክሰም ፡ የሚጀምረው ።

« መንግሥት ፡ ይከስማል » የሚለው ፡ አገላለፅ ፤ ሁለቱንም ፡ የቀስ ፡ በቀሱን ፡ ሂደትም ፡ ሆነ ፡ ግብታዊውን ፡ ሂደት ፡ ስለሚያመለክት ፤ ጥሩ ፡ ተመርጧል ። አሁንም ፡ ሆነ ፤ ያለጥርጥር ፡ ወደፊት ፤ የዚህ ፡ ዓይነት ፡ ውጤት ፡ ሊሰጥ ፡ የሚችለው ፡ ልምድ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ ምክንያቱም ፡ በአካባ

ቢያችን ፡ በሚሊዮን ፡ በሚቆጠሩ ፡ ሁኔታዎች ፡ እንደምን መለከተው ፡ ብዝበዛ ፡ ከሌለ ፤ ሕዝቡን ፡ የሚያስቆጣ ፤ ቅ ዋሚንና ፡ አመፅን ፡ የሚቀሰቅስ ፤ የጭቆናን ፡ አስፈላጊነት ፡ የሚፈጥር ፡ ምንም ፡ ነገር ፡ ከሌለ ፤ ሰዎች ፡ አብሮ ፡ ለመ ኖር ፡ የሚያስፈልጉዋቸውን ፡ ሕጎች ፡ አክብረው ፡ መጠበ ቅን ፡ በቀላሉ ፡ ይለምዳሉ ።

ስለዚህም ፤ በካፒታሊስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ያለው ፡ ዴሞክራሲ ፡ ጐደሎ ፤ ጎስቋላና ፡ የውሸት ፡ ነው ፤ ዴሞክ ራሲ ፡ ለሃብታሞች ፡ ብቻ ፡ የሆነ ፤ ዴሞክራሲ ፡ ለጥቂቶች ፡ ብቻ ፡ የሆነ ፡ ነው ። የወዝ ፡ አደሩ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፤ ወደ ኮሙኒዝም ፡ ባለው ፡ የሽግግር ፡ ጊዜ ፡ በመጀመሪያ ፡ ጊዜ ፡ ዴሞክራሲ ፡ ለሕዝቡ ፤ ለአብዛኛው ፡ ያጐናፅፋል ፤ በጥቂቶቹ ፤ በበዝባገሮቹ ፡ ላይ ፡ አስፈላጊውን ፡ ጭቆና ፡ ይዘረጋል ። በእርግጥ ፡ የተሟላ ፡ ዴሞክራሲ ፡ ሊሰጥ ፡ የሚ ችለው ፡ ኮሙኒዝም ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ ስለሆነም ፡ ይበልጥ ፡ የተሟላ ፡ በሆነ ፡ መጠን ፤ ይበልጥ ፡ የማያስፈልግ ፡ ይሆናል ፤ ራሱ ፡ በራሱም ፡ ይከስማል ።

በሌላ ፡ አነጋገር ፤ በካፒታሊዝም ፡ ሥር ፡ ያለው ፡ መን ግሥት ፤ በቃሉ ፡ ትክክለኛ ፡ ፍች ፤ አንዱ ፡ መደብ ፡ ሌላ ውን ፤ ይኸውም ፡ በተለይ ፡ ጥቂቶቹ ፡ አብዛኛውን ፡ ክፍል ፡ የሚጨቁኑበት ፡ ልዩ ፡ መኪና ፡ ነው ። እርግጥ ፡ ነው ፤ ይህ ፡ ጉዳይ ፡ የተሳካ ፡ እንዲሆን ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ በባር ነት ፤ በጭሰኝነትና ፡ በቅጥር ፡ ባርነት ፡ ሲሄድ ፡ ጥቂቶቹ ፡ በዝባገሮች ፡ ብዙሀኖቹን ፡ ተበዝባገሮች ፡ በተቀነባበረ ፡ አኳኋን ፡ ሲጨቁኑ ፡ የሚያስፈልጓቸው ፡ የመጨረሻ ፡የጨ ካኝነትና ፡ የአውሬነት ፡ ጭቆናና ፡ የደም ፡ ባህሮች ፡ ናቸ ው ።

ከዚህ ፡ በላይ ፤ ከካፒታሊዝም ፡ ወደ ፡ ኮሙኒዝም ፡ ባለው ፡ የሽግግር ፡ ጊዜ ፡ ጭቆና ፡ ገና ፡ አስፈላጊ ፡ ነው ፤ ይ ሁን ፡ እንጂ ፡ አሁን ፡ ጥቂቱ ፡ በዝባዥ ፡ በሰፊው ፡ ተበዝ ባዥ ፡ የሚጨቆንበት ፡ ነው ። ለመጨቆን ፡ ልዩ ፡ አውታ ር ፤ ልዩ ፡ መኪና ፡ ማለትም ፡ መንግሥት ፡ አስፈላጊ ያስፈልጋል ፤ ሆኖም ፡ ይህ ፡ የመሸጋገሪያ ፡ መንግሥት ፡ ነው ፤ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፤ እንደቃሉ ፡ ትክክለኛ ፡ ፍች ፡ መንግሥት ፡ አይደለም ፤ ምክንያቱም ፡ ጥቂቶቹን ፡ በዝባ ገሮች ፡ በብዙሀኑ ፡ የትላንት ፡ የቅጥር ፡ ባሪያዎች ፡ በነበሩት ፡ መጨቆን ፤ ሲነፃፀር ፡ በጣም ፡ አነስተኛ ፤ ቀላልና ፡ የተለ መደ ፡ ነው ፤ የባሪያዎች ፤ የጭሰኞችና ፡ የቅጥር ፡ ወዝ አደሮች ፡ አመፆች ፡ ሲጨቆኑ ፡ ከፈሰሰው ፡ ደም ፡ ጋር ፡ ሲነፃፀር ፡ የሚፈሰው ፡ ደም ፡ በጣም ፡ ያነሰ ፡ ሲሆን ፤ የሰው ፡ ልጅ ፡ ለዚህ ፡ የሚከፍለው ፡ ዋጋ ፡ በጣም ፡ አነስ ተኛ ፡ ነው ። ይህም ፡ ዴሞክራሲ ፡ ለአብዛኛው ፡ ሰፊ ፡ ሕዝብ ፡ ከማስፋፋት ፡ ጋር ፡ ስለሚስማማ ፤ ለመጨቆን ፡ የልዩ ፡ መኪና ፡ አስፈላጊነቱ ፡ መጥፋት ፡ ይጀምራል ። በዝባገሮች ፡ ሕዝቡን ፡ ለመጨቆን ፤ ይህን ፡ ተግባር ፡ ለመፈ ፀም ፡ ያለ ፡ ከፍተኛ ፡ ውስብስብ ፡ መኪና ፡ እንደማይችሉ ፡ የታወቀ ፡ ነው ፤ ሕዝቡ ፡ ግን ፡ በዝባገሮችን ፡ የሚጨቁ ነው ፡ በጣም ፡ ቀላል ፡ በሆነ « መኪና » ፤ እንድያውም ፡ ያለ « መኪና » ፤ ያለ ፡ ልዩ ፡ አውታር ፡ ነው ፡ ለማለት ፡ ይቻላል ፤ በቀላሉ ፡ በታጠቀ ፡ የሰፊ ፡ ሕዝቡ ፡ ድርጅት ፡ ነው (ልክ ፡ እንደ ፡ ወዝ ፡ አደሮችና ፡ የወታደሮች ፡ ሶቪ ዬቶች — የወደፊቱን ፡ ቀድመን ፡ ለመጥቀስ) ።

በመጨረሻም ፤ ኮሙኒዝም ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ መንግሥ ትን ፡ ፍጹም ፡ የማያስፈልግ ፡ የሚያደርገው ፤ ምክንያቱም ፡ ማንም ፡ የሚጨቆን ፡ አይኖርምና — « ማንም » — በመ ደብ ፡ ረገድ ፤ ከተወሰነ ፡ የሕዝብ ፡ ክፍል ፡ ጋር ፡ በተቀ ነባበረ ፡ ትግል ፡ ረገድ ፡ ማለት ፡ ነው ። እኛ ፡ ተምኔታው ያን ፡ አይደለንም ፤ ስለሆነም ፡ ግለ ፡ ሰብ ፡ ሰዎች ፡ ከልክ ፡ ማለፍ ፡ እንደሚችሉና ፡ ከልክ ፡ ሳያልፉም ፡ እንደማይ ቀሩ ፤ እና ፡ እነዚህን ፡ ከልክ ፡ ያለፉትን ፡ ማቆም ፡ አስ ፈላጊ ፡ መሆኑን ፡ ቅንጣት ፡ ያህል ፡ እንኳን ፡ አንክድም ። ቢሆንም ፤ በመጀመሪያ ፡ ደረጃ ፤ ይህን ፡ ለመጨቆን ፡ ልዩ ፡

መኪና ፤ ልዩ ፡ አውታር ፡ አያስፈልግም ፤ ይህን ፡ የሚያከናውነው ፡ የታጠቀው ፡ ሕዝብ ፡ ራሱ ፡ በቀላሉና ፡ ያለ ፡ ችግር ፡ ነው ፤ ይኸውም ፡ በዘመናዊው ፡ ኅብረተ ፡ ሰብም ፡ እንኳን ፡ ቢሆን ፤ ማንኛውም ፡ የሠለጠኑ ፡ ሰዎች ፡ ክምችት ፡ የሚጣሉ ፡ ሰዎችን ፡ በቀላሉ ፡ እንደሚያለያዩ ፤ ወይም ፡ ሴትን ፡ ከመጠቃት ፡ በቀላሉ ፡ እንደሚያድነው ፡ ሁሉ ፡ ነው ። በሁለተኛ ፡ ደረጃም ፤ አብሮ ፡ የመኖር ፡ ሕጎችን ፡ የመጣስ ፡ ከልክ ፡ የማለፍ ፡ መሠረታዊ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብአዊ ፡ ምክንያት ፡ የሚሆነው ፡ በሰፊው ፡ ሕዝብ ፡ መበዝበዝ ፤ የሱ ፡ መቸገርና ፡ የሱ ፡ መደኽየት ፡ እንደሆነ ፡ እናውቃለን ። የነዚህ ፡ የሕጎችን ፡ መጣስ ፡ አቢይ ፡ ምክንያት ፡ ከተወገደ ፡ ከልክ ፡ ማለፎች ፡ ያለ ፡ ጥርጥር « መክሰም » ይጀምራሉ ። በምን ፡ ዓይነት ፡ ፍጥነትና ፡ በምን ፡ ዓይነት ፡ ደረጃ ፡ እንደሆነ ፡ አናውቅም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እንደሚከስሙ ፡ የታወቀ ፡ ነው ። ከእነርሱ ፡ መክሰም ፡ ጋር ፡ አብሮ ፡ መንግሥትም ፡ ይከስማል ።

ማርክስ ፡ በተምኔታዊነት ፡ ሳይዘፈቅ ፡ የዚህ ፡ የወደፊቱን ፤ ማለትም ፡ የኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ በመጀመሪያና ፡ በከፍተኛ ፡ ደረጃዎቹ ፡ መካከል ፡ ያለውን ፡ ልዩነት ፡ በሚመለከት ፡ አሁን ፡ መወሰን ፡ የሚቻለውን ፡ በሰፊው ፡ ገልፆታል ።

## ፫ የኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ የመጀመሪያው ፡ ደረጃ ።

ማርክስ « በጎታ ፡ ፕሮግራም ፡ ሂሱ » ወዝ ፡ አደሮች ፡ በሶሺያሊዝም ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ « ያልተሸራረፈ » ወይም « ሙሉ ፡ የጉልበትን ፡ ውጤት » ማግኘት ፡ አለባቸው ፡ የሚለውን ፡ የላሳል ፡ ሀሳብ ፡ ትክክለኛ ፡ አለመሆኑን ፡ በሰፊው ፡ ዘርዝሮታል ። ማርክስ ፡ ከመላ ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ጠቅላላ ፡



ኅብረተ ፡ ሰብአዊ ፡ ምርት ፡ ላይ ፡ ተጠባባቂ ፡ ተቀማጭ ፡ ገንዘብ ፤ ለምርት ፡ ማስፋፊያ ፤ « ከጥቀም ፡ ውጭ » የሆኑትን ፡ መኪናዎችን ፡ መተኪያና ፡ ለሌሎችም ፡ የሚሆን ፡ ገንዘብ ፡ እየተቀነሰ ፡ መቀመጥ ፡ እንዳለበት ፤ ከዚያም ፡ ከእያንዳንዱ ፡ የመገልገያ ፡ ፍጆታ ፡ ለአስተዳደር ፤ ለትምህርት ፡ ቤቶች ፤ ለሆስፒታሎች ፤ ለአረጁ ፡ ሰዎች ፡ መኖሪያ ፡ ቤቶችና ፡ ለሌሎችም ፡ ወጪ ፡ የሚሆን ፡ ገንዘብ ፡ መቀነስ ፡ እንዳለበት ፡ አሳይቷል ።

(« ለወዝ ፡ አደሩ— ሙሉ ፡ የጉልበቱን ፡ ውጤት ») በሚል ፡ ደብዛዛ ፤ ያልተብራራ ፤ አጠቃላይ ፡ የላሳል ፡ ሀረግ ፡ ፋንታ ፡ ማርክስ ፡ የሶሺያሊስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ጉዳዮቹን ፡ ሁሉ ፡ እንዴት ፡ ማከናወን ፡ እንዳለበት ፡ በጥሞና ፡ ገምግሞታል ። ማርክስ ፡ ካፒታሊዝም ፡ የማይኖርበትን ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ የኑሮ ፡ ሁኔታ ፡ ተጨባጭ ፡ ትንተና ፡ በማድረግ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፤

« እዚህ ፡ ላይ ፡ መገንዘብ ፡ ያለብን » (የወዝ ፡ አደሩን ፡ ፓርቲ ፡ ፕሮግራም ፡ በሚተነትንበት ፡ ጊዜ) « የምንወያይበት ፡ የኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ያደገው ፡ በራሱ ፡ መሰረቶች ፡ ላይ ፡ አለመሆኑንና ፤ እንድያውም ፡ በተቃራኒው ፡ አሁን ፡ ገና ፡ ከካፒታሊስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ መውጣቱን ፡ ነው ፤ ስለሆነም ፡ በሁለመናው ፤ በኤኮኖሚ ፤ በሞራል ፤ በእውቀት ፤ የዚህ ፡ የወጣበት ፡ ማህፀን ፡ ቅሪቶችን ፡ ገና ፡ እንዳዘለ ፡ ነው ።»

ይህን ፤ ከካፒታሊዝም ፡ ማህፀን ፡ ገና ፡ አሁን ፡ ወደ ፡ ፀሀይ ፡ ብርሃን ፡ ብቅ ፡ ያለውን ፤ በሁለመናው ፡ የአሮጌው ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ቅሪቶች ፡ ያዘለውን ፡ ዓይነት ፡ የኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብን ፡ ነው ፡ ማርክስ ፡ የኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ « የመጀመሪያው » ወይም ፡ ዝቅተኛ ፡ ደረጃ ፡ ብሎ ፡ የሚጠራው ።

የምርት ፡ መገልገያዎች ፡ የግለሰቦች ፡ የግል ፡ ንብረት ፡ መሆናቸው ፡ ቀርቷል ። የምርት ፡ መገልገያዎች ፡ የጠቅላላው ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ንብረት ፡ ናቸው ። እያንዳንዱ ፡ የኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ አባል ፡ የተወሰነ ፡ የኅብረተ ፡ ሰብአዊ-አስፈላጊ ፡ ሥራ ፡ ድርሻውን ፡ ሲፈጽም ፤ የዚህን ፡ ያህል ፡ የሥራ ፡ መጠን ፡ ሠርቷል ፡ የሚል ፡ የምስክር ፡ ወረቀት ፡ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ይቀበላል ። በዚህ ፡ የምስክር ፡ ወረቀትም ፡ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ የመጠቀምያ ፡ እቃዎች ፡ ጎተራ ፡ ተመጣጣኝ ፡ የሆነ ፡ ምርት ፡ ይቀበላል ። ለኅብረተ ፡ ሰብአዊ ፡ ግልጋሎት ፡ የሚውል ፡ የጉልበቱ ፡ ውጤት ፡ ከተቀነሰበት ፡ በኋላ ፡ እያንዳንዱ ፡ ሠራተኛ ፤ እሱም ፡ በበኩሉ ፡ ለኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ የሰጠውን ፡ ያህል ፡ ይቀበላል ።

« እኩልነት » በከፍተኛ ፡ ደረጃ ፡ የሰፈነ ፡ ይመስላል ።

ነገር ፡ ግን ፡ ላሳል ፡ ይህን ፡ ስለሚመስሉት ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ሥርዓቶች (አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ ሶሺያሊዝም ፡ ስለሚባለው ፤ ማርክስ ፡ ግን ፡ የኮሙኒዝም ፡ የመጀመሪያ ፡ ደረጃ ፡ ብሎ ፡ ስለሚጠራው) ሲናገር ፡ ይህ « ትክክለኛ ፡ ማከፋፈል » ነው ፤ ይህ « የእያንዳንዱ ፡ ሰው ፡ ለእኩል ፡ የጉልበት ፡ ውጤት ፡ የእኩልነት ፡ መብት » ነው ፤ ሲል ፡ ላሳል ፡ ይሳሳታል ፡ ማርክስ ፡ ደግሞ ፡ ይህን ፡ ስህተት ፡ በማብራራት ፡ ያጋልጣል ።

« ስለዚህም ፤ የእኩልነት ፡ መብት » ይላል ፡ ማርክስ « በእርግጥ ፡ እዚህ ፡ ላይ ፡ አለ ። ይሁን ፡ እንጂ ፤ ይህ ፡ የሁሉም ፡ መብት ፡ እኩል ፡ አለመሆንን ፡ እንደሚያመለክት ፡ ሁሉ ፤ ገና « የቡርዥዋ ፡ መብት » ነው ። እኩል ፡ ያልሆኑ ፡ ሰዎች ፡ እኩል ፡ መብት ፡ ሲኖራቸው « የእኩልነት ፡ መብት » እኩልነት ፡ የሚጣስበትና ፡ ኢፍትህ ፡ የሆነ ፡ ነው ። በእርግጥም ፡ እያንዳንዱ ፡ ሰው ፡ የሌላውን ፡ ያህል ፡ ኅብረተ ፡ ሰብአዊ ፡ ሥራ ፡ ሰርቶ ፤ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ምርት (እላይ ፡ ከተጠቀሰው ፡ ቅነሳ ፡ በኋላ) እኩል ፡ ክፍያ ፡ ይቀበላል ።

ነገር ፡ ግን ፡ ሁሉም ፡ ሰዎች ፡ አንድ ፡ ዓይነት ፡ አይደ



ሉም ። አንዱ ፡ ጠንካራ ፤ ሌላው ፡ ደካማ ፤ አንዱ ፡ ያገባ ፤ ሌላው ፡ ያላገባ [illegible] ያሉት ፤ ሌላው ፡ ጥቂት ፡ ልጆች ፡ ያሉት ፤ ወዘተ ፡ ነው ።

ማርክስ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ይደመድማል ፤ «... ስለዚህም ፡ ለእኩል ፡ የሥራ ፡ ክንውን ፤ ብሎም ፡ በኅብረተ ፡ ሰብአዊ ፡ ፍጆታዊ ፡ ተቀማጭ ፡ እኩል ፡ ተሳትፎ ፡ እያላቸው ፤ በገቢር ፡ ላይ ፡ ሲታይ ፡ አንዱ ፡ ከሌላው ፡ የበለጠ ፡ ይቀበላል ፤ አንዱ ፡ ከሌላው ፡ የበለጠ ፡ ሃብታም ፡ ይሆናል ፤ ወዘተ ። እነዚህን ፡ ጉድለቶች ፡ ሁሉ ፡ ለማስወገድ ፤ መብት ፡ እኩል ፡ በመሆን ፡ ፈንታ ፡ እኩል ፡ ያልሆነ ፡ መሆን ፡ ይኖርበታል ።»

ስለዚህም ፡ የኮሙኒዝም ፡ የመጀመሪያው ፡ ደረጃ ፡ ፍትህንና ፡ እኩልነትን ፡ ገና ፡ ሊሰጥ ፡ አይችልም ። በሀብት ፡ በኩል ፡ ልዩነቶች ፤ ትክክል ፡ ያልሆኑ ፡ ልዩነቶች ፤ ገና ፡ ይኖራሉ ። ይሁን ፡ እንጂ ፤ አንዱ ፡ ሰው ፡ ሌላውን ፡ ሰው ፡ ለመበዝበዝ ፡ የማይቻል ፡ ይሆናል ፤ ምክንያቱም ፡ የምርት ፡ መገልገያዎችን ፡ ፋብሪካዎችን ፤ ማሽኖችን ፤ መሬትንና ፡ የመሳሰሉትን...በግል ፡ ንብረት ፡ ስር ፡ መያዝ ፡ አይቻልም ። ማርክስ ፡ የላሳልን ፡ በአጠቃላይ ፡ ስለ « እኩልነት » እና « ፍትህ » ግልፅ ፡ ያልሆነ ፡ ንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ሀረግን ፡ በመሰባበር ፤ የኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ የእድገት ፡ ሂደትን ፡ ያሳያል ፤ ይኸውም ፡ በመጀመሪያ ፡ የምርት ፡ መገልገያዎችን ፡ በግለ ፡ ሰቦች ፡ በግል ፡ ንብረት ፡ ስር ፡ መሆንን ፡ የመሰለ « ኢፍትህን » ብቻ ፡ ለማጥፋት ፡ ይገደዳል ፤ ሆኖም ፡ ይህ ፡ ሌላውን ፡ ኢፍትህ ፤ ማለትም ፡ ፍጆታዊ ፡ እቃዎችን « እንደ ፡ ስራው ፡ መጠን » (እንደ ፡ ፍላጎቱ ፡ ሳይሆን) ማከፋፈልን ፤ ወድያውኑ ፡ ሊያጠፋ ፡ አይችልም ።

ስንኩል ፡ ኤኮኖሚስቶች ፤ ከነሱም ፡ መሃል ፡ የቡርዥዋ ፡ ፕሮፌሰሮችና « የኛው » ቱጋን ፡ ሶሺያሊስቶች ፡ የሰዎች ፡

እኩል ፡ አለመሆንን ፡ በመርሳታቻቸውና ፡ ይህ ፡ እኩል ፡ አለመሆንን ፡ ለማጥፋት « በማለማቸው » ሶሺያሊስቶችን ፡ ሁልጊዜ ፡ ያለማቋረጥ ፡ ይወቅሳሉ ። ይህ ፡ የመሰለ ፡ ወቀሳ ፡ እንደምናየው ፤ ጌቶች ፡ የቡርዥዋ ፡ አይዲኦሎጂስቶች ፡ እጅግ ፡ አላዋቂነታቸውን ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ የሚያረጋግጠው ።

ማርክስ ፡ በከፍተኛ ፡ ጥንቃቄ ፡ ያጤነው ፡ ሊዘለል ፡ የማይችለውን ፡ የሰዎች ፡ እኩል ፡ አለመሆን ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፤ እንደዚሁም ፡ የምርት ፡ መገልገያዎች ፡ ወደ ፡ ጠቅላላው ፡ ኅብረተ ፡ ሰብአዊ ፡ የወል ፡ ንብረት ፡ መዛወር ፡ ብቻ (« ሶሺያሊዝም » እየተባለ ፡ የሚጠራው) ፤ ምርቶች ፡ የሚከፋፈሉት « እንደስራው ፡ ክንውን » እስከሆነ ፡ ድረስ ፡ የሚኖረው ፤ የማከፋፈልንና ፡ የ« ቡርዥዋ ፡ ሕግ » እኩል ፡ ያለመሆን ፡ ጉድለቶችን ፡ ሊያስወግድ ፡ እንደማይችልም ፡ አጢኗል ።

ማርክስ ፡ በመቀጠል ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፤ « ... ነገር ፡ ግን ፡ እነዚህ ፡ ጉድለቶች ፡ በኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ የመጀመሪያው ፡ ደረጃ ፤ ከካፒታሊስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ረጅም ፡ የምጥ ፡ ጭንቀቶች ፡ በኋላ ፡ ገና ፡ እንደወጣ ፡ ስለሆነ ፡ የማይቀሩ ፡ ናቸው ። መብት ፡ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ኤኮኖሚያዊ ፡ መዋቅርና ፡ በዚህም ፡ ምክንያት ፡ ከሚደረሰው ፡ ባህላዊ ፡ እድገት ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ በላይ ፡ ሊሆን ፡ አይችልም ... »

ስለዚህም ፡ በኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ የመጀመሪያ ፡ ደረጃ (እንደተለመደው ፤ ሶሺያሊዝም ፡ ተብሎ ፡ የሚጠራው) «የቡርዥዋ ፡ መብት » በሞላ ፡ አይደለም ፡ የሚወገደው ፤ በከፊል ፡ ብቻ ፤ በተደረሰበት ፡ የኤኮኖሚ ፡ አብዮት ፡ አኳያ ፡ በተመጣጣኝ ፡ ብቻ ፤ ማለትም ፡ የምርት ፡ መገልገያዎችን ፡ በሚመለከት ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ። « የቡርዥዋ ፡ መብት ፡ የምርት ፡ መገልገያዎች ፡ የግለሰቦች ፡



የግል ፡ ንብረት ፡ መሆናቸውን ፡ ያውቀጣቸዋል ። ሶሺያሊዝም ፡ እነዚህን ፡ የወል ፡ ንብረት ፡ [illegible] ። እስከዚህ ፡ ደረጃ ፡ ድረስ ፤ — እስከዚህ ፡ ደረጃ ፡ ድረስ ፡ ብቻ ፤ « የቡርዥዋ ፡ መብት » ይጠፋል ።

ይሁን ፡ እንጂ ፡ የሌላው ፡ የቀረው ፡ ክፍል ፡ ህልውና ፡ ይቀጥላል ፤ በኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ መካከል ፡ በምርት ፡ ማከፋፈልና ፡ በስራ ፡ ማደላደል ፡ እንደ ፡ አጠናቃሪ ፡ ሆኖ ፡ ህልውናውን ፡ ይቀጥላል ። « የማይሰራ ፡ አይብላ » የሚለው ፡ የሶሺያሊዝም ፡ መርህ ፡ አስቀድሞ ፡ ተከናውኗል ። ሌላው « ለእኩል ፡ የሥራ ፡ መጠን ፡ እኩል ፡ የድርሻ ፡ መጠን » የሚለው ፡ የሶሺያሊዝም ፡ መርህም ፡ አስቀድሞ ፡ ተከናውኗል ። ይሁን ፡ እንጂ ፡ ይህ ፡ ገና ፡ ኮሙኒዝም ፡ አይደለም ፤ ይህ ፡ እኩል ፡ ላልሆኑ ፡ ግለሰቦች ፡ እኩል ፡ ላልሆነ (በእርግጥም ፡ እኩል ፡ ላልሆነ) የስራ ፡ መጠን ፡ እኩል ፡ የምርት ፡ መጠን ፡ የሚሰጠው « የቡርዥዋ ፡ መብትን » ገና ፡ አያስወግድም ።

ይህ « ጉድለት ፡ ነው » — ይላል ፡ ማርክስ — ነገር ፡ ግን ፡ ይህ ፡ በኮሙኒዝም ፡ የመጀመሪያ ፡ ደረጃ ፡ የማይቀር ፤ የማይወገድ ፡ ነው ፤ በተምኔታዊነት ፡ ካልተዘፈቅን ፡ በስተቀር ፤ ሰዎች ፡ ካፒታሊዝምን ፡ ገልብጠው ፡ ወድያውኑ ፡ ያለ ፡ ምንም ፡ ሕጋዊ ፡ ደንቦች ፡ ለኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ መስራት ፡ ይማራሉ ፡ ብለን ፡ ማሰብ ፡ የለብንም ፤ በተጨማሪም ፡ የካፒታሊዝም ፡ መደምሰስ ፡ ለዚህ ፡ ዓይነት ፡ ለውጥ ፡ ኤኮኖሚያዊ ፡ ቀዳሚ ፡ መነሻዎችን ፡ ከመቅፅበት ፡ አይፈጥርም ።

አሁን « ከቡርዥዋ ፡ መብት » በስተቀር ፡ ሌላ ፡ ደንቦች ፡ የሉም ። ስለዚህም ፡ በዚሁ ፡ አኳኋን ፡ የምርት ፡ መገልገያዎች ፡ የወል ፡ ንብረትን ፡ በሚጠብቅበት ፡ ጊዜ ፤ አብሮም ፡ የሥራ ፡ እኩል ፡ ተሳትፎንና ፡ የምርት ፡ ውጤቶች ፡ እኩል ፡ መከፋፈሉን ፡ ለመጠበቅ ፡ ለመንግሥት ፡ ያለው ፡ አስፈላጊነት ፡ አሁንም ፡ እንዳለ ፡ ይቀራል ።

ካፒታሊስቶች ፡ ከሌሉ ፤ መደቦች ፡ ከሌሉ ፤ የሚጨቆን ፡ መደብ ፡ ከሌለ ፤ መንግሥት ፡ ይከስማል ።

ነገር ፡ ግን ፡ መንግሥት ፡ ገና ፡ እስከናካቴው ፡ አልከሰመም ፤ ምክንያቱም ፡ በእርግጥ ፡ እኩል ፡ አለመሆንን ፡ የሚያፀድቀውን « የቡርዥዋ ፡ መብት » መጠበቅ ፡ ይቀረዋልና ። መንግሥት ፡ ፍጹም ፡ እንዲከስም ፡ የተሟላ ፡ ኮሙኒዝም ፡ ያስፈልጋል ።

## ፩. የኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ከፍተኛው ፡ ደረጃ ።

ማርክስ ፡ ይቀጥላል ፤

« ... በኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ከፍተኛው ፡ ደረጃ ፡ የግለሰብ ፡ በሥራ ፡ ክፍፍል ፡ የጥገኝነት ፡ ባርነቱ ፡ ከጠፋ ፡ በኋላ ፤ ብሎም ፡ በአእምሮና ፡ በጉልበት ፡ ሥራ ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ ቅራኔ ፡ አብሮት ፡ ሲጠፋ ፤ ሥራ ፡ ለኑሮ ፡ መንገድ ፡ ብቻ ፡ ከመሆን ፡ አልፎ ፤ ራሱ ፡ ለኑሮ ፡ ዋና ፡ አስፈላጊ ፡ ነገር ፡ ሲሆን ፤ እንደዚሁም ፡ ከጠቅላላ ፡ የግለሰቦች ፡ እድገት ፡ ጋር ፡ የምርት ፡ ኃይሎች ፡ ሲያድጉና ፤ ሁሉም ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ የሃብት ፡ ምንጮች ፡ በብዛት ፡ ሲፈልቁ ፤ — ያን ፡ ጊዜ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ የቡርዥዋ ፡ መብት ፡ ጠባብ ፡ አድማስ ፡ በፍፁም ፡ የምንወጣውና ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡም ‘ ከእያንዳንዱ ፡ እንደችሎታው ፤ ለእያንዳንዱ ፡ እንደፍላጎቱ !’ ብሎ ፡ በሰንደቁ ፡ ላይ ፡ ለመቅረፅ ፡ የሚችለው ።»

« ነፃነት » እና « መንግሥት » የሚሉትን ፡ ቃላት ፡ በሚያጣምር ፡ ሞኝነት ፡ ላይ ፡ ኤንግልስ ፡ ያለ ፡ ምሕረት ፡ አዋርዶ ፡ ያፌዘባቸውን ፡ አስተያየቶች ፡ አሁን ፡ ብቻ ፡





ነው ፡ ትክክለኛነታቸውን ፡ [illegible] ቅ ፡ የምንችለው ። መንግሥት ፡ እስካለ ፡ ድረስ ፡ ነፃነት ፡ የለም ። ነፃነት ፡ ሲኖር ፡ መንግሥት ፡ አይኖርም ።

መንግሥት ፡ ፍጹም ፡ የሚከስምበት ፡ ኤኮኖሚያዊ ፡ መሠረት ፡ ከፍተኛ ፡ የሆነ ፡ የኮሙኒዝም ፡ የእድገት ፡ ደረጃ ፡ ሲሆን ፤ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ በአእምሮአዊ ፡ ሥራና ፡ በጉልበት ፡ ሥራ ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ ቅራኔ ፡ ይጠፋል ፤ ማለት ፡ የዘመናዊው ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ እኩል ፡ አለመሆን ፡ ዋናው ፡ ምንጩ ፡ ይጠፋል ፤ ይህን ፡ ምንጭ ፤ በተለይ ፤ የምርት ፡ መገልገያዎችን ፡ ወደ ፡ ሕዝብ ፡ ንብረት ፡ በማዛወር ፡ ብቻ ፤ ካፒታሊስቶችን ፡ በመውረስ ፡ ብቻ ፡ በምንም ፡ ዓይነት ፡ ረገድ ፡ ወዲያውኑ ፡ ማስወገድ ፡ አይቻልም ።

ይህ ፡ ውርስ ፡ የምርት ፡ ኃይሎች ፡ ታላቅ ፡ እድገት ፡ ሊያደርጉ ፡ የሚችሉበት ፡ መንገድ ፡ ይፈጥራል ። ይህን ፡ እድገት ፡ ካፒታሊዝም ፡ በጣም ፡ ሲጎትተው ፡ በምናይበት ፡ ጊዜ ፤ አሁን ፡ በተደረሰበት ፡ የቴክኒክ ፡ ደረጃ ፡ ተመስርቶ ፡ ምን ፡ ያህል ፡ እርምጃ ፡ ወደፊት ፡ ሊገኝ ፡ ይችል ፡ እንደነበር ፡ በምናይበት ፡ ጊዜ ፤ የካፒታሊስቶች ፡ መወረስ ፡ ለሰብአዊ ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ የምርት ፡ ኃይሎች ፡ ታላቅ ፡ እድገት ፡ እንደሚሰጥ ፡ ያለ ፡ ጥርጥር ፡ በሙሉ ፡ እምነት ፡ ለመናገር ፡ ያስችለናል ። ነገር ፡ ግን ፡ ይህ ፡ እድገት ፡ በእንዴት ፡ ያለ ፡ ፍጥነት ፡ እንደሚቀጥል ፤ በምን ፡ ፍጥነት ፡ ደርሶ ፡ የሥራ ፡ ክፍፍልን ፡ እንደሚሰብር ፤ በአእምሮአዊና ፡ በጉልበት ፡ ሥራ ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ ቅራኔን ፡ እንደሚያስወግድ ፤ ሥራን ፡ ወደ « የኑሮ ፡ ዋና ፡ አስፈላጊነት » እንደሚያሸጋግር ፡ አናውቅም ፤ ለማወቅም ፡ አንችልም ።

ስለዚህም ፡ እኛ ፡ ለመናገር ፡ የምንችለው ፤ የሂደቱን ፡ እርዝማኔንና ፡ የሚወሰነውም ፡ በኮሙኒዝም ፡ ከፍተኛ ፡ ደረጃ ፡ የእድገት ፡ ፍጥነት ፡ መሆኑን ፡ በአፅንኦት ፡ በመጥቀስ ፤ ስለማይቀረው ፡ የመንግሥት ፡ መክሰምን ፡ ብቻ ፡

ነው ። ለመክሰም ፡ የሚያስፈልገው ፡ ጊዜና ፡ የተጨበጡ ፡ ቅርያችን ፡ የሚነካ ፡ ጥያቄን ፡ ግን ፡ ፍጹም ፡ ክፍት ፡ እንደሆነ ፡ እንተወዋለን ፤ ምክንያቱም ፡ እነዚህን ፡ ጥያቄዎች ፡ ለመፍታት ፡ የሚያስችሉ ፡ መሠረቶች ፡ የሉም ።

መንግሥት ፡ በፍጹም ፡ ሊከስም ፡ የሚችለው « ከእያንዳንዱ ፡ እንደችሎታው ፤ ለእያንዳንዱ ፡ እንደፍላጎቱ » የሚለው ፡ መርህ ፡ በተግባር ፡ በሚውልበት ፡ ጊዜ ፡ ነው ፤ ይኸውም ፡ ሰዎች ፡ የኅብረተ ፡ ሰቡን ፡ አብሮ ፡ የመኖር ፡ ደንቦችን ፡ አክብረው ፡ መጠበቅ ፡ ሲለምዱና ፡ ሥራቸውም ፡ ብዙ ፡ ምርት ፡ ሰጭ ፡ ሲሆንና ፤ እነሱም ፡ በፈቃዳቸው ፡ እንደችሎታቸው ፡ ሲሠሩ ፡ ነው ። « ጠባቡ ፡ የቡርዥዋ ፡ መብት ፡ አድማስ » አንዱ ፡ ሰው ፡ ከሌላው ፡ ይበልጥ ፡ ግማሽ ፡ ሰዓት ፡ ያህል ፡ እንኳ ፡ ትርፍ ፡ እንዳይሠራ ፤ አንዱ ፡ ሰው ፡ ከሌላው ፡ ያነሰ ፡ ክፍያ ፡ እንዳያገኝ ፤ እንደ ፡ ሽይሎክ ፡[39] ተንኮለኛ ፡ ልብ ፡ እንዲያሰላ ፡ የሚያስገድደው ፤ ይህ ፡ ጠባብ ፡ አድማስ ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ ቦታ ፡ አይኖረውም ። ያን ፡ ጊዜ ፡ ምርት ፡ በሚከፋፈልበት ፡ ጊዜ ፡ ለእያንዳንዱ ፡ የሚደርሰውን ፡ የምርት ፡ መጠን ፡ ማስተካከል ፡ ለኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ አስፈላጊ ፡ አይሆንም ፤ እያንዳንዱ « እንደ ፍላጎቱ » በነፃ ፡ ይወስዳልና ።

በቡርዥዋ ፡ ርዕየት ፡ አንፃር ፡ የዚህ ፡ ዓይነቱ ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ሥርዓት « ፍጹም ፡ ተምኔታዊ » ነው ፡ ብሎ ፡ ለማወጅና ፡ ሶሺያሊስቶች ፤ የእያንዳንዱን ፡ ግለሰብ ፡ ሥራ ፡ ሳይቆጣጠሩ ፤ እያንዳንዱ ፡ ሰው ፡ ከኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ የሆነውን ፡ ያህል ፡ ቸኮላት ፤ አውቶሞቢሎች ፤ ፒያኖዎች ፤ … ወዘተ ፡ ለመቀበል ፡ መብት ፡ አለው ፡ ብለው ፡ ተስፋ ፡ ይሰጣሉ ፡ ብሎ ፡ ለመሳለቅ ፡ ቀላል ፡ ነው ። አብዛኞቹ ፡ የቡርዥዋ « ሊቃውንት » እስከዛሬ ፡ ድረስ ፡ በዚህ ፡ ዓይነቱ ፡ መሳለቅ ፡ ራሳቸውን ፡ ይወስናሉ ፤ በዚህም ፡ አላዋቂነታቸውንና ፡ ለካፒታሊዝም ፡ ቅጥር ፡ ተዋጊነታቸውን ፡ ያጋልጣሉ ።



ይህ ፡ አላዋቂነት ፡ ነው ፤ ምክንያቱም ፡ የኮሙኒዝም፡ እድገት ፡ ከፍተኛ ፡ ደረጃ ፡ መጣ ፡ ብሎ « ተስፋ ፡ ለመስጠት » በማንኛውም ፡ ሶሺያሊስት ፡ አእምሮ ፡ አልተቀረፀም ፡ ነበር ፤ ግን ፡ ታላላቅ ፡ ሶሺያሊስቶች ፡ አስቀድመው ፡ እንደተገነዘቡት ፡ ይመጣል ፤ ሆኖም ፡ በአሁኑ ፡ የሥራ ፡ አምራችነት ፡ ሁኔታ ፡ አይደለም ፤ እንደዚሁም ፡ በአሁኑ ፡ የሐሳበ ፡ ውሱን ፡ ሰው ፡ ጊዜ ፡ አይደለም ፡ — እንደፖምያሎቭስኪይ ፡ ተረቶች ፡ ዓይነት — « ለቀልድ ፡ ያህል ፡ በከንቱ »[40] የሕዝቡን ፡ ሀብት ፡ የሚያጠፉና ፡ የማይቻለውን ፡ ለመጠየቅ ፡ እንደሚችለው ፡ ዓይነት ፡ ሰው ፡ አይደለም ።

የኮሙኒዝም « ከፍተኛው » ደረጃ ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ፡ በሥራ ፡ መጠንና ፡ በፍጆታ ፡ መጠን ፡ ላይ ፡ ከኅብረተ ፡ ሰቡና ፡ ከመንግሥቱ ፡ በኩል ፡ በጣም ፡ ጥብቅ ፡ ቁጥጥር ፡ እንዲደረግ ፡ ሶሺያሊስቶች ፡ ይጠይቃሉ ። ነገር ፡ ግን ፡ ይህ ፡ ቁጥጥር ፡ መጀመር ፡ ያለበት ፡ ካፒታሊስቶችን ፡ በመውረስ ፤ በካፒታሊስቶች ፡ ላይ ፡ ወዝ ፡ አደሩን ፡ ተቆጣጣሪ ፡ በማድረግ ፡ ነው ፤ መካሄድም ፡ ያለበት ፡ በመንግሥት ፡ ቢሮክራቶች ፡ ሳይሆን ፡ በታጠቁ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ መንግሥት ፡ ነው ።

ቅጥር ፡ ተዋጊዎቹ ፡ የቡርዥዋ ፡ ርእዮተ ፡ ዓለማውያን (እንደ ፡ ጸረተሊዎች ፤ ቼርኖቮችና ፡ መሰል ፡ ተከታዮቻቸው) ካፒታሊዝምን ፡ የሚከላከሉት ፡ የዛሬውኑ ፡ የፖለቲካ ፡ ዋናና ፡ አንገብጋቢ ፡ ጥያቄ ፤ ማለትም ፡ የካፒታሊስቶችን ፡ መወረስ ፤ የጠቅላላውን ፡ ዜጋዎች ፡ ወደ ፡ አንድ ፡ የወዝ ፡ አደሮችና ፡ የተቀጣሪዎች ፡ ግዙፍ « ሲንዲኬት » — ወደ ፡ ጠቅላላ ፡ መንግሥት ፡ መለወጥንና ፤ የዚህንም ፡ ሲንዲኬት ፡ ጠቅላላ ፡ ሥራ ፡ በእውነተኛ ፡ ዴሞክራሲያዊ ፡ መንግሥት ፤ በወዝ ፡ አደሮችና ፡ በወታደሮች ፡ ተወካዮች ፡ ሶቪዬቶች ፡ መንግሥት ፡ ሥር ፡ የማድረግን ፡ ጥያቄ ፤ በሩቅ-ወደፊት ፡ ጥያቄዎች ፡ ጭቅጭቅና ፡ ውይይት ፡ በመተካት ፡ ነው ።





በመሠረቱ ፤ አንድ ፡ ሊቅ ፡ ፕሮፌሰር ፤ ጮርቃ ፡ ተከታዮቹ ፤ ከዛም ፡ እነ ፡ ጸረተሊዎችና ፡ ቼርኖቮች ፡ ስለ ፡ መሠረተ ፡ ቢስ ፡ ተምኔታዊነቶች ፤ ስለ ፡ ቦልሼቪኮች ፡ ቀኖናዊ ፡ ተስፋ ፡ መስጠትና ፤ ሶሺያሊዝም « በተግባር ፡ ማዋል » አይቻልም ፡ ብለው ፡ ሲናገሩ ፡ በአንጎላቸው ፡ ያለው ፡ የኮሙኒዝም ፡ ከፍተኛው ፡ ደረጃ ፡ ነው ፤ ነገር፡ ግን ፡ ይህን « በተግባር ፡ ለማዋል » ተስፋ ፡ የሰጠ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ ያለመም ፡ የለም ፤ ምክንያቱም ፡ እሱን « በተግባር ፡ ለማዋል » በፍፁም ፡ አይቻልምና ።

ይህም ፡ የሚወስደን ፡ ከዚህ ፡ በላይ ፡ በጠቀስነው ፡ ኤንግልስ « ሶሺያል-ዴሞክራት » የሚለው ፡ ስም ፡ ትክክል ፡ ስለአለመሆኑ ፡ ሲገልፅ ፡ ወደ ፡ ነካው ፡ ጥያቄ ፤ በሶሺያሊዝምና ፡ በኮሙኒዝም ፡ መካከል ፡ ስለአለው ፡ ሳይንሳዊ ፡ ልዩነት ፡ ነው ። በፖለቲካ ፡ አንፃር ፡ በኮሙኒዝም ፡ የመጀመሪያው ፡ ወይም ፡ የዝቅተኛው ፡ እና ፡ ከፍተኛው ፡ ደረጃ ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ ልዩነት ፡ ከጊዜው ፡ ጋር ፡ ምናልባት ፡ ትልቅ ፡ ይሆናል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አሁን ፤ በካፒታሊዝም ፡ ወቅት ፡ ይህን ፡ መቀበል ፡ አስቂኝ ፡ በሆነ ፡ ነበርና ፡ ምናልባትም ፡ ይህን ፡ ተቀዳሚ ፡ ተግባር ፡ ሊያደርጉት ፡ የሚችሉ ፡ ሥርዓተ-አልበኛ ፡ ግለሰቦች ፡ ብቻ ፡ ናቸው (ከሥርዓተ-አልበኞቹ ፡ መካከል ፡ አሁንም « በፕሌኻኖቭ » ዓይነት ፡ የክሮፖትኪኖች ፤ የግራቭ ፤ ኮርነሊሰንና ፡ ሌሎችም ፡ የሥርዓተ-አልበኞች « ኮከቦች » ወደ ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስቶች ፤ ወይም — ካሉት ፡ ጥቂቶች ፡ ሥርዓተ-አልበኞች ፡ መካከል ፡ አሁንም ፡ ለዚሁ ፡ ክብርና ፡ ሕሊና ፡ ያለው ፡ አንዱ ፡ ጌ ፡ እንዳስቀመጠው — ወደ ፡ አናርኮ-ትሬንቺስቶች ፡ መለወጥ ፡ ምንም ፡ ትምህርት ፡ ያልቀሰሙ ፡ ካሉ ፡ ነው ።)

ነገር ፡ ግን ፡በሶሺያሊዝምና ፡ በኮሙኒዝም ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ ሳይንሳዊ ፡ ልዩነት ፡ ግልፅ ፡ ነው ። አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ ሶሺያሊዝም ፡ እየተባለ ፡ የሚጠራው ፤ ማርክስ ፡ የኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ « የመጀመሪያው » ወይም ፡ ዝቅ



ተኛ ፡ ደረጃ ፡ ብሎ ፡ ነበር ፡ የሰየመው ። የምርት ፡ መገልገያዎች ፡ በጋራ ፡ ንብረት ፡ ሥር ፡ እስከሆኑ ፡ ድረስ ፤ « ኮሙኒዝም » የሚለውን ፡ ቃል ፡ ለመጠቀም ፡ ይቻላል ፤ ሆኖም ፡ ይህ ፡ የተሟላ ፡ ኮሙኒዝም ፡ አለመሆኑን ፡ የማንረሳ ፡ ከሆነ ፡ ነው ። የማርክስ ፡ ትንተና ፡ ከፍተኛ ፡ ጥቅም ፡ ያለው ፡ እዚህም ፡ ቢሆን ፡ የቁስ ፡ አካላዊነትን ፡ ዲያሌክቲክስ ፤ የእድገት ፡ ቴዎሪን ፡ አቀነባብሮ ፡ በመጠቀም ፡ ኮሙኒዝም ፡ ከካፒታሊዝም ፡ እንደሚያድግ ፡ ነገር ፡ አድርጎ ፡ መመልከቱን ፡ ነው ። በቃላት ፡ ላይ (ሶሺያሊዝም ፡ ምንድን ፡ ነው? ኮሙኒዝም ፡ ምንድን ነው? በሚሉት) በምሁራዊነት ፡ በተፈጠሩ « ልብ ፡ ወለድ » ፍቺዎችና ፡ ፍሬቢስ ፡ ክርክሮች ፡ ፈንታ ፡ ማርክስ ፡ የኮሙኒዝም ፡ የኤኮኖሚ ፡ እድገት ፡ ደረጃዎች ፡ የትኞቹ ፡ እንደሆኑ ፡ ትንተና ፡ ይሰጣል ።

ኮሙኒዝም ፡ በመጀመሪያው ፡ ደረጃ ፤ በቀዳማይ ፡ ክፍሉ ፡ በኤኮኖሚ ፡ በኩል ፡ በተሟላ ፡ ሊያድግና ፤ ከካፒታሊዝም ፡ ወጎች ፡ ርዝራዦች ፡ ፍጹም ፡ ነፃ ፡ ለመሆን ፡ ገና ፡ አይችልም ። ስለዚህም ፡ አስገራሚው ፡ ክስተት ፤ ኮሙኒዝም ፡ በመጀመሪያው ፡ ደረጃ « ጠባቡን ፡ የቡርዧዋ ፡ መብት ፡ አድማስ » መያዙ ፡ ነው ። በእርግጥ ፡ የቡርዧዋ ፡ መብት ፡ በፍጆታዊ ፡ እቃዎች ፡ ማከፋፈል ፡ አንፃር ፡ ሲታይ ፡ የቡርዧዋውን ፡ መንግሥት ፡ ህልውና ፡ ማረጋገጡ ፡ የማይቀር ፡ ነው ፤ ምክንያቱም ፡ መብቱ ፤ ያለ ፡ የመብቱ ፡ ደንቦች ፡ አስከባሪ ፡ አስገዳጅ ፡ አውታር ፡ ሊኖር ፡ ስለማይችል ፡ ነው ።

ስለዚህም ፡ በኮሙኒዝም ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ለጊዜው ፡ የሚቀየው ፡ የቡርዧዋው ፡ መብት ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን — ያለ ፡ ቡርዧዋ — የቡርዧዋው ፡ መንግሥትም ፡ ጭምር ፡ ነው!

የማርክሲዝም ፡ በጣም ፡ ጥልቅ ፡ የሆነውን ፡ ይዘት ፡ ለማጥናት ፡ ቅንጣት ፡ ያህል ፡ ለማይደክሙት ፤ ግን ፡





አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፡ ለሚወነጅሉት ፡ ሰዎች ፡ ይህ ፡ የማይመስል ፡ ነገር ፤ ወይም ፡ በቀላሉ ፡ ዲያሌክቲካዊ ፡ የእውቀት ፡ መራቀቅ ፡ ሆኖ ፡ ይሰማቸው ፡ ይሆናል ።

ነገር ፡ ግን ፡ እንደ ፡ እውነቱ ፡ ከሆነ ፡ በአዲሱ ፡ ውስጥ ፡ የቀሩት ፡ የአሮጌው ፡ ቅሪቶች ፡ በኑሮአችን ፡ ውስጥ ፤ በተፈጥሮም ፡ ሆነ ፡ በኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ በእያንዳንዱ ፡ እርምጃ ፡ ይታዩናል ። ማርክስ ፡ በኮሙኒዝም ፡ ውስጥ « የቡርዥዋ » መብት ፡ ፍርፋሪዎችን ፡ እንዲያው ፡ ዝም ፡ ብሎ ፡ አልጨመረም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከካፒታሊዝም ፡ ማህፀን ፡ ለሚወጣ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ በኤኮኖሚና ፡ በፖለቲካ ፡ የማይቀረውን ፡ ነገር ፡ አመለከተ ፡ እንጂ ።

ዴሞክራሲ ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ ከካፒታሊስቶች ፡ ጋር ፡ ለሚያደርገው ፡ የነፃነት ፡ ትግሉ ፡ ታላቅ ፡ ጠቀሜታ ፤ አለው ። ነገር ፡ ግን ፡ ዴሞክራሲ ፡ በፍጹም ፡ የማይዘለል ፡ ወሰን ፡ አይደለም ፤ ከፊውዳሊዝም ፡ ወደ ፡ ካፒታሊዝም ፡ ከካፒታሊዝም ፡ ወደ ፡ ኮሙኒዝም ፡ ባለው ፡ መንገድ ፡ ላይ ፡ ካሉት ፡ ደረጃዎች ፡ አንዱ ፡ ብቻ ፡ እንጂ ።

ዴሞክራሲ ፡ ማለት ፡ እኩልነት ፡ ማለት ፡ ነው ። ወዝ ፡ አደሩ ፡ ለእኩልነት ፡ የሚያደርገው ፡ ትግልና ፡ የእኩልነት ፡ መፈክሩ ፡ ታላቅ ፡ ትርጉም ፡ ግልፅ ፡ የሚሆነው ፤ የዚህ ፡ ትርጉም ፡ የመደቦች ፡ መደምሰስ ፡ ማለት ፡ መሆኑን ፡ በትክክል ፡ ከገባን ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ ዴሞክራሲ ፡ ማለት ፡ ፎርማል ፡ እኩልነት ፡ ብቻ ፡ ማለት ፡ ነው ። ጠቅላላ ፡ የኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ አባሎች ፡ የምርት ፡ መገልገያዎች ፡ ንብረት ፡ ግንኙነትን ፡ በሚመለከት ፡ እኩል ፡ ከሆኑ ፡ ማለትም ፡ የሥራ ፡ እኩልነት ፤ የደመወዝ ፡ እኩልነት ፡ ከተጎናፀፉ ፤ በኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ፊት ፡ ሊታለፍ ፡ የማይቻል ፡ ወደፊት ፡ የመራመድ ፡ ጥያቄ ፤ ከፎርማል ፡ እኩልነት ፡ ወደ ፡ ህያው ፡ እኩልነት ፡ የመራመዱ ፡ ጥያቄ ፤ ማለትም « ከእያንዳንዱ ፡ እንደ ፡ ችሎታው ፤ ለእያንዳንዱ ፡ እንደ ፡ ፍላጎቱ » የሚለው ፡ መርህ ፡ በተግባር ፡ የማዋልን ፡ ጥያቄ ፡



መደቀኑ ፡ የማይቀር ፡ ነው ። ወደዚህ ፡ ከፍተኛ ፡ ዓላማ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ በምን ፡ ዓይነት ፡ ደረጃዎች ፤ በምን ፡ ዓይነት ፡ ተግባራዊ ፡ እርምጃዎች ፡ እንደሚገፋ ፡ አሁን ፡ አናውቅም ፤ ለማወቅም ፡ አንችልም ። ነገር ፡ ግን ፡ እዚህ ፡ መገንዘቡ ፡ አስፈላጊ ፡ የሚመስለን ፡ የተለመደው ፡ የቡርዥዋ ፡ ርዕየት ፡ የገደብ ፡ አልባ ፡ ውሸት ፡ ሶሺያሊዝምን ፡ የሚመለከተው ፡ እንደ ፡ ሕይወት ፡ አልባ ፡ ነገር ፤ እንደ ፡ ደረቅ ፤ በአንድ ፡ ጊዜ ፡ ለዘለዓለም ፡ እንደቆመ ፡ አድርጎ ፡ እንደሆነና ፤ እንደ ፡ እውነቱ ፡ ከሆነ ፡ ግን ፡ በሶሺያሊዝም ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ብቻ ፡ ፈጣን ፤ ሀቀኛ ፤ በእውነት ፡ ሰፊውን ፡ አቀፍ ፤ መጀመሪያ ፡ አብዛኛው ፡ ሕዝብ ፤ ከዚያም ፡ ጠቅላላው ፡ ሕዝብ ፡ የሚካፈልበት ፡ ወደፊት ፡ ተራማጅ ፡ እንቅስቃሴ ፡ በሁሉም ፡ የሕዝባዊና ፡ የግላዊ ፡ ኑሮ ፡ መስኮች ፡ እንደሚጀመር ፡ ነው ።

ዴሞክራሲ ፡ የመንግሥት ፡ ቅርፅ ፡ ነው ፤ ከብዙ ፡ መልኮቹ ፡ አንዱ ፡ ነው ። ስለዚህም ፡ ዴሞክራሲ ፡ እንደማንኛውም ፡ መንግሥት ፡ ሁሉ ፡ በሰዎች ፡ ላይ ፡ የማያቋርጠውን ፡ ጭቆና ፡ ለመጠቀም ፡ የተደራጀ ፡ ድርጅት ፡ ነው ፡ ይህ ፡ በአንድ ፡ በኩል ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ በሌላ ፡ በኩል ፡ የዜጎችን ፡ እኩልነት ፤ የመንግሥቱን ፡ መዋቅር ፡ ለመወሰንና ፡ ለማስተዳደር ፡ የሁሉንም ፡ ፎርማል ፡ የእኩልነትን ፡ መብት ፡ ያውቃል ። ይህ ፡ በበኩሉ ፡ ዴሞክራሲ ፡ በአንድ ፡ የተወሰነ ፡ የእድገት ፡ ደረጃ ፡ ላይ ፡ ሲደርስ ፤ አንደኛ ፡ ካፒታሊዝምን ፡ ለመጣል ፡ አብዮታዊ ፡ ትግል ፡ የሚያካሂደውን ፡ መደብ — ወዝ ፡ አደሩን ፡ አንድ ፡ ያደርጋል ፤ ይህም ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ የቡርዥዋውን ፤ የሪፑብሊካዊ-ቡርዥዋን ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ ጭምር ፤ ቋሚ ፡ ወታደርን ፤ ፖሊስንና ፡ ቢሮክራሲን ፡ ለመሰባበር ፡ እስከ ፡ መጨረሻው ፡ ድረስ ፡ ለማድቀቅና ፡ ከመሬት ፡ ገጽ ፡ ለመጥረግ ፡ በሌላ ፡ ይበልጥ ፡ ዴሞክራቲክ ፡ በሆነ ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ እንዲተካው ፡ ያስችለዋል ። ሆኖም ፡ ይህ ፡ የመንግሥት ፡






መኪና ፡ በታጠቁ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ ቅርፅ ፡ ጠቅላላ ፡ ሕዝብ ፡ የሚሳተፍበት ፡ ሕዝባዊ ፡ ወታደርነትን ፡ ይመሠርታል ።

እዚህ ፡ ላይ ፡ መጠን ፡ ወደ ፡ ጥራት ፡ ይሸጋገራል ። ይህን ፡ መሳይ ፡ የዴሞክራሲ ፡ ደረጃ ፡ የሚያመለክተው ፡ የቡርዥዋ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ድንበሮች ፡ መታለፍንና ፡ የሶሺያሊስት ፡ ሥርዓት ፡ መገንባት ፡ መጀመሩን ፡ ነው ። በእርግጥ ፡ በመንግሥቱ ፡ አስተዳደር ፡ ሁሉም ፡ ከተካፈሉ ፡ ካፒታሊዝም ፡ ለመቆም ፡ አይችልም ። የካፒታሊዝም ፡ እድገትም ፡ በበኩሉ « ሁሉም » በመንግሥቱ ፡ አስተዳደር ፡ በእርግጥ ፡ መሳተፍ ፡ የሚያስችላቸው ፡ ቅድመ ፡ ሁኔታዎችን ፡ ይፈጥራል ። ከነዚህ ፡ ቅድመ ፡ ሁኔታዎች ፡ ጥቂቶቹ ፡ — ትምህርት ፡ ለሁሉ ፤ ይህ ፡ በአብዛኞቹ ፡ በጣም ፡ ያደጉ ፡ የካፒታሊስት ፡ አገሮች ፡ ተደርሶበታል ፤ ከዚያም ፡ ግዙፍ ፤ ውስብስብና ፡ ማኅበራዊ ፡ በሆኑት ፤ በፖስታ ፤ በባቡር ፡ ሐዲድ ፤ በታላላቅ ፡ ፋብሪካዎች ፤ በሰፋፊ ፡ ንግዶች ፤ በባንክ ፡ ጉዳይ ፡ ወዘተ … ወዘተ ፤ የአገልግሎት ፡ ድርጅቶች ፡ በሚሊዮን ፡ የሚቆጠሩ ፡ ሠራተኞችን « ማሰልጠኑንና ፡ ሥነ ፡ ሥርዓታዊ ፡ ማድረጉን ፡ ነው » ።

እነዚህ ፡ የኤኮኖሚ ፡ ቅድመ ፡ ሁኔታዎች ፡ ተሟልተው ፤ ካፒታሊስቶችና ፡ ቢሮክራቶች ፡ ከተገለበጡ ፡ በኋላ ፡ ወድያውኑ ፤ ከዛሬ ፡ ለነገ ፤ የምርትንና ፡ የማከፋፈሉን ፡ መቆጣጠር ፤ የሥራና ፡ የምርት ፡ እቃዎች ፡ የሂሳብ ፡ መዝገብ ፡ መያዝን ፡ የሥራ ፡ ክንውን ፤ በታጠቁ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፤ በጠቅላላው ፡ በታጠቀ ፡ ምልአተ-ሕዝብ ፡ ተክቶ ፡ ለመቀጠል ፡ በእርግጥ ፡ ይቻላል ። (የመቆጣጠርና ፡ የሂሳብ ፡ መዝገብ ፡ አያያዝ ፡ ጥያቄ ፡ በሳይንስ ፡ ከሰለጠኑ ፡ መሀንዲሶች ፤ አግሮኖሞች ፤ ወዘተ … ጥያቄ ፡ ጋር ፡ መምታታት ፡ የለበትም ፤ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ዛሬ ፡ በካፒታሊስቶች ፡ ፍላኅት ፡ በመ[illegible]ው ፡ በታጠቁ ፡






ወዝ ፡ አደሮች ፡ ትእዛዝና ፡ ፍላጎት ፡ በበለጠ ፡ አኳኋን ፡ ይሠራሉ ።)

የሂሳብ ፡ መዝገብ ፡ አያያዝና ፡ መቆጣጠር — እነዚህ ፡ ናቸው ፡ ለኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ የመጀመሪያው ፡ ደረጃ « ለተሳካ ፡ ሥራው » ፤ ለትክክለኛ ፡ ተግባሩ ፤ የሚያስፈልጉ ፡ አበይት ፡ ነገሮች ። እዚህ ፡ ላይ ፡ ሁሉም ፡ ዜጎች ፤ የመንግሥቱ ፡ ማለት ፡ የታጠቁት ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ ቅጥር ፡ አገልጋዮች ፡ ይሆናሉ ። ሁሉም ፡ ዜጎች ፡ የአንድ ፡ አገር-አቀፍ ፡ የመንግሥት « ሲንዲኬት » ቅጥረኞችና ፡ ሠራተኞች ፡ ይሆናሉ ። የሚፈለገው ፡ ነገር ፡ ሁሉም ፡ እኩል ፡ ሥራ፡ እንዲሠሩ ፤ ተገቢ ፡ የሥራ ፡ ድርሻቸውን ፡ እንዲያከናውኑና ፡ እኩል ፡ ክፍያ ፡ እንዲያገኙ ፡ ነው ። ለዚህ ፡ የሚያስፈልገው ፡ የሂሳብ ፡ መዝገብ ፡ አያያዝና ፡ የቁጥጥር ፡ ሥር ፡ ከመጠን ፡ በላይ ፡ ቀላል ፡ ወደሆኑ ፤ ሁሉም ፡ የተማረ ፡ ሰው ፡ ሊያከናውናቸው ፡ መደሚቻሉ ፡ ሥራዎች ፡ በካፒታሊዝም ፡ እስከመጨረሻው ፡ ድረስ ፡ በመቃለሉ ፤ መቆጣጠርንና ፡ መመዝገብን ፡ ማንኛውም ፡ የአራቱን ፡ የሂሳብ ፡ መደቦች ፡ እውቀት ፡ ያለውና ፡ ደረሰኞችን ፡ በትክክል ፡ መስጠት ፡ የሚያውቅ ፡ ሰው ፡ ሊያከናውናቸው ፡ ይችላል* ።

---

* አብዛኞቹ ፡ በጣም ፡ አስፈላጊ ፡ የመንግሥት ፡ ሥራዎች ፡ ይህን ፡ በሚመስል ፡ የሂሳብ ፡ መዝገብ ፡ አያያዝና ፡ ቁጥጥር ፡ በወዝ ፡ አደሮች ፡ በራሳቸው ፡ ሲከናወኑ ፡ መንግሥቱ « የፖለቲካ ፡ መንግሥት » መሆኑን ፡ ያቆማል ። « ኅብረተሰባዊ ፡ ሥራዎችም ፡ የፖለቲካ ፡ ጠባያቸውን ፡ አጥተው ፡ ወደ ፡ ቀላል ፡ የአስተዳደር ፡ ሥራዎች ፡ ብቻ ፡ ይለወጣሉ ። » (ከላይ ፤ ምዕራፍ ፡ IV ፤ ቁጥር ፪ ላይ ፡ የኤንግልስ ፡ ከሥርዓተ-አልበኞች ፡ ጋር ፡ ክርክርን ፤ ተመልከት) ።

አብዛኛው ፡ ሕዝብ ፡ ራሱ ፡ በማንኛውም ፡ ቦታ ፡ የዚህ ፡ ዓይነቱን ፡ የሂሳብ ፡ መዝገብ ፡ ይዞታንና ፡ የዚህ ፡ ዓይነቱን ፡ ቁጥጥሮች ፡ በካፒታሊስቶች (አሁን ፡ ወደተቀጣሪነት ፡ በተዛወሩት) ላይና ፡ የካፒታሊስት ፡ ጠባይ ፡ አጥባቂ ፡ በሆኑ ፡ የቡርዥዋ ፡ ምሁራን ፡ ላይ ፡ ማካሄድ ፡ ሲጀምር ፤ ይህ ፡ ቁጥጥር ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ በእውነት ፡ ሁሉ ፡ አቀፍ ፤ አጠቃላይና ፡ ሕዝባዊ ፡ ይሆናል ፤ ያን ፡ ጊዜም ፡ ከዚህ ፡ ማምለጥ ፡ አይቻልም ፤ « የማያወላዳም ፡ ይሆናል » ።

ጠቅላላው ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ የሥራ ፡ እኩልነትና ፡ የክፍያ ፡ እኩልነት ፡ ያለው ፡ አንድ ፡ ቢሮና ፡ አንድ ፡ ፋብሪካ' ፡ ይሆናል ።

ነገር ፡ ግን ፡ ይህ ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ ካፒታሊስቶችን ፡ ካሸነፈ ፡ በኋላ ፤ በዝባዦችን ፡ ከገለበጠ ፡ በኋላ ፡ ለጠቅላላው ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ የሚያስፋፋው « የፋብሪካ » ሥነ ፡ ሥርዓት ፡ በምንም ፡ ዓይነት ፡ የኛ ፡ ምኞት ፡ አይደለም ፤ የመጨረሻ ፡ ግባችንም ፡ አይደለም ፤ ይህ ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡን ፡ ከካፒታሊስት ፡ ብዝበዛ ፡ ጠቅላላው ፡ አሳፋሪና ፡ አሰቃቂ ፡ ቅሪቶች ፡ ፍጹም ፡ ለማንፃትና ፡ እድገትን ፡ ወደፊት ፡ ለማራመድ ፡ የሚጠቅም ፡ አስፈላጊ ፡ እርምጃ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

መላ ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ወይም ፡ ቢያንስ ፡ አብዛኛው ፡ ሰፊ ፡ ሕዝብ ፡ መንግሥቱን ፡ ራሱ ፡ ማስተዳደር ፡ ከተማረበት ፡ ጊዜ ፡ ጀምሮ ፤ ራሱ ፡ ይህን ፡ ጉዳይ ፡ በእጆቹ ፡ ከጨበጠበት ፡ ጊዜ ፤ እፍኝ ፡ በማይሞሉት ፡ ጥቂት ፡ ካፒታሊስቶች ፡ ላይ ፤ ካፒታሊስታዊ ፡ ጠባዮች ፡ ለማቆየት ፡ በሚፈልጉ ፡ ጌቶች ፡ ላይ ፤ ካፒታሊዝም ፡ በጣም ፡ ባባለጋቸው ፡ ሠራተኞች ፡ ላይ ፡ ቁጥጥሩ « ሲሳካ » — ከዚህ ፡ ጊዜ ፡ ጀምሮ ፡ የማንኛውም ፡ አስተዳደር ፡ ባጠቃላይ ፡ አስፈላጊነቱ ፡ መጥፋት ፡ ይጀምራል ። ዴሞክራሲ ፡ ይበልጥ ፡ የተሟላ ፡ በሆነ ፡ መጠን ፤ አስፈላጊ ፡ የማይሆንበት ፡ ጊዜ ፡ ይበልጥ ፡ እየተቀረበ ፡ ይሄዳል ። [illegible] ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡





የተመሠረተውና « በትክክለኛ ፡ የቃሉ ፡ ፍች ፡ መንግሥት ፡ መሆኑን ፡ ያቆመው » መንግሥት ፡ ይበልጥ ፡ ዴሞክራሲያዊ ፡ በሆነ ፡ መጠን ፤ ማንኛውም ፡ የመንግሥት ፡ ቅርፅ ፡ ይበልጥ ፡ ፈጣን ፡ በሆነ ፡ አኳኋን ፡ መክሰም ፡ ይጀምራል ።

ምክንያቱም ፡ ሁሉም ፡ ማስተዳደርን ፡ ሲማሩና ፡ የኅብረተ ፡ ሰቡን ፡ ምርት ፡ በእርግጥ ፡ ራሳቸው ፡ ሲያስተዳድሩ ፤ ራሳቸው ፡ የሂሳብ ፡ መዝገብ ፡ አያያዝ ፡ ሲያካሂዱና ፡ በመኀገሮች ፤ በከበርቴ ፡ ልጆች ፤ በአታላዮችና ፡ በመሰሎቻቸው « የካፒታሊዝም ፡ ወግ ፡ ጠባቂዎች » ላይ ፡ ቁጥጥር ፡ ሲያደርጉ ፤ — ያን ፡ ጊዜ ፡ ከዚህ ፡ መላ ፡ ሕዝብ ፡ አቀፍ ፡ የሂሳብ ፡ መዝገብ ፡ አያያዝና ፡ ቁጥጥር ፡ መወላመጥ ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ አስቸጋሪ ፤ እጅግ ፡ በጣም ፡ ያልተለመደ ፡ ነገር ፡ ይሆናል ፤ እንዲያውም ፡ ፈጣንና ፡ ከባድ ፡ ቅጣት ፡ የሚያስከትል ፡ ስለሚሆን (ምክንያቱም ፡ የታጠቁት ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ የተግባር ፡ ሰዎች ፡ እንጂ ፡ ሴንቲሜንታላዊ ፡ ምሁራን ፡ ስላልሆኑ ፤ ማንም ፡ ሰው ፡ እንዲቀልድባቸው ፡ ፍጹም ፡ ስለማይፈቅዱ) ፤ ቀላልና ፡ መሠረታዊ ፡ የሆኑት ፡ የማንኛውም ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ አብሮ ፡ የመኖር ፡ ደንቦችን ፡ አክብሮ ፡ የመጠበቅንን ፡ አስፈላጊነት ፡ በቶሎ ፡ ይለመዳል ።

ከዚያም ፡ በኮሙኒስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ከመጀመሪያው ፡ ደረጃ ፡ ወደ ፡ ከፍተኛው ፡ ደረጃ ፡ ያለው ፡ የመሸጋገሪያ ፡ በር ፡ በሰፊው ፡ ይከፈታል ፤ ብሎም ፡ መንግሥቱ ፡ ፍጹም ፡ ይከስማል ።

## ምዕራፍ ፡ VI.

## ማርክሲዝም ፡ በአድርባዮች ፡ ሲጐድፍ ።

መንግሥት ፡ ከኅብረተ ፡ ሰብአዊ ፡ አብዮት ፡ ጋር ፡ ያለው ፡ ግንኙነትና ፡ ኅብረተ ፡ ሰብአዊ ፡ አብዮት ፡ ከመንግሥት ፡ ጋር ፡ ያለው ፡ ግንኙነት ፡ ጥያቄ ፤ በጠቅላላው ፡ እንደ ፡

አብዮት ፡ ጥያቄ ፤ የሁለተኛው ፡ ኢንተርናሽናል (፲፰፻፷፬-፲፰፻፸፮ ዓ. ም.) የቴዎሪ ፡ ሰዎችንና ፡ ጸሐፊዎችን ፡ እስከዚህም ፡ አላስጨነቃቸውም ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ በ ፲፰፻፹፱ ዓ. ም. ለሁለተኛው ፡ ኢንተርናሽናል ፡ ውድቀት ፡ ምክንያት ፡ ለሆነው ፡ የአድርባይነት ፡ የዝግምታ ፡ እድገት ፡ ሂደት ፡ ታላቅ ፡ የመለያ ፡ ጠባይ ፤ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ይህ ፡ ጥያቄ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ሲጋፈጣቸውም ፡ እንኳን ፡ ጥያቄውን ፡ ወደ ፡ ጎን ፡ ለማግለል ፤ ወይም ፡ እያዩ ፡ እንዳላዩ ፡ ለመተው ፡ መሞከራቸው ፡ ነው ።

በአጠቃላይ ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት ፡ ከመንግሥት ፡ ጋር ፡ ያለውን ፡ ግንኙነት ፡ በሚመለከት ፡ ጥያቄ ፡ ላይ ፡ መወላመጥ ፤ ይህ ፡ አድርባይነትን ፡ የጠቀመና ፡ ያጐለመሰ ፡ መወላመጥ ፡ ማርክሲዝም ፡ እንዲጣመምና ፡ ፍጹም ፡ እንዲጐድፍ ፡ አድርጓል ፡ ለማለት ፡ ይቻላል ።

የዚህ ፡ አሳዛኝ ፡ ሂደት ፡ ጠባይ ፤ በአጭሩ ፡ እንኳን ፡ ቢሆንም ፡ ለማየት ፤ የማርክሲዝም ፡ በጣም ፡ የታወቁ ፡ ቴዎሪያውያን ፡ ፕሌኻኖቭንና ፡ ካውትስኪይን ፡ እንወስዳለን ።

## ፩ የፕሌኻኖቭ ፡ ከሥርዓተ-አልበኞች ፡ ጋር ፡ ክርክር ።

ፕሌኻኖቭ ፡ ሥርዓተ-አልበኝነት ፡ ከሶሺያሊዝም ፡ ጋር ፡ ስላለው ፡ ግንኙነት « ሥርዓተ-አልበኝነትና ፡ ሶሺያሊዝም » የተባለው ፤ ልዩ ፡ ጽሑፍ ፡ በ ፲፰፻፺፬ ዓ. ም. ፡ በጀርመንኛ ፡ ቋንቋ ፡ አሳተመ ።

ፕሌኻኖቭ ፡ ይህን ፡ ጉዳይ ፡ ሲመረምር ፡ ከሥርዓተ-አልበኝነት ፡ ጋር ፡ በሚደረገው ፡ ትግል ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ አስቸኳይ ፤ አንገብጋቢና ፡ አስፈላጊ ፡ የሆነውን ፡ የፖለቲካ ፡ ጥያቄ ፤ ማለትም ፡ አብዮት ፡ ከመንግሥት ፡ ጋር ፡ ያለውን ፡ የግንኙነት ፡ ጥያቄና ፡ የመንግሥት ፡ ጥያቄ ፡ በጠቅላላ ፡ አግልሎ ፡ ለማለፍ ፡ ሞክሯል! ጽሁፉ ፡ በሁለት ፡ክፍል ፡







ለመክፈል ፡ ይቻላል ፤ አንደኛው ፤ ታሪካዊና ፡ ስነ ፡ ጽሁፋዊ ፡ ሲሆን ፡ በሽቲርነር ፤ በፕሩዶንና ፡ በሌሎችም ፡ ሀሳቦች ፡ ታሪክ ፡ ላይ ፡ ጠቃሚ ፡ የሆኑ ፡ ማስረጃዎችን ፡ ይዟል ። ሌላው ፤ ሁለተኛው ፡ ክፍል ፡ ጮርቃዊ ፡ ሲሆን ፤ ሥርዓተ-አልበኛ ፡ ከሽፍታ ፡ ሊለይ ፡ አይችልም ፡ በሚል ፡ ርእስ ፡ የማይረባ ፡ አስተያየት ፡ ይዟል ።

ይህ ፤ በሩሲያ ፡ ውስጥ ፡ በአብዮቱ ፡ ዋዜማና ፡ በአብዮታዊው ፡ ወቅት ፡ በጣም ፡ የሚያስደንቅ ፡ የጉዳዮችና ፡ የፕሌኻኖቭ ፡ ጠቅላላ ፡ ድርጊት ፡ አጠቃላይ ፡ ባህርይ ፡ መጣመር ፡ የሚያሳይ ፡ ነው ፤ በእርግጥም ፡ ከ ፲፰፻፷፰ ዓ. ም. እስከ ፲፰፻፸፪ ዓ. ም. ባሉት ፡ ዓመታት ፡ ፕሌኻኖቭ ፡ በፖለቲካ ፡ የቡርዥዋውን ፡ ፈለግ ፡ የሚከተል ፤ ከፊል ፡ ቴዎሪያዊ ፤ ከፊል ፡ ጮርቃ ፡ መሆኑን ፡ ራሱን ፡ አሳይቷል ።

ማርክስና ፡ ኤንግልስ ፡ ከሥርዓተ-አልበኞች ፡ ጋር ፡ ባደረጉት ፡ ክርክር ፤ አብዮት ፡ ከመንግሥት ፡ ጋር ፡ ባለው ፡ ግንኙነት ፡ ላይ ፡ ያላቸውን ፡ አስተያየት ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ግልፅ ፡ በሆነ ፡ መንገድ ፡ ማስረዳታቸውን ፡ ተመልክተናል ። በ ፲፰፻፸፭ ዓ. ም. ለማርክሱ ፡ « የጐታው ፡ ፕሮግራም ፡ ሂሱ » በጻፈው ፡ መቅድም ፡ ላይ ፡ ኤንግልስ ፡ ሲጽፍ ፡ እንዲህ ፡ ይላል — « እኛ » (ማለትም ፡ ኤንግልስና ፡ ማርክስ) ፤ « በዚያን ፡ ጊዜ — በሄግ ፡ ከተደረገው ፡ የአንደኛው ፡ ኢንተርናሽናል ፡ [41]ጉባኤ ፡ በኋላ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ሳይሞላው — ከባኩኒንና ፡ ከተከታይ ፡ ሥርዓተ-አልበኞቹ ፡ ጋር ፡ በጣም ፡ በከረረ ፡ ትግል ፡ ላይ ፡ ነበርን ። »[42]

ሥርዓተ-አልበኞቹ ፡ የፓሪሱን ፡ ኮሙን « የግላቸው » እንደ ፡ ሆነ ፡ አድርገው ፤ ለስብከታቸው ፡ ተጨማሪ ፡ ማረጋገጫ ፡ ለማድረግ ፡ ሞክረው ፡ ነበር ፤ ይሁንና ፡ የኮሙን ፡ትምህርቶችና ፡ በእነዚህ ፡ ትምህርቶች ፡ ላይ ፡ ማርክስ ፡ ያደረገው ፡ ትንተናም ፡ በፍፁም ፡ አልገባቸውም ፡ ነበር ። ሥርዓተ-አልበኝነት ፤ አሮጌው ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ መደቆስ ፡ አለበትን? በሱስ ፡ ምንድን ፡ ነው ፡ የሚተካው?

ለሚሉት ፡ የተጨበጡ ፡ የፖለቲካ ፡ ጥያቄዎች ፡ ወደ ፡ ትክክለኝነት ፡ የሚጠጋ ፡ ምንም ፡ ዓይነት ፡ መልስ ፡ አልሰጠም ።

ነገር ፡ ግን ፡ የመንግሥት ፡ ጥያቄ ፡ በጠቅላላው ፡ ወደ ጎን ፡ በመተው ፤ ከኮሙን ፡ በፊትም ፡ ሆነ ፡ በኋላ ፡ ያለውን ፡ ጠቅላላ ፡ የማርክሲዝምን ፡ እድገት ፡ ሳይገነዘቡ ፤ ስለ « ሥርዓተ-አልበኝነትና ፡ ሶሺያሊዝም » መናገር ፤ ያለ ፡ ጥርጥር ፡ ወደ ፡ አድርባይነት ፡ መንሻራተት ፡ ማለት ፡ ነው ። አድርባይነት ፡ በተለይ ፡ ከሁሉም ፡ በላይ ፡ የሚፈልገው ፡ ቀደም ፡ ሲል ፡ የተጠቀሱት ፡ ሁለት ፡ ጥያቄዎች ፡ በፍጽም ፡ እንዳይነሱ ፡ ነው ። ይህ ፡ ራሱ ፡ ለአድርባይነት ፡ ድል ፡ ነው ።

## ፪ የካውትስኪይ ፡ ከአድርባዮች ፡ ጋር ፡ ክርክር ።

እርግጥ ፡ ነው ፤ እጅግ ፡ በጣም ፡ ብዙ ፡ የሆኑ ፡ የካውትስኪይ ፡ ጽሑፎች ፡ ከሌላ ፡ ቋንቋ ፡ ይልቅ ፡ በሩሲያንኛ ፡ ቋንቋ ፡ በብዛት ፡ ተተርጉመዋል ። ያለ ፡ ምክንያት ፡ አይደለም ፡ የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ ሲቀልዱ ፡ ካውትስኪይ ፡ ከጀርመን ፡ ይልቅ ፡ በሩሲያ ፡ በብዛት ፡ ያነቡታል ፡ የሚሉት (በቅንፍ ፡ ውስጥ ፡ እናስቀምጠውና ፤ ይህን ፡ ቀልድ ፡ በመጀመሪያ ፡ የተናገሩት ፡ ሰዎች ፡ ከጠረጠሩት ፡ የበለጠ ፤ እጅግ ፡ በጣም ፡ ጥልቅ ፡ የሆነ ፡ ታሪካዊ ፡ ይዘት ፡ አለው ። ይኸውም ፡ በ ፲፱፻፳ ዓ. ም. የሩሲያ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ በዓለም ፡ ውስጥ ፡ ከነበሩት ፡ የተሻሉ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ የተሻሉ ፡ ስነ ፡ ጽሑፎች ፡ ለማግኘት ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ከፍተኛና ፡ ታይቶ ፡ የማይታወቅ ፡ ፍላጎት ፡ በማሳየታቸው ፤ ከዚያም ፡ የነዚህ ፡ ጽሑፎች ፡ ትርጉሞችና ፡ እትሞች ፤ በሌሎች ፡ አገሮች ፡ ታይቶ ፡ በማይታወቅ ፡ መጠን ፤ በብዛት ፡ በማግኘት ፤ በዚህ ፡ አኳኋን ፡ የጎረቤትና ፡ በጣም ፡ ያደገችን ፡ አገር ፡ ትልቅ ፡ ልምድ ፡ ወደ ፡ እኛው ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ እንቅስቃሴ ፡ ድንግል ፡ አፈር ፡ በፍጥነት ፡ ተዳረሰ) ።



ካውትስኪይ ፡ ማርክሲዝም ፡ ዝነኛ ፡ ከማድረጉም ፡ ሌላ ፤ ከአድርባዮችና ፡ የነሱ ፡ ቀንደኛ ፡ ከሆነው ፡ ከቤርንስተይን ፡ ጋር ፡ ባደረገው ፡ ክርክር ፡ በተለይ ፡ በእኛ ፡ አገር ፡ የታወቀ ፡ ነው ። ይሁን ፡ እንጂ ፡ ካውትስኪይ ፡ በማይታመን ፡ አሳፋሪ ፡ ሁኔታ ፡ እንዴት ፡ ውዥምብር ፡ ረግረግ ፡ ውስጥ ፡ እንደመሰጠና ፤ በ ፲፱፻፲፬-፲፱፻፲፰ ዓመታት ፡ አቢይ ፡ የቀውስ ፡ ጊዜ ፡ ሶሺያል ፡ ትምክህተኝነትን ፡ በመደገፍ ፡ እንዴት ፡ እዚሁ ፡ ረግረግ ፡ ውስጥ ፡ እንደተዘፈቀ ፡ ማጣራት ፡ ብንሞክር ፡ አንድ ፡ በደምብ ፡ ያልታወቀ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ልንዘነጋው ፡ የማይገባን ፡ ሀቅ ፡ አለ ። ሀቁ ፡ እንደሚከተለው ፡ ነው — የአድርባይነት ፡ ቀንደኛ ፡ ተወካዮች ፡ በሆኑት ፤ በፈረንሳይ (ሚልየራንና ፡ ዦረስ) እንዲሁም ፡ በጀርመን (ቤርንስተይን) ፡ ላይ ፡ ከመነሳቱ ፡ በፊት ፡ ካውትስኪይ ፡ በጣም ፡ ከፍተኛ ፡ ወላዋይነት ፡ ታይቶበታል ። በስቱትጋርት ፡ በ ፲፱፻፭-፲፱፻፱ ዓመታት ፡ ሲታተም ፡ የነበረውና ፡ ለአብዮታዊ ፡ ወዝ ፡ አደራዊ ፡ ርዕዮቶች ፡ የተሟገተው ፡ ማርክሳዊ ፡ መጽሔት « ዛርያ »[43] (« ጎህ ») ፤ ከካውትስኪይ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ክርክር ፡ ለመግባት ፡ ተገድዶ ፡ ነበርና ፡ በፓሪሱ ፡ የ ፲፱፻ ዓ. ም. ዓለም ፡ አቀፍ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ጉባዔ ፡ ላይ ፡ [44]ያቀረበውን ፤ ግማሽ ፡ ልብ ፡ የሆነውን ፤ ወላዋይውን ፤ ከአድርባዮች ፡ ጋር ፡ እርቅ ፡ የሚሻውን ፡ ውሳኔ « ላስቲክ » ብሎ ፡ ሰይሞታል ። ከቤርንስተይን ፡ ጋር ፡ የክርክር ፡ መድረክ ፡ ከመከፈቱ ፡ በፊት ፡ በጀርመን ፡ ሥነ ፡ ጽሑፍ ፡ የታተሙት ፡ የካውትስኪይ ፡ ደብዳቤዎች ፤ በእርሱ ፡ በኩል ፡ ከዚህ ፡ ያላነሰ ፡ ማመንታት ፡ እንደነበር ፡ ያረጋግጣሉ ።

ይሁን ፡ እንጂ ፡ ከፍተኛ ፡ የሆነ ፡ ትልቅ ፡ ጠቀሜታ ፡ ያለው ፡ ነገር ፤ ከአድርባዮች ፡ ጋር ፡ ባደረገው ፡ ክርክር ፤ በጥያቄው ፡ አቀራረብና ፡ በጥያቄው ፡ አመለካከት ፡ ዘይቤ ፤ አሁን ፡ የካውትስኪይን ፡ የቅርብ ፡ ጊዜ ፡ የማርክሲዝም ፡ ክህደቱን ፡ ታሪክ ፡ በምናጠናበት ፡ ጊዜ ፤ በተለይም ፡ በመ

ንግሥት ፡ ጥያቄ ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ አድርባይነት ፡ ያደረገው ፡ የተቀነባበረ ፡ ማፈግፈግ ፡ ልንገነዘብ ፡ እንችላለን ።

በአድርባይነት ፡ ላይ ፡ የተጻፈውን « ቤርንስተይንና ፡ ሶሺያል-ዴሞክራሲያዊው ፡ ፕሮግራም » የተባለውን ፡ የካውትስኪይ ፡ የመጀመሪያው ፡ ዋና ፡ ጠቃሚ ፡ መጽሐፉን ፡ እንውሰድ ። ካውትስኪይ ፡ ቤርንስተይንን ፡ በዝርዝር ፡ ያወግዛል ። ቢሆንም ፡ መለያ ፡ ነገሩ ፡ ይኸውና ።

ቤርንስተይን « የሶሺያሊዝም ፡ ቀዳሚ ፡ ሁኔታዎች » በተባለው ፤ ባለ ፡ ሄሮስትራቴአዊ ፡ ዝና ፡ ሥራው ፡ ማርክሲዝምን « በብላንኪዝም » ይከሳል (ከዚያን ፡ ጊዜ ፡ ጀምሮ ፡ በሩሲያ ፡ ውስጥ ፡ ባሉት ፡ አድርባዮችና ፡ ሊበራል ፡ ቡርዥዋዎች ፡ አማኻኝነት ፤ በአብዮታውያን ፡ ማርክሲስቶች ፤ በቦልሼቪኮች ፡ ላይ ፡ ሺህ ፡ ጊዜ ፡ በመደጋገም ፡ የተሰነዘረ ፡ ክስ ፡ ነው) ። በዚህ ፡ ላይ ፡ ቤርንስተይን ፡ በማርክስ ፡ ጽሑፍ « የእርስ ፡ በርስ ፡ ጦርነት ፡ በፈረንሳይ » ላይ ፡ ያተኩራል ፤ እንዳየነውም ፡ በኮሙኑ ፡ ትምህርቶች ፡ ላይ ፡ ያሉትን ፡ የማርክስን ፡ አስተያየቶች ፡ ከፕሩዶን ፡ አስተያየቶች ፡ ጋር ፡ ለማመሳሰል ፡ ያልተሳካ ፡ ሙከራ ፡ ያደርጋል ። ቤርንስተይን ፡ በተለይ ፡ የሚያተኩረው ፤ ማርክስ ፡ በ፲፰፻፸፪ ዓ. ም. « በኮሙኒስት ፡ ማኒፌስቶ » መቅድሙ ፡ ላይ ፡ በአፅንኦት ፡ የጠቀሰውን ፤ « የወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ ዝግጁውን ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ እንዳለ ፡ በመውረስ ፤ ለራሱ ፡ ዓላማ ፡ ሊገለገልበት ፡ አይችልም » የሚለው ፡ መደምደሚያን ፡ ነው ።

ይህ ፡ አረፍተ ፡ ነገር ፡ ቤርንስተይንን ፡ በጣም « ስላስደሰተው » ፤ በጣም ፡ በተጣመመና ፡ አድርባይ ፡ በሆነ ፡ መንገድ ፡ በመተርጎም ፤ በመጽሐፉ ፡ ውስጥ ፡ ከሶስት ፡ ባላነሰ ፡ ጊዜ ፡ ደጋግሞ ፡ ጠቅሶታል ።

እንዳየነው ፤ ማርክስ ፡ ለማለት ፡ የፈለገው ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ ጠቅላላውን ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ መደቆስ ፤ [illegible] (... ፡ በሚጠቀምበት ፡






አገላለፅ ፡ Sprengung ማፈንዳት) እንዳለበት ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ቤርንስተይን ፡ ከሆነ ፡ ማርክስ ፡ በእነዚህ ፡ ቃላት ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ መደብ ፡ ሥልጣን ፡ በሚይዝበት ፡ ጊዜ ፡ ከልክ ፡ ባለፈ ፡ አብዮታዊ ፡ ስሜት ፡ እንዳይነሳ ፡ ማስጠንቀቂያ ፡ እንደሰጠ ፡ አስመስሎ ፡ ነው ፡ የሚያቀርበው ።

የማርክስን ፡ ሀሳብ ፡ ከዚህ ፡ በጣም ፡ ግርድፍና ፡ አሳፋሪ ፡ ከሆነው ፡ ማጣመም ፡ የባሰ ፡ ለማሰብ ፡ አይቻልም ።

ለመሆኑ ፡ ካውትስኪይ ፡ በጣም ፡ በተብራራ ፡ ቤርንስተይንነት ፡[45] ሲያወግዝ ፡ እንዴት ፡ ነው ፡ የቀጠለው?

በዚህ ፡ ነጥብ ፡ ላይ ፡ ማርክሲዝም ፡ በአድርባይነት ፡ በጣም ፡ መጠምዘዙን ፡ ከመተንተን ፡ ተቆጥቧል ። ኤንግልስ ፡ ለማርክሱ ፡ ጽሑፍ « የእርስ ፡ በርሱ ፡ ጦርነት » ከጻፈው ፡ መቅድም ፡ ከዚህ ፡ በላይ ፡ የጠቀስነውን ፡ ጥቅስ ፡ ጠቅሶ ፤ እንዳለው — በማርክስ ፡ አባባል ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ ዝም ፡ ብሎ ፡ ዝግጁውን ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ መያዝ ፡ አይችልም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በአጠቃላይ ፡ አነጋገር ፡ እሱን ፡ ብቻ ፡ ሊይዘው ፡ ይችላል ። ማርክስ ፡ ከ ፲፰፻፶፪ ዓ. ም. ጀምሮ ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት ፡ ተግባር ፡ የመንግሥቱን ፡ መኪና « መሰባበር » ነው ፡[46] ብሎ ፡ ላቀረበው ፤ ለዚህ ፡ ትክክለኛ ፡ የማርክስ ፡ ሀሳብ ፡ ቤርንስተይን ፡ ቀጥታ ፡ ተቃራኒውን ፡ በማርክስ ፡ ላይ ፡ ሲለድፍ ፤ ካውትስኪይ ፡ ስለዚህ ፡ ጉዳይ ፡ አንድም ፡ ቃል ፡ አልተናገረም ።

በዚህም ፡ የተነሳ ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት ፡ ተግባሮች ፡ በሚለው ፡ ጥያቄ ፡ ላይ ፡ በማርክሲዝምና ፡ በአድርባይነት ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ በጣም ፡ አስፈላጊ ፡ ልዩነት ፡ በካውትስኪይ ፡ ተድበስብሷል!

« የወዝ ፡ አደሩን ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ ጉዳይ ፡ መፍትሄ — ይላል ፡ ካውትስኪይ ፡ በቤርንስተይን « አንፃር » ሲጽፍ — ያለምንም ፡ ስጋት ፡ ለወደፊቱ ፡ ጊዜ ፡ ልንተወው ፡ እንችላለን » (ገጽ ፡ ፲፻፸፪ ፤ የጀርመን ፡ እትም) ።

ይህ ፡ በቤርንስተይን ፡ ላይ ፡ የተሰነዘረ ፡ ክርክር ፡ ሳይ ሆን ፤ በውስጠ ፡ ነገሩ ፤ በሱ ፡ ፊት ፡ መንበርከክ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ለአድርባይነት ፡ እጅን ፡ መስጠት ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ምክንያቱም ፡ በአሁኑ ፡ ጊዜ ፡ አድርባዮቹ ፡ ሁሉም ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት ፡ ተግባሮች ፡ መሠረታዊ ፡ ጥያቄዎች « ያለ ፡ ምንም ፡ ስጋት ፡ ለወደፊቱ ፡ ጊዜ ፡ እንተወው » ከሚለው ፡ በስተቀር ፡ ሌላ ፡ ምንም ፡ ተጨማሪ ፡ አይፈልጉ ምና ፡ ነው ።

ማርክስና ፡ ኤንግልስ ፡ ግን ፡ ከ ፲፰፻፶፪ ዓ. ም. ጀምረው ፡ እስከ ፡ ፲፰፻፺፩ ዓ. ም. ድረስ ፡ ለአርባ ፡ አመታት ፡ ያህል ፤ ወዝ ፡ አደሩን ፡ ያስተማሩት ፡ የመንግሥትን ፡ መኪና ፡ መስበር ፡ እንዳለበት ፡ ነው ። ሆኖም ፡ ካውትስኪ ፡ በ ፲፰፻፺፱ ዓ. ም. በዚህ ፡ ነጥብ ፡ ላይ ፡ ማርክሲዝምን ፡ ፍጹም ፡ ከከዱት ፡ አድርባዮች ፡ ጋር ፡ ተጋፍጦ ፡ ሳለ ፤ የመንግሥትን ፡ መኪና ፡ መስበር ፡ ያስፈልጋል ፡ ወይ ፤ የሚለውን ፡ ጥያቄ ፡ መንግሥት ፡ በምን ፡ ዓይነት ፡ የተጨበጡ ፡ መንገዶች ፡ ይሰበር ፡ በሚል ፡ ጥያቄ ፡ በማጭበርበር ፡ ይተካል ፤ ከዚያም ፡ የተጨበጡ ፡ ቅርፆችን ፡ በቅድምያ ፡ ለማወቅ ፡ አንችልም ፡ በሚለው « የማያከራክር » (እና ፡ ባዶ) የጮርቃነት ፡ እውነት ፡ ጓዳ ፡ ውስጥ ፡ ይደበቃል!!

የወዝ ፡ አደሩ ፡ ፓርቲ ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ መደብ ፡ ለአብዮት ፡ ማደራጀትን ፡ በሚመለከት ፡ ጉዳይ ፡ ላይ ፡ በማርክስና ፡ በካውትስኪይ ፡ መካከል ፡ የማይዘለል ፡ ገደል ፡ ይገኛል ።

የሚቀጥለውን ፤ ይበልጥ ፡ ብስለት ፡ ያለውን ፤ በሰፊው ፡ አድርባይነትን ፡ ለማውገዝ ፡ የፃፈውን ፡ የካውትስኪይ ፡ ሥራ ፡ እንውሰድ ። ይህም « ኅብረተ ፡ ሰባዊ ፡ አብዮት » የተባለው ፡ ጽሑፍ ፡ ነው ። በዚህ ፡ ጽሑፍ ፡ ውስጥ ፡ ደራሲው ፡ እንደ ፡ ልዩ ፡ ርእስ ፡ የወሰደው ፡ ጥያቄ « የወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮትን » እና « የወዝ ፡ አደሩ ፡ መንግሥትን » ነው ። ጸሐፊው ፡ ብዙ ፡ ከመጠን ፡ በላይ ፡ የሚጠቅሙ ፡ ነገሮች ፡ ሰጥቷል ፤ በሆንም ፡ በተለይ ፡ የመንግሥትን ፡ ጥያቄ ፡



ግን ፡ ዘልሎታል ። በጽሑፉ ፡ ውስጥ ፡ በየቦታው ፡ ስለ ፡ መንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ መጨበጥ ፡ ይናገራል ፤ ግን ፡ ሌላ ፡ ምንም ፡ አይጨምርም ፤ ማለትም ፡ የመንግሥትን ፡ መኪና ፡ ሳይደመስስ ፡ ሥልጣን ፡ መጨበጥ ፡ ይቻላል ፡ የሚል ፤ ለአድርባዮች ፡ ቦታ ፡ የሚያስለቅቅ ፡ አገላለጽን ፡ መርጧል ። ማርክስ ፡ በ ፲፰፻፵፪ ዓ. ም. « በኮሙኒስት ፡ ማኒፌስቶ »[47] ፕሮግራም « አርጅቷል » ብሎ ፡ ያወጀው ፡ ነገር ፤ በ ፲፱፻፪ ዓ. ም. በካውትስኪይ ፡ ተሃድሶ ፡ እያገኘ ፡ ነው ።

በጽሑፉ ፡ ውስጥ « ለኅብረተ ፡ ሰባዊ ፡ አብዮት ፡ ቅርፆችና ፡ መሳሪያዎች » ልዩ ፡ ክፍል ፡ ተመድቧል ። እዚህ ፡ ስለ ፡ ሰፊ ፡ ሕዝባዊ ፡ ፖለቲካዊ ፡ አድማ ፤ ስለ ፡ እርስ ፡ በርስ ፡ ጦርነት ፤ « ስለ ፡ ዘመናዊው ፡ ታላቅ ፡ መንግሥት ፡ ታላቅ ፡ መሳሪያዎች ፤ እንደ ፡ ቢሮክራሲና ፡ የጦር ፡ ኃይል » ስለመሳሰሉት ፡ ይናገራል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ኮሙን ፡ ለወዝ ፡ አደሩ ፡ ስለሰጠው ፡ ትምህርት ፡ ግን ፡ አንድም ፡ ቃል ፡ አይናገርም ። በእርግጥም ፡ ኤንግልስ ፡ በመንግሥቱ « መለኮታዊ ፡ አክብሮት » ላይ ፡ በተለይ ፡ ለጀርመን ፡ ሶሺያሊስቶች ፡ ማስጠንቀቂያ ፡ የሰጠው ፡ ያለ ፡ ምክንያት ፡ አልነበረም ።

ካውትስኪይ ፡ ነገሩን ፡ የሚመለከተው ፡ እንደሚከተለው ፡ ነው ። ድል ፡ የመታው ፡ ወዝ ፡ አደር « ዴሞክራሲያዊ ፡ ፕሮግራሙን ፡ ያከናውናል » ፤ ብሎም ፡ ዝርዝሮቹን ፡ ያብራራል ። ነገር ፡ ግን ፡ ፲፰፻፷፩ ዓ. ም. ስለሰጠው ፡ ስለ ፡ አዲሱ ፡ ትምህርት ፡ የቡርዥዋ ፡ ዴሞክራሲ ፡ በወዝ አደሩ ፡ ዴሞክራሲ ፡ መተካት ፡ አለበት ፡ ስለሚለው ፡ ጥያቄ ፡ አንድም ፡ ቃል ፡ አይናገርም ። ካውትስኪይ ፡ ለጆሮ « ማራኪ » በሆኑ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በሰለቹ ፡ ልፈፋዎች ፡ ጥያቄውን ፡ አድበስብሶ ፡ ለማለፍ ፡ ይሞክራል ።

«አሁንም ፡ ቢሆን ፤ በአሁኑ ፡ ሁኔታ ፡ የበላይነትን ፡ እንደማናገኝ ፡ ሳይታለም ፡ የተፈታ ፡ ነው ። አብዮት ፡ ራሱ ፡ ረጅምና ፡ ጥልቅ - ሥር - ሰደድ ፡ ትግ

ልን ፡ ይጠይቃል ። ይህ ፡ ትግል ፡ ራሱ ፡ የኛን ፡ የዛሬውኑ ፡ የፖለቲካና ፡ የኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ መዋቅርን ፡ ይለውጣል ።»

ያለ ፡ ጥርጥር ፡ ይህ ፤ ልክ ፡ ፈረሶች ፡ አጃ ፡ ይበላሉ ፤ ወይም ፡ ቮልጋ (ወንዝ) ወደ ፡ ካስፒያን ፡ ባህር ፡ ይፈሳል ፤ እንደሚለው ፡ ሀቅ ፡ ዓይነት « ሳይታለም ፡ የተፈታ ፡ ነው » ። የሚያሳዝነው ፡ ግን ፡ ስለ « ጥልቅ - ሥር - ሰደድ » ትግል ፡ ባዶና ፡ ከንቱ ፡ ሀረጎችን ፡ በመሰንዘር ፤ ለአብዮታዊው ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ በጣም ፡ ጠቃሚ ፡ የሆነውን ፡ ጥያቄ ፤ ማለትም ፡ መንግሥትን ፤ ዴሞክራሲን ፡ በሚመለከት ፡ ከቀድሞዎቹ ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ያልሆኑ ፡ አብዮቶች ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት ፡ የተለየ « ጥልቅ - ሥር - ሰደድ » የሚያደርገው ፡ ምን ፡ እንደሆነ ፡ ሳይጠቅስ ፡ መታለፉ ፤ ብቻ ፡ ነው ።

ይህን ፡ ጥያቄ ፡ በማግለል ፡ ካውትስኪይ ፤ ምንም ፡ እንኳን ፡ በቃላት ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ የከረረ ፡ ጦርነት ፡ ቢያውጅም ፤ « የአብዮትን ፡ ሀሳብ » (አንድ ፡ ሰው ፡ ለወዝ ፡ አደሮች ፡ የተጨበጡ ፡ የአብዮቶችን ፡ ትምህርቶች ፡ ማስተማር ፡ ከፈራ ፤ ይህ « ሀሳብ » ምን ፡ ያህል ፡ ዋጋ ፡ ይኖረዋል?) አስፈላጊነት ፡ በአፅንኦት ፡ ቢጠቅስም ፤ ወይም « አብዮታዊ ፡ አይዴያሊዝም ፡ ይቅደም » ቢልም ፤ ወይም ፡ የእንግሊዝ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ አሁን « ከንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ አይበልጡም » ብሎ ፡ ቢያስታውቅም ፤ በተግባር ፡ ግን ፡ በዚህ ፡ በጣም ፡ አስፈላጊ ፡ ነጥብ ፡ ላይ ፡ ለአድርባይነት ፡ ቦታ ፡ ለቋል ።

« በሶሺያሊስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ »ይላል ፡ ካውትስኪይ ፡ ሲጽፍ « በጣም ፡ የተለያዩ ፡ ድርጅታዊ ፡ ቅርፆች — ቢሮክራሲያዊ (??) ፤ የሙያ ፡ ማኅበር ፤ የኅብረት ፤ ግላዊ [illegible] ሊኖሩ ፡ ይችላሉ ። ... ለምሳሌ ፡ ያለ ፡ ቢሮክራሲያዊ (??) ድርጅት ፡ ሊሠሩ ፡ የማ






ይችሉ ፤ እንደባቡር ፡ አገልግሎቶች ፡ የመሳሰሉት ፡ የሥራ ፡ ድርጅቶች ፡ አሉ ። እዚህ ፡ ላይ ፡ ዴሞክራሲያዊው ፡ ድርጅት ፡ የሚከተለውን ፡ ቅርፅ ፡ ሊወስድ ፡ ይችላል ። ወዝ ፡ አደሮች ፡ እንደ ፡ ፓርላማ ፡ ዓይነት ፡ የሚመሠርቱ ፡ ወኪሎችን ፡ ይመርጣሉ ። ይህ ፡ ፓርላማ ፡ የሥራ ፡ ደንቦችን ፡ ይደነግጋል ፤ የቢሮክራሲያዊውን ፡ ድርጅት ፡ አስተዳደርንም ፡ ይቆጣጠራል ። የሌሎቹ ፡ የሥራ ፡ ድርጅቶች ፡ አስተዳደር ፡ ለሠራተኛ ፡ ማኅበራት ፡ መስጠት ፡ ይቻላል ፤ ከነዚህም ፡ ሌሎች ፡ እንደዚሁ ፡ በየሥራ ፡ ድርጅቶች ፡ ኅብረት ፡ መሠረት ፡ ሊደራጁ ፡ ይችላሉ ።» (የሩሲያ ፡ ትርጉም ፤ የጄኒቭ ፡ እትም ፤ ፲፱፻፫ ዓ. ም. ፤ ገጽ ፡ ፻፵፰ እና ፡ ፻፲፭)

ይህ ፡ ክርክር ፡ ስህተተኛ ፡ ነው ። ማርክስና ፡ ኤንግልስ ፡ የኮሙንን ፡ ትምህርቶች ፡ እንደምሳሌ ፡ በመውሰድ ፡ በሰባኛዎቹ ፡ ዓመታት ፡ ከሰጧቸው ፡ ማብራሪያዎች ፡ ጋር ፡ ሲነፃፀር ፡ አንድ ፡ እርምጃ ፡ ወደኋላ ፡ ነው ።

አስፈላጊ ፡ ነው ፡ ተብሎ ፡ በተገመተው « ቢሮክራሲያዊ » ድርጅትን ፡ በሚመለከት ፡ ረገድ ፤ የባቡር ፡ አገልግሎት ፡ ከሌላ ፡ በጠቅላላው ፡ ከማንኛውም ፡ ትልቅ ፡ የማሽን ፡ ኢንዱስትሪ ፡ ድርጅት ፤ ከማንኛውም ፡ ፋብሪካ ፤ ትልቅ ፡ ሱቅ ፡ ወይም ፡ ሰፊ ፡ የካፒታሊስት ፡ የእርሻ ፡ ድርጅት ፡ የሚለየው ፡ ምንም ፡ የለም ። የሁሉም ፡ የእነዚህ ፡ የሥራ ፡ ድርጅቶች ፡ ቴክኒክ ፡ ዲሲፕሊን ፡ እጅግ ፡ ጥብቅ ፡ እንዲሆን ፤ ሁሉም ፡ የተመደበለትን ፡ ሥራ ፡ በበለጠ ፡ ትክክለኛነት ፡ እንዲሠራ ፡ ፍጹም ፡ አስፈላጊ ፡ ያደርገዋል ፤ ካልሆነ ፡ ግን ፡ ጠቅላላው ፡ የሥራ ፡ ድርጅት ፡ ሊቆም ፡ ይችላል ፤ ወይም ፡ ማሺነሪው ፡ ይበላሻል ፤ ያለቀለት ፡ ምርት ፡ ይበላሻል ። በእነዚህ ፡ የሥራ ፡ ድርጅቶች ፡ ሁሉ ፤ እርግጥ ፡ ነው ፤ ወዝ ፡ አደሮች « እንደ ፡ ፓርላማ ፡ ዓይነት ፡ የሚመሠርቱ ፡ ወኪሎችን ፡ ይመርጣሉ ።»

ይሁን ፡ እንጂ ፡ የነጥቡ ፡ ፍሬ ፡ ነገር ፡ ይህንን « ዓይ ነት ፡ ፓርላማ » እንደቡርዥዋ ፡ ፓርላማ ፡ ተቋም ፡ ዓይ ነት ፡ የሆነ ፡ ፓርላማ ፡ አይሆንም ። የነጥቡ ፡ ፍሬ ፡ ነገር ፤ ከቡርዥዋ ፡ ፓርላሜንታዊነት ፡ ወሰን ፡ የማያልፍ ፡ አስተ ሳሰብ ፡ ያለው ፡ ካውትስኪይ ፡ እንደሚገምተው ፡ ይህንን « ዓይነቱ ፡ ፓርላማ ፡ የሥራ ፡ ደንቦችን ፡ በመደንገግ ፤ የቢሮክራሲውን ፡ ድርጅት ፡ አስተዳደርን ፡ በመቆጣጠር » ብቻ ፡ አይወሰንም ። በሶሺያሊስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ እንዲህ « ዓይነቱ ፡ ፓርላማ » የወዝ ፡ አደሮች ፡ ተወካዮችን ፡ የ ያዘ ፤ እርግጥ « የሥራ ፡ ደንቦችን ፡ ይደነግጋል ፤ የአውታሩን ፡ አስተዳደርም ፡ ይቆጣጠራል ። » ይሁን ፡ እንጂ ፡ ይህ ፡ ድርጅት « ቢሮክራሲያዊ » አይሆንም ። ወዝ ፡ አደሮቹ ፡ የፖለቲካ ፡ ሥልጣንን ፡ ከጨበጡ ፡ በኋላ ፡ አሮጌውን ፡ ቢሮክራሲያዊ ፡ አውታር ፡ ይደቁሳሉ ፤ ሥረ ፡ መሠረቱን በመሰባበር ፡ ድምጥማጡን ፡ ያጠፋሉ ፤ በአዲስ ፤ እነዚ ያኑ ፡ የበፊቶቹ ፡ ወዝ ፡ አደሮችንና ፡ ቅጥሮችን ፡ በያዘ ፡ አውታር ፡ ይተኩታል ። እነርሱም ፡ ወደ ፡ ቢሮክራቶች ፡ እንዳይሸጋገሩ ፡ ወድያውኑ ፡ በማርክስና ፡ በኤንግልስ ፡ በዝርዝር ፡ የተጠቀሱትን ፡ እርምጃዎች ፡ ሥራ ፡ ላይ ፡ ያው ላሉ ፤ — ፩. መምረጥ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፤ በማንኛውም ፡ ጊዜ ፡ መሻር ፡ መለወጥን ፤ — ፪. ክፍያው ፡ ከወዝ ፡ አደሩ ፡ ደመ ወዝ ፡ መብለጥ ፡ የለበትም ፤ — ፫. ወድያውኑ ፡ ሁሉም ፡ ቁጥጥርንና ፡ ጥበቃን ፡ እንዲያከናውኑ ፤ ሁሉም ፡ ለጊዜ ው « ቢሮክራቶች » እንዲሆኑና ፡ በዚህም ፡ ምክንያት ፡ ማንም « ቢሮክራት » ለመሆን ፡ እንዳይችል ፡ መደረግ ፡ አለበት ።

ካውትስኪይ « ኮሙን ፡ ፓርላማዊ ፡ አካል ፡ አል ነበረም ፤ የሚሠራ ፤ በአንድ ፡ ጊዜ ፡ ሕግ ፡ አውጪና ፡ ሕግ ፡ አስፈፃሚ ፡ አካል ፡ እንጂ »[48] የሚሉት ፡ የማርክስን ፡ ቃ ላት ፡ በፍጹም ፡ አላሰላሰለም ።

ካውትስኪይ ፤ ዴሞክራሲን (ለሕዝብ ፡ ያልሆነ) ከቢሮ ክራሲ ( [illegible])ን ፡ [illegible]ሚያጣምረው ፡ በቡር






ዥዋ ፡ ፓርላማዊነትና ፤ ቢሮክራሲን ፡ ከሥሩ ፡ ለመንቀል ፡ አስቸኳይ ፡ እርምጃዎች ፡ በሚወስደው ፤ እነዚህን ፡ እርም ጃዎች ፡ እስከ ፡ መጨረሻ ፡ ድረስ ፤ ቢሮክራቲዝምን ፡ ፍጹም ፡ እስከ ፡ ማጥፋት ፡ ድረስ ፤ ዴሞክራሲ ፡ ለሕዝቡ ፡ ፍጹም ፡ እስከ ፡ መታወቅ ፡ ድረስ ፡ ማዳረስ ፡ በሚችለው ፡ በወዝ ፡ አደሩ ፡ ዴሞክራሲ ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ ልዩነት ፡ በፍጹም ፡ አልገባውም ።

ካውትስኪይ ፡ እዚህ ፡ ላይ ፡ የሚያሳየው ፡ ያው ፡ ያረ ጀው ፡ በመንግሥት ፡ ላይ ፡ ያለውን « መለኮታዊ ፡ አክብ ሮት » እና ፡ በቢሮክራቲዝም ፡ ላይ ፡ ያለውን « መለኮ ታዊ ፡ እምነት » ነው ።

አሁን ፡ ወደ ፡ መጨረሻውና ፡ ከሁሉም ፡ በበለጠ ፡ በአድ ርባዮች ፡ ላይ ፡ ወደተጻፈው ፤ « ወደ ፡ ሥልጣን ፡ መን ገዱ » ወደተባለው ፡ የካውትስኪይ ፡ ጽሑፍ ፡ እናልፋለን (እንደሚመስለኝ ፡ ይህ ፡ ጽሑፍ ፡ በሩሲያንኛ ፡ ቋንቋ ፡ አልታተመም ። ምክንያቱም ፡ የተጻፈው ፡ በአገራችን ፡ በአድሃሪው ፡ አገዛዝ ፡ ወቅት ፡ በ ፲፱፻፱ ዓ. ም. ስለ ፡ ነበር ፡ ነው) ። ይህ ፡ ጽሑፍ ፡ አንድ ፡ ትልቅ ፡ እርምጃ ፡ ወደፊት ነው ፤ ምክንያቱም ፡ በዚህ ፡ ጽሑፍ ፡ ውስጥ ፡ በ ፲፰፻፺፱ ዓ. ም. በቤርንስተይን ፡ ላይ ፡ እንደተጻፈው ፡ ዓይነት ፡ በአጠ ቃላይ ፡ አብዮታዊ ፡ ፕሮግራም ፡ ብቻ ፡ አይወሰንም ፤ ወይም ፡ በ ፲፱፻፪ ዓ. ም. « ኅብረተ ፡ ሰብአዊው ፡ አብዮት » በሚለው ፡ ጽሑፍ ፡ እንዳለው ፡ ከጊዜ ፡ ጋር ፡ ባልተያያዘ ፡ የኅብረተ ፡ ሰብአዊ ፡ አብዮት ፡ ተግባራት ፡ ብቻ ፡ አይደ ለም ። ጽሑፉ « የአብዮቶች ፡ ዘመን » መድረሱን ፡ እንድን ገነዘብ ፡ የሚያስገድዱን ፡ ተጨባጭ ፡ ሁኔታዎችን ፡ ያመለ ክታል ።

ደራሲው ፡ በእርግጥ ፡ የሚጠቁመው ፡ በአጠቃላይ ፡ ተፃራሪ ፡ መደባዊ ፡ ቅራኔዎች ፡ መባባሳቸውንና ፡ በተለይ ፡ በዚህ ፡ ረገድ ፡ ከፍተኛ ፡ ሚና ፡ የሚጫወተው ፡ ኢምፔሪ ያሊዝምን ፡ ነው ። በምእራብ ፡ አውሮፓ « ከ ፲፯፻፹፱ እስከ ፡ ፲፰፻፸፩ ዓ. ም. ድረስ ፡ እንደነበረው ፡ አብዮታዊ ፡ ወቅ

ት » ዓይነት ፤ ተመሳሳይ ፡ ወቅት ፡ በምስራቅ ፡ በ ፲፱፻፭ ዓ. ም. እንደጀመረ ፡ ይናገራል ። የዓለም ፡ ጦርነት ፡ በአደገኛ ፡ ፍጥነት ፡ በመምጣት ፡ ላይ ፡ ነው ። « ወዝ ፡ አደሩ ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ የአብዮት ፡ ጊዜ ፡ አልደረሰም ፡ ለማለት ፡ አይችልም ።» « ወደ ፡ አብዮታዊው ፡ ወቅት ፡ ውስጥ ፡ ገብተናል ። » « አብዮታዊ ፡ ዘመን ፡ እየጀመረ ፡ ነው ።»

እነዚህ ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ ፍጹም ፡ ግልፅ ፡ ናቸው ። ይህ ፡ የካውትስኪይ ፡ ጽሑፍ ፡ የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ ከኢምፔሪያሊስቱ ፡ ጦርነት ፡ በፊት ፡ ምን ፡ ለመሆን ፡ ቃል ፡ እንደገቡና ፡ ጦርነቱ ፡ በተነሳ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ እነሱ (ራሱ ፡ ካውትስኪይም ፡ ጭምር) ምን ፡ ዓይነት ፡ የውርደት ፡ አዘቅት ፡ ውስጥ ፡ እንዴት ፡ እንደሰመጡ ፡ እንደ ፡ ማወዳደሪያ ፡ ሚዛን ፡ ማገልገል ፡ አለበት ። እየመረመርነው ፡ ባለነው ፡ ጽሑፍ ፡ ካውትስኪይ ፡ ሲጽፍ « የአሁኑ ፡ ሁኔታ ፡ አስፈሪ ፡ ሲሆን ፤ እኛ (የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች) በቀላሉ ፤ ካለን ፡ እውነተኛ ፡ ምንነት ፡ ይልቅ ፤ ይበልጥ ፡ መለስተኞች ፡ መስለን ፡ ልንታይ ፡ እንችላለን » ይላል ። ሀቁ ፡ ግን ፡ የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ ፓርቲ ፡ ለመምሰል ፡ ከሚጥረው ፡ ፍፁም ፡ የባሰ ፡ በጣም ፡ መለስተኛና ፡ አድርባይ ፡ ነው!

በጣም ፡ የሚገርመው ፡ ደግሞ ፤ ምንም ፡ እንኳን ፡ ካውትስኪይ ፡ እንደዚያ ፡ በቁርጥ ፡ የአብዮቶች ፡ ዘመን ፡ ከጀመረ ፡ ቆይቷል ፡ ብሎ ፡ ቢያውጅም ፤ እሱ ፡ ራሱ ፡ እንዳለው ፡ በተለይ « ለፖለቲካዊ ፡ አብዮት » ጥያቄ ፡ ትንተና ፡ የዋለ ፡ ነው ፡ በሚለው ፡ ጽሑፍ ፤ አሁንም ፡ እንደገና ፡ የመንግሥትን ፡ ጥያቄ ፡ ማግለሉ ፡ ነው ።

እነዚህን ፡ የጥያቄው ፡ ማግለል ፡ ሙከራዎች ፤ በዝምታ ፡ ማለፍና ፡ መወላመጦች ፡ አሁን ፡ ቀጥለን ፡ መናገር ፡ ወደምንገደደው ፤ ወደማይቀረው ፡ አድርባይነት ፡ ፍጹም ፡ እንዲሸጋገር ፡ አድርገዋል ።

የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ ቀላጤ ፡ ካውት







ስኪይ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ የሚያውጅ ፡ ይመስላል ፤ — ለአብዮታዊ ፡ ርዕዮቶች ፡ ፅኑ ፡ ነኝ (፲፰፻፺፱ ዓ. ም.) ። ከሁሉም ፡ በላይ ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብአዊ ፡ አብዮት ፡ የማይቀር ፡ መሆኑን ፡ አምናለሁ (፲፱፻፪ ዓ. ም.) ። የአብዮቶች ፡ አዲስ ፡ ዘመን ፡ መድረሱን ፡ እገነዘባለሁ (፲፱፻፱ ዓ. ም.) ። ሆኖም ፡ መንግሥትን ፡ በሚመለከት ፡ ረገድ ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት ፡ ተግባሮች ፡ ጥያቄ ፡ ከተነሳ ፡ በ ፲፰፻፺፪ ዓ. ም. ማርክስ ፡ በተናገረው ፡ ላይ ፡ ወደኋላ ፡ መመለሴ ፡ ነው (፲፱፻፲፪ ዓ. ም.) ።

ካውትስኪይ ፡ ከፓኔኩክ ፡ ጋር ፡ ሲከራከር ፡ በዚህ ፡ ዓይነት ፡ ግትር ፡ መንገድ ፡ ነበር ፡ ጥያቄውን ፡ ያቀረበው ።

## ፫ የካውትስኪይ ፡ ከፓኔኩክ ፡ ጋር ፡ ክርክር ።

ፓኔኩክ ፡ ካውትስኪይን ፡ በመቃወም ፡ የተነሳው ፤ ሮዛ ፡ ሉክሴምቡርግን ፤ ካርል ፡ ራዴክንና ፡ ሌሎችንም ፡ ካቀፈው « ከግራ ፡ ስርነቀል » መስመር ፡ ተከታዮች ፡ እንደ ፡ አንዱ ፡ ተወካይ ፡ በመሆን ፡ ነው ። አብዮታዊውን ፡ ታክቲክ ፡ በመደገፍ ፡ በማርክሲዝምና ፡ በአድርባይነት ፡ መካከል ፡ መርህ ፡ በሌለው ፡ ሁኔታ ፡ ሲዋዥቅ ፡ የነበረው ፡ ካውትስኪይ ፡ ወደ « መሀከል » መሸጋገሩንም ፡ ተረድተዋል ። የዚህ ፡ አስተያየት ፡ ፍጹም ፡ ትክክለኝነት ፡ የተረጋገጠው ፤ በጦርነቱ ፡ ይህ ፡ «ከመሀከለኝነት » (በስህተት ፡ ማርክሳዊ ፡ የተባለው)መስመር ፤ ወይም ፡ ካውትስካዊነት ፡ ሁለመናውና ፡ አስፀያፊ ፡ ስንኩልነቱ ፡ በተፍረጠረጠ ፡ ጊዜ ፡ ነው ።

የመንግሥትን ፡ ጥያቄ ፡ በሚነካው ፤ « ሰፊ ፡ እርምጃና ፡ አብዮት » በተባለው ፡ ጽሑፉ («Neue Zeit» ፲፱፻፲፪ ዓ. ም. ፤ XXX ፤ ቁ.፪) ፓኔኩክ ፡ የካውትስኪይን ፡ አቋም ፡ የሚገልፀው ፡ እንደ « ግኡዝ ፡ ስርነቀልነት » ፤ እንደ « የደነዘዘ ፡ የምኞት ፡ ቲዎሪ » ነው ። « ካውትስኪይ ፡

የአብዮትን ፡ ሂደት ፡ ለማየት ፡ አይሻም » (ገጽ ፡ ፯፻፲፯) ።

ጥያቄውን ፡ በዚህ ፡ አኳኋን ፡ በማቅረብ ፡ ፓኔኩክ ፡ ወደ ምንፈልገው ፤ መንግሥትን ፡ በሚመለከት ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ የአብዮት ፡ ተግባሮች ፡ ወደሚመለከት ፡ ርእስ ፡ ደርሷል !።

« የወዝ ፡ አደሩ ፡ ትግል ፤ — ይላል ፡ ሲጽፍ — ለመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ ብቻ ፡ ከቡርዠዋው ፡ ጋር ፡ የሚደረግ ፡ ትግል ፡ አይደለም ፤ በመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ ላይ ፡ የሚደረግ ፡ እንጂ ። ... የዚህ ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት ፡ ይዘት ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ የሥልጣን ፡ መሳሪያዎችን ፡ በመጠቀም ፡ የመንግሥቱን ፡ የሥልጣን ፡ መሳሪያዎችን ፡ መደቆስና ፡ ማውደም ፡ ነው (Auflösung) ... ትግሉ ፡ የሚቆመው ፡ በትግሉ ፡ ውጤት ፡ የመንግሥት ፡ ድርጅት ፡ ፍጹም ፡ ሲወድም ፡ ብቻ ፡ ነው ። ያን ፡ ጊዜ ፡ የብዙሀኑ ፡ ድርጅቶች ፤ የጥቂቶች ፡ ገዢ ፡ ድርጅትን ፡ በመደምሰስ ፡ የራሱን ፡ የበላይነት ፡ ያስመሰክራል ።» (ገጽ ፡ ፫፻፵፰)

የፓኔኩክ ፡ ሀሳብ ፡ አቀራረብ ፡ በጣም ፡ ትልቅ ፡ ጉድለቶች ፡ አሉበት ። ይሁን ፡ እንጂ ፡ ፍቺው ፡ ግልፅ ፡ ነው ። ካውትስኪይ ፡ ይህንን ፡ እንዴት ፡ እንደተቃወመው ፡ ማስተዋል ፡ ጠቃሚ ፡ ነው ።

«እስከዛሬ ፡ ድረስ ፤ » ይላል ፡ ካውትስኪይ « በሶሺያል-ዴሞክራቶችና ፡ በሥርዓተ-አልበኞች ፡ መካከል ፡ የነበረው ፡ ቅራኔ ፤ የፊተኞቹ ፡ የመንግሥትን ፡ ድል ፡ ለማድረግ ፡ ሲፈልጉ ፤ የኋለኞቹ ፡ ግን ፡ የመንግሥትን ፡ ሥልጣን ፡ ለማውደም ፡ በመፈለጋቸው ፡ ነበር ። ፓኔኩክ ፡ ግን ፡ የሚፈልገው ፡ ሁለቱንም ፡ ለማድረግ ፡ ነው ፤» (ገጽ ፡ [illegible])



የፓኔኩክ ፡ ገለጣ ፡ ጥራትና ፡ ትክክለኛነት ፡ ቢያጥረውም ፡ ቅሉ — (በጽሑፉ ፡ ውስጥ ፡ በመመርመር ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ ርእስ ፡ የማይመለከቱ ፡ ሌሎች ፡ ጉድለቶችን ፡ እንተውና) — ካውትስኪይ ፡ የወሰደው ፡ በተለይ ፡ ያነሳውን ፡ የመርህ ፡ ነጥብ ፡ ነው ፤ በዚህ ፡ መሠረታዊ ፡ የመርህ ፡ ነጥብ ፡ ጥያቄ ፡ ካውትስኪይ ፡ የማርክሲዝምን ፡ አቋም ፡ እርግፍ ፡ አድርጎ ፡ በመጣል ፤ ወደ ፡ አድርባይነት ፡ ተሸጋግሯል ። በሶሺያል-ዴሞክራቶችና ፡ በሥርዓተ-አልበኞች ፡ መካከል ፡ ስላለው ፡ ልዩነት ፡ የሰጠው ፡ ትርጉም ፡ በፍጹም ፡ የተሳሳተ ፡ ነው ፤ ማርክሲዝምን ፡ ይጠመዝዛል ፤ ፍጹም ፡ ያውገረግራል ።

በማርክሲስቶችና ፡ በሥርዓተ-አልበኞች ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ ልዩነት ፡ ይህ ፡ ነው — ፩. የመጀመሪያዎቹ (ማርክሲስቶች) ግባቸው ፡ መንግሥትን ፡ ፍጹም ፡ መደምሰስ ፡ ቢሆንም ፤ ይህ ፡ ዓላማ ፡ እግቡ ፡ የሚደርሰው ፡ መንግሥት ፡ ከስሞ ፡ የሚጠፋው ፡ ሶሺያሊዝም ፡ ሲመሠረት ፤ ማለትም ፡ በሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ መደቦች ፡ ከተደመሰሱ ፡ በኋላ ፡ ብቻ ፡ መሆኑን ፡ ያውቃሉ ። የኋለኞቹ ፡ መንግሥትን ፡ ለመደምሰስ ፡ የሚቻልበትን ፡ ሁኔታዎች ፡ ባለመረዳት ፡ ወድያውኑ ፡ በነጋታው ፡ ጨርሶ ፡ ለማውደም ፡ ይሻሉ ። ፪. የመጀመሪያዎቹ ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ የፖለቲካ ፡ ሥልጣን ፡ ከጨበጠ ፡ በኋላ ፡ አሮጌውን ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ በፍጹም ፡ በመሰባበር ፡ በቦታው ፡ የታጠቁ ፡ ወዝ ፡ አደሮችን ፡ በያዘ ፡ በአዲስ ፡ ድርጅት ፤ በኮሙን ፡ ዓይነት ፡ መተካት ፡ ያስፈልጋል ፡ ብለው ፡ ያምናሉ ። የኋለኞቹ ፡ የመንግሥቱን፡ መኪና ፡ መደምሰስ ፡ ቢፈልጉም ፤ ወዝ ፡ አደሩ ፡ በዚህ ፡ ቦታ ፡ ምን ፡ እንደሚተካና ፡ አብዮታዊ ፡ ሥልጣኑን ፡ እንዴት ፡ እንደሚጠቀምበት ፡ በፍጹም ፡ ግልፅ ፡ ሀሳብ ፡ የላቸውም ። ሥርዓተ-አልበኞች ፡ አብዮታዊ ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ የመንግሥትን ፡ ሥልጣን ፡ መጠቀም ፡ እንደሚገባው ፡ እንኳን ፡ ይክዳሉ ፤ የእሱን ፡ አብዮታዊ ፡ የበላይ ፡ ገዥነትም ፡

አይቀበሉም ። ፫. የመጀመሪያዎቹ ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ የአሁኑን ፡ መንግሥት ፡ በመጠቀም ፡ ለአብዮቱ ፡ ይዘጋጅ ፡ ብለው ፡ ይጠይቃሉ ። ሥርዓተ-አልበኞች ፡ ይህን ፡ አይቀበሉም ።

በዚህ ፡ ክርክር ፡ ማርክሲዝም ፡ የሚከተለው ፡ ካውትስኪይ ፡ ሳይሆን ፡ ፓኔኩክ ፡ ነው ። ምክንያቱም ፡ ማርክስ ፡ እንዳስተማረው ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ ሥልጣን ፡ መቀዳጀት ፣ እንዲሁ ፡ በቀላሉ ፡ አሮጌውን ፡ የመንግሥት ፡ አውታር ፡ በአዲሶቹ ፡ እጆች ፡ ማስገባት ፡ ማለት ፡ አይደለም ፣ ይህንን ፡ አውታር ፡ መስበር ፣ መደቆስ ፡ እንጂ ።

ካውትስኪይ ፡ ማርክሲዝም ፡ በመተው ፡ ወደ ፡ አድርባይነት ፡ ምሽግ ፡ ይኮበልላል ፣ ምክንያቱም ፡ ይህ ፡ አድርባዮች ፡ ፍጹም ፡ የማይቀበሉትን ፣ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ መደምሰስ ፡ አለበት ፡ የሚለውን ፡ በክርክሩ ፡ ውስጥ ፡ በፍጹም ፡ የለም ። እንደዚሁም « ድል ፡ መቀዳጀት » የሚለውን፡ ሥልጣኑን ፡ በብዙሀን ፡ እጆች ፡ ማስገባት ፡ ማለት ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ስለሚተረጉመው ፡ ለአድርባዮች ፡ ቀዳዳ ፡ ይተውላቸዋል ።

ካውትስኪይ ፡ ማርክሲዝምን ፡ መጠምዘዙን ፡ ለመሸፋፈን ፡ ጥራዝ ፡ ነጠቅ ፡ ለመሆን ፡ ይሞክራል ፣ ከማርክስም « ጥቅስ » ይደረድራል ። በ ፲፰፻፵፱ ዓ. ም. ማርክስ ፡ ሲጽፍ « ቁርጠኛ ፡ የሥልጣን ፡ ማእከላዊነት ፡ ኃይል ፡ በመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ እጅ ፡ መሆን »[49] አስፈላጊ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ነበር ። ካውትስኪይም ፡ ድል ፡ የመታ ፡ ይመስል ፣ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ይጠይቃል ፡ — ፓኔኩክ « ሴንትራሊዝምን » (« ዋህድነትን ») ለመደምሰስ ፡ ይፈልጋልን?

ይህ ፡ እንኳ ፣ ልክ ፡ ቤርንስተይን ፡ ፌደራሊዝም ፡ ሴንትራሊዝምን ፡ ይቃረናል ፡ በሚለው ፡ ጉዳይ ፡ ላይ ፡ ባላቸው ፡ አስተያየት ፡ ማርክሲዝምና ፡ ፕሩዶኒዝም ፡ አንድ ፡ ናቸው ፡ ብሎ ፡ እንዳቀረበው ፡ ማታለያ ፡ ይመስላል ።

ካውትስኪይ ፡ የወሰደው « ጥቅስ » ለዚህም ፡ ሆነ ፡ ለዚያ ፡ አይበጅም ፡ [illegible] ሆነ ፡ በአዲሱ ፡ የመን





ግሥት ፡ መኪና ፡ ይቻላል ። ወዝ ፡ አደሮች ፡ በፈቃዳቸው ፡ የትጥቅ ፡ ኃይሎቻቸውን ፡ ቢያስተባብሩ ፣ ይህ ፡ ዋህድነት ፡ ይሆናል ፣ ነገር ፡ ግን ፡ይህ ፡ የሚመሠረተው ፡ ማእከላዊውን ፡ የመንግሥት ፡ አውታር ፡ ቋሚውን ፡ ወታደር ፣ ፖሊሱን ፣ ቢሮክራሲን « ፍጹም ፡ በመደምሰስ » ነው ። ካውትስኪይ ፡ እዚህ ፡ ላይ ፡ ስለኮሙን ፡ በጣም ፡ የታወቁትን ፡ የማርክስና ፡ የኤንግልስ ፡ አስተያየቶችን ፡ በማግለል ፣ ከጥያቄው ፡ ጋር ፡ ግንኙነት ፡ የሌለውን ፡ ጥቅስ ፡ በመደንጐር ፡ በጣም ፡ ያጭበረብራል ።

ካውትስኪይ ፡ በመቀጠል ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፣ « ... ምናልባት ፡ ፓኔኩክ ፡ የመንግሥትን ፡ ባለሥልጣኖች ፡ ተግባሮች ፡ ለመደምሰስ ፡ ይፈልግ ፡ ይሆን? — ነገር ፡ ግን ፡ በመንግሥቱ ፡ አስተዳደር ፡ ይቅርና ፡ በፓርቲና ፡ በሙያ ፡ ድርጅቶች ፡ እንኳን ፡ ሳይቀር ፡ ያለ ፡ ባለሥልጣኖች ፡ ልንሠራ ፡ አንችልም ። ፕሮግራማችን ፡ የሚጠይቀው ፡ የመንግሥት ፡ ባለሥልጣኖች ፡ እንዲደመሰሱ ፡ ሳይሆን ፣ በሕዝብ ፡ እንዲመረጡ ፡ ነው ፡ እንጂ ... እዚህ ፡ ላይ ፡ አሁን ፡ የምንወያየው « የወደፊቱ ፡ መንግሥት » የአስተዳደር ፡ ድርጅት ፡ ስለሚይዘው ፡ ቅርፅ ፡ ሳይሆን ፣ « የመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ ከመያዛችን ፡ በፊት » (ስርዝ ፡ የካውትስኪይ) የፖለቲካ ፡ ትግላችን ፡ መንግሥቱን ፡ ሊደመስሰው ፡ ይችል ፡ እንደሆን ፡ ነው ። የትኛው ፡ የሚኒስቴር ፡ መሥሪያ ፡ ቤት ፡ ከነባለሥልጣኖቹ ፡ ለመደምሰስ ፡ ይቻላል?» ከዚያም ፡ የትምህርት ፣ የፍርድ ፣ የገንዘብና ፡ የጦር ፡ ሚኒስቴሮች ፡ ዝርዝር ፡ ይቀጥላል ። « የለም ፣ አገዛዙን ፡ በመቃወም ፡ በምናደርገው ፡ ትግላችን ፡ ከአሁኑ ፡ የሚኒስቴር ፡ መሥሪያ ፡ ቤቶች ፡ አንዱም ፡ አይወገድም ... አለመግባባትን ፡ ለማስወገድ ፡ በድጋሚ ፡ ልበለውና ... እዚህ ፡ ላይ ፡ የምንወያየው ፡ ድል ፡ አድራጊው ፡ ሶሺ

ያል-ዴሞክራቶች « ለወደፊቱ ፡ መንግሥት » ስለሚ ሰጡት ፡ ቅርፅ ፡ አይደለም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የአሁኑ ፡ መንግ ሥት ፡ በእኛ ፡ ቅዋሜ ፡ እንዴት ፡ እንደተለወጠ ፡ እን ጂ ።» (ገጽ ፡ ፻፷፰)

ይህ ፡ ግልፅ ፡ ማታለያ ፡ ነው ። ፓኔኩክ ፡ ያነሳው ፡ የአብዮትን ፡ ጥያቄ ፡ ነው ። የጽሑፉ ፡ አርእስትም ፡ ሆነ ፤ እላይ ፡ የተጠቀሱት ፡ ጥቅሶች ፡ ይህንን ፡ በግልፅ ፡ ያመለክታሉ ። ካውትስኪይ ፡ ወደ « ቅዋሜ » ጥያቄ ፡ እን ጣጥ ፡ በማለት ፡ አብዮታዊውን ፡ ርዕየት ፡ በአድርባይ ነት ፡ ይተካል ። እሱ ፡ የሚለው — በአሁኑ ፡ ጊዜ ፡ እኛ ፡ ተቃዋሚዎች ፡ ነን ፤ ሥልጣን ፡ ከያዝን ፡ በኋላ ፡ ምን ፡ እንደምንሆን ፡ እንወያይበታለን ። አብዮት ፡ ውሃ ፡ በላው! ልክ ፡ ይህንኑን ፡ ነው ፡ አድርባዮች ፡ የሚፈልጉት ።

አንገብጋቢው ፡ ጥያቄ ፡ በአጠቃላይ ፡ ቅዋሜ ፡ ወይም ፡ የፖለቲካ ፡ ትግል ፡ ሳይሆን ፡ አብዮት ፡ ነው ። የአብዮት ፡ ይዘት ፡ ወዝ ፡ አደሩ « የአስተዳደሩን ፡ አውታር » እና ፡ ጠቅላላውን ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ በማጥፋት ፤ በታጠቁ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ በተመሠረተ ፡ በአዲስ ፡ ድርጅት ፡ መተካ ትን ፡ ነው ። ካውትስኪይ « ለሚኒስቴሮች ፡ መሥሪያ ፡ ቤቶች » « መለኮታዊ ፡ አክብሮትን » ያሳያል ። ነገር ፡ ግን ፡ እነዚህ ፡ ፍጹም ፡ የበላይ ፡ ሥልጣን ፡ ባላቸው ፡ የወዝ ፡ አደርና ፡ የወታደር ፡ ተወካዮች ፡ ሶቪዬቶች ፡ ሥር ፡ በሚሠሩ፡ የባለሙያዎች ፡ ኮሚቴዎች ፡ ለምን ፡ ሊተኩ ፡ አይችሉም?

የነጥቡ ፡ ፍሬ ፡ ነገር ፡ ፈጽሞ « ስለ ፡ ሚኒስትሮች ፡ መሥ ሪያ ፡ ቤቶች ፡ ማቆየት ፤ ወይስ ፡ ስለ « ባለሙያዎች ፡ ኮሚቴ ዎች » ወይም ፡ ሌሎች ፡ አካሎች ፡ ስለ ፡ መመሥረት ፡ አይ ደለም ። ይህ ፡ ፍጹም ፡ ዋጋ ፡ የለውም ። የነጥቡ ፡ ፍሬ ፡ ነገር ፡ የመንግሥቱ ፡ መኪና (ከቡርዧዋው ፡ ጋር ፡ በሺህ ፡ ክር ፡ የተሳሰረውና ፡ በእለታዊ ፡ ተግባሩም ፡ ሆነ ፡ በማን ኛውም ፡ [illegible] ፡ የ[illegible] መቆየት ፡ አለበት ፡





ወይስ ፡ ተደምስሶ ፡ በሌላ ፡ በአዲስ ፡ መተካት ፡ አለበት ፡ ነው ። የአብዮቱ ፡ ዋና ፡ ይዘት ፡ አዲሱ ፡ መደብ ፡ በአሮጌው ፡ የመንግስት ፡ መኪና ፡ እየተጠቀመ ፡ እንዲገዛና ፡ እንዲያ ስተዳድር ፡ አይደለም ፤ ዋና ፡ ይዘቱ ፡ አዲሱ ፡ መደ ብ ፡ ይህን ፡ መኪና ፡ በመደምሰስ ፤ በአዲስ ፡ መኪና ፡ እየተገለገለ ፡ እንዲገዛና ፡ እንዲያስተዳድር ፡ ነው ፤ — ይህ ን ፡ የማርክሲዝምን ፡ መሠረታዊ ፡ ሀሳብ ፡ ነው ፡ ካውትስ ኪይ ፡ ያውገረገረው ፤ ወይም ፡ በፍጹም ፡ ያልገባው ።

ስለ ፡ ባለሥልጣኖች ፡ ጥያቄ ፡ ማቅረቡ ፡ በግልፅ ፡ የሚ ያሳየው ፤ የኮሙን ፡ ትምህርቶችና ፡ የማርክስ ፡ ትምህ ርት ፡ እንዳልገባው ፡ ነው ። « ያለ ፡ ባለሥልጣኖች ፡ በፓ ርቲም ፡ ሆነ ፡ በሙያ ፡ ማኅበሮች ፡ ልንሠራ ፡ አንችልም... »

በካፒታሊዝም ፡ ሥር ፤ በቡርዧዋ ፡ አገዛዝ ፡ ሥር ፡ ያለ ፡ ባለሥልጣኖች ፡ ለመሥራት ፡ አንችልም ። በካፒ ታሊዝም ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ ተበዝብዘዋል ፤ ሰፊ ፡ ሠር ቶ-አደሮች ፡ ባሪያ ፡ ሆነዋል ። በካፒታሊዝም ፡ ሥር ፡ ዴሞ ክራሲ ፡ በጠቅላላው ፡ የቅጥር ፡ ባርነት ፡ ሁኔታዎች ፡ በሰፊ ው ፡ ህዝብ ፡ ችግርና ፡ ድህነት ፡ ጠቧል ፤ ተጨማዷል ፤ ተጐራርዷል ፤ ተቆነፃፅሏል ። ለዚህ ፡ ነው ፤ ለዚህም ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ የኛ ፡ የፖለቲካና ፡ የሙያ ፡ ማኅበር ፡ ድርጅ ቶች ፡ ሥራ ፡ አስኪያጅ ፡ መሪዎች ፡ በካፒታሊዝም ፡ ሁኔ ታዎች ፡ ብልሹ ፡ የሚሆኑት (ወይም ፡ በትክክል ፡ ለመና ገር ፤ ብልሹ ፡ ለመሆን ፡ የሚያዘነብሉት) ፤ ቢሮክራቶች ፡ ማለ ትም ፡ ከሰፊው ፡ ሕዝብ ፡ የተነጠሉ ፤ ከሰፊው ፡ ሕዝብ ፡ በላይ ፡ በመቆም ፡ ያለአግባብ ፡ ተጠቃሚ ፡ ሰዎች ፡ ለመሆ ን ፡ የሚያዘነብሉት ።

ይህ ፡ ነው ፡ የቢሮክራሲ ፡ ውስጠ ፡ ነገር ፤ እና ፡ ካፒታ ሊስቶች ፡ እስካልተወረሱ ፡ ድረስ ፤ ቡርዧዋው ፡ እስካል ተገለበጠ ፡ ድረስ ፤ የወዝ ፡ አደሩ ፡ ሥራ ፡ አስኪያጆች ፡ እንኳ ፡ ሳይቀሩ ፡ እስከተወሰነ ፡ ደረጃ ፡ ድረስ « ቢሮክራሲ ያዊ » መሆናቸው ፡ ነው ።

እንደ ፡ ካውትስኪይ ፡ ከሆነ ፤ በሶሺያሊዝም ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ የተመረጡ ፡ ሥራ ፡ አስኪያጆች ፡ ስለሚኖሩ ፤ ባለሥልጣኖችም ፡ ይኖራሉ ፤ ቢሮክራሲም ፡ ይኖራል! የተሳሳተበት ፡ ልክ ፡ እዚህ ፡ ላይ ፡ ነው ። ማርክስ ፡ በተለይ ፡ የኮሙን ፡ ምሳሌን ፡ በመጥቀስ ፡ ያሳየው ፡ በሶሺያሊዝም ፡ ሥር ፡ ባለሥልጣኖችን ፡ መምረጥ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፤ በማንኛውም ፡ ጊዜ ፡ የመሻር ፡ መለወጥም ፡ መርህ ፡ እንደዚሁ ፡ ስለሚታወቅ ፤ እንደዚሁም ፡ የሚከፈላቸው ፡ በአማካይ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ ደመወዝ ፡ ያህል ፡ ልክ ፡ ስለሚል ፤ በተጨማሪም ፡ ፓርላማዊ ፡ ተቋሞች « በሚሠሩ ፤ ማለት ፡ ሕግ ፡ በሚያወጡና ፡ ሕግ ፡ በሚያስፈፅሙ ፡ አካሎች » ስለሚተኩ ፤ እነዚህ ፡ በሥራ ፡ ላይ ፡ በዋሉ ፡ መጠን ፡ ሥራ ፡ አስኪያጆች « ቢሮክራቶች » መሆናቸው ፡ ቀርቶ ፤ « ባለሥልጣኖች » መሆናቸው ፡ ያከትማል ።[50]

በመሠረቱ ፡ የካውትስኪይ ፡ በፓኔኩክ ፡ ላይ ፡ ጠቅላላ ፡ ክርክር ፤ በተለይም ፡ በፓርቲያችንም ፡ ሆነ ፡ በሙያ ፡ ድርጅቶቻችን ፡ ያለ ፡ ባለሥልጣኖች ፡ መሥራት ፡ አንችልም ፡ የሚለው ፡ የካውትስኪይ ፡ የሚያስገርም ፡ ሀሳቡ ፡ የሚያሳየው ፡ ቤርንስተይን ፡ ማርክሲዝም ፡ በአጠቃላይ ፡ የተቃረነባቸው ፡ አሮጌ « ሀሳቦች » በካውትስኪይ ፡ መደገማቸውን ፡ ነው ። ቤርንስተይን « የሶሺያሊዝም ፡ ተቀዳሚ ፡ ሁኔታዎች » በሚለው ፡ የክህደት ፡ መጽሐፉ « ጥንታዊ » ዴሞክራሲን ፡ ይቃወማል ፤ « የስብከት ፡ ዴሞክራሲ » ብሎ ፡ የሚጠራውን ፤ ማለትም ፡ የታወቀ ፡ ሥልጣን ፡ የተሰጣቸው ፡ ተወካዮችን ፤ የማይከፈሉ ፡ ባለሥልጣኖችን ፤ ደካማ ፡ ማእከላዊ፡ የውክልና ፡ ድርጅቶችን ፡ ወዘተ ፤ ይቃወማል ። ይህ፤«የጥንታዊው » ዴሞክራሲ ፡ ፍሬ ፡ቢስ ፡ ነው ፡ ብሎ ፤ በርንስተይን ፡ የእንግሊዝ ፡ የሙያ ፡ ማኅበር ፡ ልምድን ፤ ባልና ፡ ሚስቱ ፡ ዌቦች ፡ [51] በተረዱት ፡ ዓይነት ፤ ይጠቅሳል ። በሰባው ፡ ዓመታት « ፍጹም ፡ ነፃነት » (ገጽ ፡ ፲፻፪ ፤ የጀርመን ፡ እትም) እድገት ፡ የሙያ ፡ ማኅበሮች ፡ የጥ [illegible] ስለተረዱ ፤ በተለመ



ደው ፡ ዴሞክራሲ ፡ ማለትም ፡ ከቢሮክራሲ ፡ ጋር ፡ በተሳሰረው ፡ ፓርላማ ፡ ተኩት ፡ ይላል ።

እንደ ፡ እውነቱ ፡ ከሆነ ፡ የሙያ ፡ ማኅበራት ፡ ያደጉት « በፍጹም ፡ ነፃነት » አይደለም ፤ ፍጹም ፡ ካፒታሊስታዊ ፡ ባርነት ፡ በሰፈነበት ፡ ሥርዓት ፡ እንጂ ። በዚህ ፡ ሥርዓት ፡ ሥር ፡ ላንሰራራው ፡ ግፈኝነት ፤ አመፅ ፤ ውሸት ፤ « ከከፍተኛ » የአስተዳደር ፡ ጉዳይ ፡ ድሆችን ፡ ለማስወገድ ፡ የተወሰነ ፡ ማፈግፈግ ፡ ሳያደርጉ « መሄድ ፡ እንደማይቻል » ግልፅ ፡ ነው ። በሶሺያሊዝም ፡ ሥር « የጥንታዊው » ዴሞክራሲ ፡ ብዙ ፡ ነገር ፡ መታደሱ ፡ የማይቀር ፡ ነው ፤ ምክንያቱም ፡ በሰለጠነው ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ታሪክ ፡ ውስጥ ፡ ለመጀመሪያ ፡ ጊዜ ፡ ሰፊው ፡ ሕዝብ ፡ በድምፅ ፡ መስጠትና ፡ በምርጫ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፤ በመንግሥቱ ፡ አስተዳደርም ፡ ጭምር ፡ ድረስ ፡ ነፃ ፡ የሆነ ፡ ተሳትፎው ፡ ከፍ ፡ ስለሚል ፡ ነው ። በሶሺያሊዝም ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ሁሉም ፡ በየተራቸው ፡ ስለሚያስተዳድሩ ፤ ወድያውኑ ፡ ያለ ፡ አንድ ፡ አስተዳዳሪ ፡ መኖርን ፡ ይለምዳሉ ።

ማርክስ ፡ በብሩህ ፡ ሂሳዊ-ትንተናዊ ፡ አእምሮው ፡ በኮሙኑ ፡ ተግባራዊ ፡ እርምጃዎች ፡ ያየውን ፡ የለውጥ ፡ ዋና ፡ ነጥብ ፤ አድርባዮቹ ፡ ከፈሪነታቸው ፡ የተነሳና ፡ ከቡርዥዋ ፡ ጋር ፡ በማያዳግም ፡ ለመለያየት ፡ ስለማይሹ ፡ ይፈሩታል ፤ ለማወቅም ፡ አይፈልጉም ። ሥርዓተ-አልበኞችም ፡ እንደዚሁ ፡ ወይ ፡ በመቸኮል ፡ ወይም ፡ በጠቅላላው ፡ ሰፊ ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ የለውጥ ፡ ሁኔታዎች ፡ ፈጽሞ ፡ ባለመረዳታቸው ፡ ምክንያት ፡ ለማየት ፡ አይፈልጉም ። ሁለመናው ፡ በጮርቃነት ፡ የተጥለቀለቀውና ፤ በሥረ ፡ መሠረቱም ፤ በአብዮትና ፡ በአብዮቱ ፡ ህያው ፡ ኃይል ፡ የማያምን ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፤ እንደዚሁም ፡ አብዮቱን ፡ ዘለአለም ፡ እንደሞት ፡ የሚፈራው ፡ አድርባይ (የኛዎቹ ፡ ሜንሼቪኮችና ፡ [5] ሶሺያሊስት-አብዮታውያን[4] ፡ እንደሚፈሩት ፡ ሁሉ) ሲከራከር « አሮጌውን ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ ለመደምሰስ ፡





ማሰብም ፡ እንኳን ፡ አይገባም ፤ ለመሆኑ ፡ ያለ ፡ ሚኒስቴሮችና ፡
ያለ ፡ ባለሥልጣኖች ፡ እንዴት ፡ ልንሠራ ፡ እንችላለን?» ይላል ።

ሥርዓተ-አልበኛው (ክሮፖትኪንንና ፡ መሰሎቹን ፡ በመ
ከተል ፡ ከቡርዥዋው ፡ ጀርባ ፡ የሚጎተቱት ፡ ሳይሆኑ ፡
በእርግጥ ፡ ከሥርዓተ-አልበኞቹ ፡ ዋነኛው) ሲከራከር « ማሰ
ብ ፡ ያለብን ፡ አሮጌውን ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ ለማጥ
ፋት ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ በተረፈ ፡ ግን ፡ የቀድሞዎቹን ፡ የወዝ ፡
አደር ፡ አብዮቶች ፡ ተጨባጭ ፡ ትምህርቶችን ፡ ጠልቆ ፡
መመርመርና ፡ የተደመሰሰው ፡ በምንና ፡ እንዴት ፡ እንደ
ሚተካ ፡ መተንተን ፡ ጥቅም ፡ የለውም » ይላል ። ስለዚ
ህም ፡ የሥርዓተ-አልበኞቹ ፡ ታክቲክ ፡ የተስፋ ፡ መቁረጥ ፡
ታክቲክ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ የሰፊውን ፡ ሕዝብ ፡ ንቅናቄዎ
ች ፡ ተግባራዊ ፡ ሁኔታዎችን ፡ በመገንዘብ ፡ የተጨበጡ ፡
ችግሮችን ፡ ለማቃለል ፡ የማያወላውል ፡ ድፍረት ፡ ያለው ፡
አብዮታዊ ፡ ጥረት ፡ አይደለም ።

ማርክስ ፡ ሁለቱንም ፡ ስህተቶች ፡ እንድናስወግድ ፡
ያስተምረናል ፤ አሮጌውን ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ በሞላ ፡ በ
ታላቅ ፡ የድፍረት ፡ እርምጃ ፡ እንድንደመስስ ፡ ያስተምረናል ፤
በተጨማሪም ፡ የሚያስተምረን ፡ ጥያቄውን ፡ በትክክል ፡
እንድናስቀምጠው ፡ ነው ፤ ኮሙኑ ፡ በጥቂት ፡ ሳምንታት ፡
ጊዜ ፡ ውስጥ ፡ ይህንና ፡ ይህንን ፡ የመሰሉ ፡ እርምጃዎችን ፡
በመውሰድ ፡ ሰፊ ፡ ዴሞክራሲን ፡ ለማጐናፀፍና ፡ ቢሮክራ
ሲን ፡ ከሥሩ ፡ ለመንቀል ፡ አዲስ ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ መንግ
ሥት ፡ መኪና ፡ መገንባት ፡ ጀመረ ። ከኮሙን ፡ ጀግኖች ፡
አብዮታዊ ፡ ደፋርነትን ፡ መማር ፡ አለብን ፤ በገቢራዊ ፡
እርምጃዎቻቸው ፡ በእውነት ፡ አጣዳፊና ፡ ወድያውኑ ፡
ለመውሰድ ፡ የሚቻሉ ፡ የተግባራዊ ፡ እርምጃዎች ፡ ቅይስ ፡
መስመርን ፡ እንመለከት ፤ ከዚያም ፡ ይህን ፡ መንገድ ፡ በመከተ
ል ፡ የቢሮክራሲ ፡ ፍጹም ፡ መደምሰስ ፡ ድል ፡ እንጐናፀፋለን ።

ይህ ፡ መደምሰስ ፡ የሚቻል ፡ ሊሆን ፡ ዋስትና ፡ ያለው ፡
ሀቅ ፡ [illegible] ፡ የሥራ ፡ ሰዓትን ፡






ስለሚያሳጥር ፤ ሰፊውን ፡ ሕዝብ ፡ ወደ ፡ አዲስ ፡ የኑሮ ፡
ሁኔታ ፡ ስለሚያሳድግ ፤ አንድም ፡ ሳይቀር ፡ እያንዳንዱ ፡ ሰው
በ« መንግሥቱ ፡ ተግባሮች » እንዲካፈል ፡ የሚያስችሉትን ፡
ሁኔታዎች ፡ ለአብዛኛው ፡ ምልአተ ፡ ሕዝብ ፡ ስለሚፈጥ
ርና ፤ ይህም ፡ እያንዳንዱን ፡ የመንግሥት ፡ ቅርፅ ፡ በአጠ
ቃላይ ፡ ወደ ፡ ፍጹም ፡ መክሰም ፡ ስለሚያመራ ፡ ነው ።

« ... የሰፊው ፡ ሕዝብ ፡ አድማ ፡ ዓላማ ፡ መምታት »
ይላል ፡ ካውትስኪይ ፡ በመቀጠል « ምን ፡ ጊዜም ፡
ቢሆን ፡ የመንግሥትን ፡ ሥልጣን ፡ ለመደምሰስ ፡
ሊሆን ፡ አይችልም ። ዓላማው ፡ ሊሆን ፡ የሚችለው ፡
አገዛዙ ፡ በአንዳንድ ፡ በተወሰኑ ፡ ጥያቄዎች ፡ ላይ ፡
ለቀቅ ፡ እንዲል ፤ ወይም ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ ጠላት ፡ አገ
ዛዝን ፡ በሌላ ፤ ለወዝ ፡ አደሩ ፡ በበለጠ ፡ በሚቸር ፡ አገ
ዛዝ ፡ ለመተካት ፡ ብቻ ፡ ነው (entgegenkommende)...
ይሁን ፡ እንጂ ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ ቢሆን ፤ በምንም ፡ ዓይ
ነት ፡ ሁኔታ ፡ ይህ » (ማለት ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ በጠላት ፡
አገዛዝ ፡ ላይ ፡ ድል ፡ መምታት) « የመንግሥትን ፡
ሥልጣን ፡ ወደ ፡ መደምሰስ ፡ ሊመራን ፡ አይችልም ።
ሊያመጣ ፡ የሚችለው ፤ እስከተወሰነ ፡ ደረጃ ፡ ድረስ ፤
በመንግሥቱ ፡ ሥልጣን ፡ ውስጥ ፡ የኃይሎች ፡ ግንኙ
ነት ፡ መለዋወጥ (Verschiebung) ብቻ ፡ ነው ...
ስለዚህም ፡ የፖለቲካ ፡ ትግላችን ፡ ዓላማ ፤ እስከዛሬ ፡
ድረስ ፡ እንደነበረው ፡ ሁሉ ፤ በፓርላማ ፡ ውስጥ ፡ አብ
ዛኛውን ፡ ድምፅ ፡ በማግኘት ፡ የመንግሥት ፡ ሥል
ጣንን ፡ መጨበጥና ፡ ፓርላማውን ፡ በመንግሥቱ ፡
ላይ ፡ የበላይ ፡ እንዲሆን ፡ ማድረግ ፡ ይሆናል ። »
(ገጽ ፡ ፫፻፷፯ ፤ ፫፻፷፱ ፤ ፫፻፵፪)

ይህ ፡ የለየለትና ፡ በጣም ፡ ወራዳ ፡ የሆነ ፡ አድርባይ
ነት ፡ ነው ፤ ይህ ፡ አብዮትን ፡ በቃላት ፡ እየተቀበሉ ፡ በተግ

ባር ፡ ግን ፡ መካድ ፡ ማለት ፡ ነው ። የካውትስኪይ ፡ ሀሳብ « ለወዝ ፡ አደሩ ፡ በበለጠ ፡ የሚቸር ፡ አገዛዝ » ከሚለው ፡ በላይ ፡ አይሄድም ። ይህ ፡ በ ፲፰፻፺፯ ዓ. ም. « የኮሙኒስት ፡ ማኒፌስቶ » « ወዝ ፡ አደሩን ፡ እንደገዥ ፡ መደብ ፡ ማደራጀት »ብሎ ፡ ካወጀው ፡ ጋር ፡ ሲወዳደር ፡ አንድ ፡ እርምጃ ፡ ወደኋላ ፤ ወደጮርቃነት ፡ ነው ።

ካውትስኪይ « ለወዝ ፡ አደሩ ፡ በበለጠ ፡ ቸር ፡ ለሚሆን » አገዛዝ ፡ ለመዋጋት ፡ ከሚስማሙት ፡ ከነ ፡ ሸይደማኖች ፤ ፕሌኻኖቮች ፤ ቫንደርቬልዶች ፡ ጋር ፡ ተወዳጅ « አንድነትን » ማግኘት ፡ አለበት ።

እኛ ፡ ግን ፡ ከነዚህ ፡ የሶሺያሊዝም ፡ ከሀዲዎች ፡ ፍጹም ፡ በመነጠል ፡ አሮጌው ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ ፈጽሞ ፡ እንዲደመሰስና ፡ የታጠቀው ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ራሱ ፡ መንግሥት ፡ እንዲሆን ፡ መዋጋት ፡ አለብን ። እነዚህ « ትልቅ ፡ ልዩነት ፡ ያላቸው ፡ ሁለት ፡ ነገሮች ፡ ናቸው ። »

ካውትስኪይ « በመንግሥቱ ፡ ሥልጣን ፡ ውስጥ ፡የኃይሎች ፡ ግንኙነትን ፡ ለመለዋወጥ » ፤ « በፓርላማ ፡ ውስጥ ፡ አብዛኛውን ፡ ድምፅ ፡ ለማግኘትና ፡ ፓርላማውን ፡ የመንግሥቱ ፡ የበላይ ፡ እንዲሆን ፡ ለማድረግ » ለመታገል ፡ ፍጹም ፡ ፈቃደኛ ፡ ከሆኑት ፡ ከነ ፡ ሌጊኖችና ፡ ዳቪዶች ፤ ከፕሌኻኖቮች ፤ ፖትሬሶቮች ፤ ጸረተሊዎች ፤ ቼርኖቮች ፡ ቡድን ፡ ጋር ፡ ባለው ፡ ጓደኝነት ፡ ሊደሰት ፡ ይገባል ። ይህም ፡ የተከበረ ፡ ዓላማ ፡ አድርባዮች ፡ ሙሉ ፡ በሙሉ ፡ የሚቀበሉትና ፡ ሁሉም ፡ ነገር ፡ በቡርዥዋው ፡ ፓርላማዊ ፡ ሪፑብሊክ ፡ አድማስ ፡ ውስጥ ፡ የሚወሰን ፡ ነው ።

ነገር ፡ ግን ፡ እኛ ፡ ከአድርባዮች ፡ መነጠል ፡ አለብን ። መላው ፡ የመደብ ፡ ንቃት ፡ ያለው ፡ ወዝ ፡ አደርም « ለኃይሎች ፡ ግንኙነት ፡ መለዋወጥ » ሳይሆን ፤ ቡርዥዋውን ፡ ለመገልበጥ ፤ የቡርዥዋውን ፡ ፓርላማዊነት ፡ ለመደምሰስ ፤ ለኮሙን ፡ ዓይነት ፡ ዴሞክራሲያዊ ፡ ሪፑብሊክ ፤ ወይም ፡ [illegible] ፡ ተወካዮች ፡ ሶሺ





ዬቶች ፡ ሪፑብሊክ ፤ ለወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮታዊ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ ለመዋጋት ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ይሆናል ።

* * *

በዓለም ፡ አቀፍ ፡ ሶሺያሊዝም ፡ ውስጥ ፡ ከካውትስኪይ ፡ የባሱ ፡ የቀኝ ፡ መስመሮች ፡ ይገኛሉ ፤ እነሱም ፡ እንደ ፡ « ወርሃዊው ፡ ሶሺያሊስታዊ »[52] በጀርመን (ሌጊን ፤ ዳቪድ ፤ ኮልብና ፡ ብዙ ፡ ሌሎችም ፤ ከስካንዲናቪያኖቹ ፡ ስታውኒንግና ፡ ብራንቲንግ ፡ ጭምር) ፤ ዡረሲስቶች ፡[53] እና ፡ ቫንደርቬልድ ፡ በፈረንሳይና ፡ በቤልጅግም ፤ በኢጣልያው ፡ ፓርቲ ፡ የቀኝ ፡ ተወካይ ፡ የሆኑ ፡ ቱራቲ ፤ ትሬቭስና ፡ ሌሎችም ፤ ፋቢያኖች ፡[2] እና ፡ « ነፃዎቹ » (« ነፃ ፡ የሠራተኛ ፡ ፓርቲ » ፤ እንደ ፡ እውነቱ ፡ ግን ፡ ሁልጊዜ ፡ በሊበራሎች ፡ ሥር ፡ ጥገኛ ፡ የነበረው) በእንግሊዝ ፡ አገር ፤ [54]እናም ፡ መሰሎቻቸው ፡ ናቸው ። እነዚህ ፡ በፓርላማ ፡ ሥራና ፡ በፓርቲዎቻቸው ፡ ጽሑፍ ፡ ታላቅና ፡ አብዛኛውን ፡ ጊዜ ፤ ከፍተኛውን ፡ ሚና ፡ የሚጫወቱት ፡ ጌቶች ፡ በሞላ ፤ የወዝ ፡ አደሩን ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ በቀጥታ ፡ በመካድ ፡ ግልጽ ፡ የሆነ ፡ የአድርባይነት ፡ መመሪያ ፡ ይከተላሉ ። በእነዚህ ፡ ጌቶች ፡ አስተያየት ፡ የወዝ ፡ አደሩ « የበላይ ፡ ገዥነት » ዴሞክራሲን « ይቃረናል »!! በእርግጥም ፡ በነሱና ፡ በንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ዴሞክራቶች ፡ መካከል ፡ መሠረታዊ ፡ ልዩነት ፡ ፈጽሞ ፡ የለም ።

ይህን ፡ ሁኔታ ፡ በመገንዘብ ፡ ሁለተኛው ፡ ኢንተርናሽናልን ፡ በአጥለቀለቁት ፡ አብዛኞቹ ፡ ሕጋዊ ፡ ተጠሪዎች ፡ አማካይነት ፡ ወደ ፡ አድርባይነት ፡ ፍጹም ፡ ሰጥመዋል ፡ ብለን ፡ መደምደሚያ ፡ ለመስጠት ፡ በቂ ፡ ምክንያት ፡ አለን ። የኮሙን ፡ ልምድ ፡ መረሳት ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፤ ተጠምዝዟልም ። ለሰፊው ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ እርምጃ ፡ በመውሰድ ፡ አሮጌውን ፡ የመንግሥት ፡ መኪና ፡ ደቁሶ ፡ በሌላ ፡ በአዲስ ፡

የሚተካበት ፡ ጊዜ ፡ መቃረቡን ፤ በዚህም ፡ መንገድ ፡ የፖለቲካ ፡ ግዛታቸው ፡ ኀብረት ፡ ሰቡን ፡ በሶሺያሊስት ፡ ሥርዓት ፡ ለማቀነባበር ፡ መሠረት ፡ የሚያደርጉበት ፡ ጊዜ ፡ መቃረቡን ፡ አላስረዱትም ፤ እንደያውም ፡ ለሰፊው ፡ ሕዝብ ፡ የተሰበከው ፡ ተቃራኒው ፡ ሲሆን ፤ « ሥልጣን ፡ የመጨበጥን » ጉዳይ ፡ የቀረበው ፡ ለአድርባይነት ፡ ሺህ ፡ ቀዳዳ ፡ በሚሰጥ ፡ ሁኔታ ፡ ነው ።

በኢምፔሪያሊስት ፡ ባላንጣነት ፡ ምክንያት ፡ የጠነከረ ፡ የጦር ፡ ድርጅት ፡ የነበራቸው ፡ መንግሥታት ፡ የጦር ፡ መናኸሪያ ፡ በመሆን ፤ እንግሊዝ ፡ ይግዛ ፡ ወይስ ፡ ጀርመን ፤ ይህኛው ፡ ወይንስ ፡ ያንኛው ፡ ፋይናንስ ፡ ካፒታል ፡ ዓለምን ፡ ይግዛ? የሚለውን ፡ ጥያቄ ፡ ለመመለስ ፡ በሚሊዮን ፡ የሚቆጠሩ ፡ ሰዎች ፡ በሚጨፈጨፉበት ፡ ጊዜ ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮት ፡ ከመንግሥት ፡ ጋር ፡ ያለውን ፡ ግንኙነት ፡ ጥያቄ ፡ መጠምዘዝና ፡ ማድበስበስ ፡ ታላቅ ፡ ሚና ፡ አልተጫወትም ፡ ለማለት ፡ አይቻልም* ።

« ምዕራፍ ፡ VII.

የ ፲፱፻፭ ዓ. ም. እና የ፲፱፻፲፯ ዓ. ም.

የሩሲያ ፡ አብዮቶች ፡ ልምድ ።

በዚህ ፡ ምዕራፍ ፡ የተጠቀሰው ፡ አርእስት ፡ በጣም ፡ ሰፊ ፡ በመሆኑ ፡ በዚሁ ፡ አርእስት ፡ ብዙ ፡ መጻሕፍት ፡ መጻፍ ፡ ይቻላል ፤ ይገባልም ። እርግጥ ፡ ነው ፤ በዚህ ፡ ድርሰት ፡ ውስጥ ፡ በቀጥታም ፡ በአብዮት ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ ተግባሮች ፡ ከመንግሥት ፡ ሥልጣን ፡ ጋር ፡ ያላቸውን ፡ ግንኙነት ፡ በሚመለከት ፡ ላይ ፡ እና ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ጠቃሚ ፡ በሆኑት ፡ የልምዱ ፡ ትምህርቶች ፡ ላይ ፡ ብቻ ፡ እንወሰናለን ።» (የእጅ ፡ ጽሑፉ ፡ እዚህ ፡ ላይ ፡ ይቋረጣል ።) (አዘጋጅው)

---

* (የእጅ ፡ ጽሑፉ ፡ እንደሚከተለው ፡ ይቀጥላል ፤







## ለመጀመሪያው ፡ እትም ፡ መደምደሚያ ።

ይህ ፡ ድርሰት ፡ የተጻፈው ፡ በ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. በነሐሴና ፡ በመስከረም ፡ ወራት ፡ ውስጥ ፡ ነው ። ለሚቀጥለው ፤ ለሰባተኛው ፡ ምዕራፍ « የ፲፱፻፭ ዓ. ም. እና ፡ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የሩሲያ ፡ አብዮቶች ፡ ልምድ » ፕላኑን ፡ አዘጋጅቻለሁ ። ይሁን ፡ እንጂ ፡ ከአርእስቶች ፡ በስተቀር ፡ በምዕራፉ ፡ አንድም ፡ መስመር ፡ ለመጻፍ ፡ ፋታ ፡ አላገኘሁም ፤ የፖለቲካ ፡ ቀውስ ፤ የ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የጥቅምቱ ፡ አብዮት ፡ ዋዜማ « አሰናከለኝ » ። አዎ ፤ በዚህ ፡ ዓይነት « መሰናከል » መደሰት ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ የሚቻለው ። ስለሆነም ፡ የጽሑፉ ፡ ሁለተኛውን ፡ ክፍል ፤ (« የ ፲፱፻፭ ዓ. ም. እና ፡ የ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የሩሲያ ፡ አብዮቶት ፡ ልምድ ») ምናልባትም ፡ ለረጅም ፡ ጊዜ ፡ ማቆየት ፡ ሊኖርብን ፡ ነው ። ስለሱ ፡ ከመጻፍ ፡ ይልቅ ፤ ይበልጥ ፡ የሚያስደስተውና ፡ የሚጠቅመው « የአብዮቱን ፡ ልምድ » ማድረጉን ፡ ነው ።

ደራሲው ።

ፔትሮግራድ ።*
ህዳር ፡ ፴ ፤ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. ።

---

* ፔትሮግራድ — አሁን ፡ ሌኒንግራድ ፡ ነው ። (አዘጋጅው)

## ማብራሪያዎች ።

1 « መንግሥትና ፡ አብዮት ። ስለ ፡ መንግሥትና ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ በአብዮት ፡ ውስጥ ፡ ስላለው ፡ ተግባሮች ፡ ማርክሳዊ ፡ ቴዎሪ ።» በሌኒን ፡ የተጻፈው ፡ በነሐሴና ፡ በመስከረም ፡ ወራት ፡ በ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. ፤ ከቡርዥዋው ፡ ጊዜያዊ ፡ መንግሥት ፡ በመሳደድ ፡ በህቡእ ፡ ተደብቆ ፡ ሳለ ፡ ነው ።

በወዝ ፡ አደሩ ፡ መንግሥታዊ ፡ ሥልጣን ፡ ባህሪ ፡ ጥያቄ ፡ ላይ ፡ ሌኒን ፡ በተለይ ፡ ያተኮረው ፡ በመጨረሻዎቹ ፡ የስደት ፡ ዓመታት ፡ ውስጥ ፡ ነው ። ሌኒን ፡ በ ፲፱፻፲፮ ዓ. ም. ሁለተኛ ፡ አጋማሽ ፡ ላይ ፡ የመንግሥት ፡ ጥያቄ ፡ ቴዎሪያዊ ፡ ማብራሪያ ፡ የሚያስፈልገው ፡ መሆኑን ፡ ተናግሮ ፡ ነበር ። በካውትስኪይና ፡ በዓለም ፡ አቀፍ ፡ አድርባይ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ ሥራዎች ፡ ውስጥ ፡ ማርክስ ፡ ስለ ፡ መንግሥት ፡ ያስተማረው ፡ በመጣመሙ ፤ ይህን ፡ መዋጋት ፡ አስፈላጊ ፡ መሆኑን ፡ ሌኒን ፡ ተገነዘበ ።

« ... አሁን ፡ የዛሬው ፡ ተቀዳሚ ፡ ተግባራችን » ይላል ፡ ሌኒን ፡ ለሽላፕኒኮቭ ፡ ሲጽፍ « የታወቀውን (በንጉሱና ፡ በመንግሥቱ ፡ ላይ) ፡ በውሳኔዎችና ፡ በፓምፍሌቶች ፡ ያለውን ፡ መስመር ፡ መቀጠል ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፤ ... እንደዚሁም ፡ [illegible] ክራሲ ፡ መፃረር



ንም (ከእነሱም ፤ ውጥረት ፡ ቅነሳን ፤ የራስን ፡ ዕድል ፡ በራስ ፡ የመወሰን ፡ መፃረርን ፤ በቴዎሪ ፡ ስህተተኛ ፡ በሆነ ፡ መንገድ ፡ የናት ፡ አገርን ፡ መከላከል « በአጠቃላይ » መፃረርን ፤ በአጠቃላይ ፡ የመንግሥትን ፡ ሚናና ፡ ትርጉምን ፡ በሚመለከት ፡ ጥያቄ ፡ ወለም ፡ ዘለም ፡ ከማለትና ፡ ከመሳሰሉ)ማንፃት ፡ ያስፈልጋት ።»

በ ፲፱፻፲፮ ዓ. ም. ሁለተኛ ፡ አጋማሽ ፡ ላይ ፡ ቡኻሪን ፡ በርከት ፡ ባሉ ፡ ጽሑፎቹ ፡ ውስጥ ፡ በመንግሥትና ፡ በወዝ ፡ አደሩ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ ላይ ፡ ፀረ-ማርክሳዊና ፡ ከፊል ፡ ሥርዓተ-አልበኛ ፡ ለሆኑ ፡ ርዕዮቶቹ ፡ ተከራክሯል ። በታህሳስ ፡ ፲፱፻፲፮ ዓ. ም. « የወጣቶች ፡ ኢንተርናሽናል » በተባለው ፡ ጽሑፉ ፡ ሌኒን ፡ የቡኻሪንን ፡ አቋም ፡ በጣም ፡ ወቅሷል ። ለወደፊቱም ፡ ማርክሲዝም ፡ በመንግሥት ፡ ላይ ፡ ስላለው ፡ አቋም ፡ ሰፊ ፡ ጽሑፍ ፡ እንደሚያቀርብም ፡ ተናግሮ ፡ ነበር ። በየካቲት ፡ ፬ (፲፯) ፤ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. ሌኒን ፡ ለሩሲያ ፡ አብዮተኛ ፡ ለኮሎንታይ ፡ በጻፈው ፡ መልእክት ፤ ማርክሲዝም ፡ በመንግሥት ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ አቋም ፡ በሚመለከት ፡ በቂ ፡ ትንተና ፡ ማዘጋጀቱን ፡ ጠቅሶላታል ። ጽሑፉን ፡ ያዘጋጀ ፡ በደብተር ፡ ቢጤ ፡ ሆኖ ፤ « ማርክሲዝም ፡ ስለ ፡ መንግሥት ፡ ጉዳይ » በሚል ፡ አርእስት ፡ ነበር ። በዚህ ፡ ጽሑፍ ፡ ውስጥ ፡ ከማርክስና ፡ ከኤንግልስ ፡ ሥራዎች ፡ የተወሰዱ ፡ ጥቅሶችና ፡ የሌኒን ፡ ሂሳዊ ፡ አስተያየቶች ፡ ያሏቸው ፤ ከካውትስኪይ ፤ ከፓኔኩክና ፡ ከቤርንስተይን ፡ መጻሕፍትና ፡ ጽሑፎች ፡ ጥቅሶችና ፡ እንዲሁም ፡ ደግሞ ፡ የሌኒን ፡ መደምደምያዎችና ፡ ትንተናዎች ፡ ይገኙበታል ።

ሌኒን « መንግሥትና ፡ አብዮት » የተባለው ፡ መጽሐፉን ፡ ሲጽፍ ፡ እነዚህ ፡ የሰበሰባቸውን ፡ አስተያየቶች ፡ እንደ ፡ መሠረት ፡ አድርጎ ፡ ተጠቅሞባቸዋል ።

በእቅዱ ፡ መሠረት « መንግሥትና ፡ አብዮት » ሰባት ፡ ምዕራፎች ፡ መያዝ ፡ ነበረበት ። ነገር ፡ ግን ፤ የመ

ጨረሻው ፤ ሰባተኛው ፡ ምዕራፍ « የ ፲፱፻፭ ዓ. ም. እና ፡ የ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የሩሲያ ፡ አብዮቶች ፡ ልምድ » ሌኒን ፡ አልጻፈውም ። በሰፊው ፡ የተቀነባበረ ፡ የዚህ ፡ አርእስት ፡ ፕላንና « የመደምደሚያ » ፕላን ፡ ትቶል ናል ። መጽሐፉ ፡ የታተመው ፡ ከጥቅምቱ ፡ ሶሺያሊ ስት ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ በ ፲፱፻፲፰ ዓ. ም. ነበር ። የእትሙ ፡ ብዛት ፡ ፴ ሺህ ፡ ፯፻ ነበር ።

መጽሐፉ ፡ ለሁለተኛ ፡ ጊዜ ፡ የታተመው ፡ በ ፲፱፻፲፱ ዓ. ም. ነው ። ደራሲው ፡ በሁለተኛው ፡ ምዕራፍ ፡ ውስ ጥ ፡ አዲስ « በ ፲፰፻፶፪ ዓ. ም. ማርክስ ፡ ጥያቄውን ፡ እንዳቀረበው » የሚል ፡ አርእስት ፡ ጨምሮበታል ።

ገጽ ፤ ፩

2 ፋቢያኖች — የፋቢያናዊ ፡ ማኅበር ፡ አባሎች — በ፲፰፻ ፹፬ ዓ. ም. የተመሠረተ ፡ የእንግሊዝ ፡ ሬፎርሚስቶች ፡ ድርጅት ። ማኅበሩ ፡ ስሙን ፡ ያገኘው ፡ ከክርስቶስ ፡ ልደት ፡ በፊት ፡ በ ፫፻ ኛው ፡ ምእት ፡ ዓመት ፡ በሮማ ፡ ከነበረው ፡ የጦር ፡ መሪ ፡ ስም ፤ ከፋቢይ ፡ ማክሲም ፡ ነው ። ከሀኒባል ፡ ጋር ፡ በተደረገው ፡ ጦርነት ፡ ቆራጥ ፡ ጦርነት ፡ ከመክፈት ፡ ባለመስማማቱ ፤ በማድፈጥ ፡ ታክ ቲኩ « ኩንክታተር » (« አዘጋሚ ») እየተባለ ፡ ይጠ ራል ። የፋቢያኖች ፡ ማኅበር ፡ አባሎች ፡ አብዛኞቹ ፡ የቡርዥዋ ፡ ምሁራን ፡ ሊቃውንት ፤ ደራሲያን ፤ የፖ ለቲካ ፡ ሰዎች ፡ ተወካዮች ፡ ነበሩ (ዌቦች ፤ ማክዶናልድ ፤ ሾውና ፡ ሌሎችም) ። እነሱም ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ የመደብ ፡ ትግልንና ፡ የሶሺያሊስት ፡ አብዮትን ፡ አስፈላጊነት ፡ አይቀበሉም ። በነሱ ፡ አስተሳሰብ ፡ ከካፒታሊዝም ፡ ወ ደ ፡ ሶሺያሊዝም ፡ ለመሸጋገር ፡ የሚቻለው ፡ በጠቃቅን ፡ ሬፎርሞች ፤ ቀስ ፡ በቀስ ፡ ኅብረተ ፡ ሰቡን ፡ በማሻሻል ፡ ብቻ ፡ ነው ። ሌኒን ፡ ፋቢያናዊነትን « የአድርባይነት ፡ አክ[illegible]ልያታል ። በ ፲፱፻



ዓ. ም. ፋቢያኖች ፡ ወደ ፡ ሌበር ፡ ፓርቲ ፡ ተቀላቅለ ዋል ። « ፋቢያናዊ ፡ ሶሺያሊዝም » ከሌበሮች ፡ የር ዕዮተ ፡ ዓለም ፡ ምንጮቻቸው ፡ አንዱ ፡ ነው ።

በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት (፲፱፻፲፬-፲፱፻፲፰ ዓ. ም.) አቋማቸው ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስቶች ፡ ነበሩ ።

ገጽ ፤ ፳ ፤ የ፹፩

3 የኤንግልስ « የቤተሰብ ፤ የግል ፡ ንብረትና ፡ የመንግ ሥት ፡ አመጣጥን » ተመልከት ።

ቀጥሎ ፡ ገጽ ፲፮-፲፯ ፤ ፲፱-፳፮ ሌኒን ፡ የሚጠቅሰው ፡ ይህንኑ ፡ የኤንግልስ ፡ ሥራ ፡ ነው ።

ገጽ ፤ ፲፪

4 ሶሺያሊስት-አብዮታውያን — በሩሲያ ፡ የንዑስ ፡ ቡርዥ ዋ ፡ ፓርቲ ፡ የተመሠረተው ፡ በ ፲፱፻፩ ዓ. ም. መጨረሻና ፡ በ ፲፱፻፪ ዓ. ም. መጀመሪያ ፡ ገደማ ፡ ላይ ፡ ነው ። በአንደ ኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ አብዛኞቹ ፡ ሶሺያሊስት-አብ ዮታውያን ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስቶች ፡ ነበሩ ።

ከ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የየካቲት ፡ የቡርዥዋ-ዴሞክራቲክ ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ ከሜንሼቪኮች ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ ላይ ፡ ሁነው ፡ የጊዜያዊው ፡ የቡርዥዋ ፡ መንግሥት ፡ ዋና ፡ ደጋፊዎች ፡ነበሩ ። የፓርቲው ፡ መሪዎች (ኬሬንስኪይ ፤ አቭክሴንትዬቭ ፤ ቼርኖቭ) የጊዜያዊው ፡ መንግሥት ፡ አባ ሎች ፡ ነበሩ ። የሶሺያሊስት-አብዮታውያን ፡ ፓርቲ ፡ የመ ሬት ፡ ከበርቴ ፡ ይውደም ፡ የሚለው ፡ የአርሶ ፡ አደሮች ፡ ጥያቄን ፡ አልደገፈም ። የመሬት ፡ ከበርቴ ፡ ይዞታ ፡ እንዳ ይነካ ፡ ተከራክሯል ። የጊዜያዊው ፡ መንግሥት ፡ ሶሺያ ሊስት-አብዮታውያን ፡ ሚኒስትሮች ፡ ከባላባቱ ፡ መሬት ፡ የነጠቁትን ፡ አርሶ ፡ አደሮች ፡ ለማስጨፍጨፍ ፡ ወታ ደሮች ፡ ልከዋል ። በጥቅምቱ ፡ የጦር ፡ አመፅ ፡ ዋዜማ ፡ ፓርቲው ፡ በግልፅ ፡ ወደ ፡ ፀረ-አብዮቱ ፡ ቡርዥዋ ፡ አቋ

ም ፡ ተሸጋግረዋል ፤ ለካፒታሊስትም ፡ ሥርዓት ፡ ታግለዋል፤ ስለሆነም ፡ ከአብዮታዊው ፡ ሰፊ ፡ ሕዝብ ፡ ተለይተዋል ።

በ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. በህዳር ፡ መጨረሻ ፡ ላይ ፡ የሶሺያሊስት ፡ አብዮታውያን ፡ ግራ ፡ ክንፍ ፡ ራሱን ፡ የቻለ ፡ የግራ ፡ ሶሺያሊስት-አብዮታውያን ፡ ፓርቲን ፡ አቋቁመዋል ። በሰፊ ፡ አርሶ ፡ አደሮች ፡ ተፅእኖአቸውን ፡ ለማጠንከር ፤ የግራ ፡ ሶሺያሊስት-አብዮታውያን ፡ ለይስሙላ ፡ የሶቪዬት ፡ መንግሥትን ፡ በማወቅ ፡ ከቦልሼቪኮች ፡ ጋር ፡ ተስማምተዋል ። ይሁን ፡ እንጂ ፡ ከጥቂት ፡ ጊዜ ፡ በኋላ ፡ የሶቪዬትን ፡ መንግሥት ፡ በመቃወም ፡ ታግለዋል ።

ገጽ ፤ ፲፫ ፤ ፳፫ ፤ ፵ ፤ ፻፸፫

5 ሜንሼቪኮች — በሩሲያ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ ውስጥ ፡ የንዑስ ፡ ቡርዥዋና ፡ የአድርባይ ፡ መስመር ፡ ተከታዮች ፡ ሲሆኑ ፤ የቡርዥዋን ፡ ተፅእኖ ፡ በወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ ላይ ፡ ለማሳደር ፡ ብዙ ፡ ታግለዋል ። ይህ ፡ ስም — ሜንሼቪክ — ያገኙት ፡ ከሁለተኛው ፡ በነሐሴ ፡ ፲፱፻፫ ዓ. ም. ከተደረገው ፡ የሩሲያ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ፓርቲ ፡ ጉባዔ ፡ በኋላ ፡ ነው ። በዚህ ፡ ጉባዔ ፡ መጨረሻ ፡ የፓርቲው ፡ ማእከላዊ ፡ አካሎች ፡ በሚመረጡበት ፡ ጊዜ ፡ እነሱ ፡ ጥቂቶች (ሜንሼንስትቮ ፡ ጥቂቶች ፤ ማለት ፡ ነው ፤ ሜንሼቪክ ፡ ከዚሁ ፡ ቃል ፡ የመጣ ፡ ነው) ነበሩ ፤ በሌኒን ፡ የሚመሩት ፡ አብዮታውያን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ ግን ፡ ብዙሀን (ቦልሼንስትቮ ፡ ማለት ፡ ነው) ነበሩ ። ከዚህ ፡ ነው ፡ ቦልሼቪክ (ቦልሼንስትቮ ፡ ከሚባለው ፡ የመጣ ፡ ነው) እና ፡ ሜንሼቪክ ፡ የሚሉት ፡ ስሞች ፡ የጀመሩት ።

ሜንሼቪኮች ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ ከቡርዥዋው ፡ ጋር ፡ እንዲስማማ ፡ በመጣር ፤ በወዝ ፡ አደሩ ፡ ንቅናቄ ፡ አድርባይ ፡ የሆነ ፡ መስመርን ፡ አካሂደዋል ። ከ ፲፱፻፲፯



ዓ. ም. የየካቲት ፡ የቡርዥዋ-ዴሞክራቲክ ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ ሜንሼቪኮች ፡ ከሶሺያሊስት-አብዮታውያን ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ ላይ ፡ ሁነው ፡ በጊዜያዊ ፡ መንግሥት ፡ ተሳትፈዋል ። የመንግሥቱን ፡ ኢምፔሪያሊስታዊ ፡ ፖለቲካን ፡ ደግፈዋል ፤ በመግፋት ፡ ላይ ፡ የነበረው ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮትን ፡ በመፃረር ፡ ታግለዋል ።

ከጥቅምቱ ፡ ሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ ሜንሼቪኮች ፡ በግልፅ ፡ ፀረ-አብዮታዊ ፡ ፓርቲ ፡ ሆነዋል ። የሶቪዬትን ፡ መንግሥት ፡ ለመጣል ፡ የሴራ ፤ የአድማ ፡ አዘጋጆችና ፡ ተካፋዮች ፡ ነበሩ ።

ገጽ ፤ ፲፫ ፤ ፳፫ ፤ ፵ ፤ ፷ ፤ ፻፱ ፤ ፻፸፫

6 የጋርዮሽ ፤ ኅሳዊ ፡ ሥርዓት — ጥንታዊ ፡ የጋርዮሽ ፡ ሥርዓት ፡ ማኅበር ፤ ወይም ፡ በሰው ፡ ዘር ፡ ታሪክ ፡ የመጀመሪያው ፡ ሶሽዮ-ኤኮኖሚክ ፡ ቅርፅ ፡ ነው ። ኅሳዊ ፡ ሕዝበ ፡ ማኅበር ፡ በደም ፡ የሚዛመዱ ፡ ሰዎች ፡ ክምችት ፡ ሲሆን ፤ እነሱም ፡ በኤኮኖሚና ፡ በሶሺያል ፡ የተሳሰሩ ፡ ናቸው ። ኅሳዊ ፡ ማኅበረ ፡ ሰብ ፡ በእድገቱ ፡ ሁለት ፡ ደረጃዎችን ፤ የናት ፡ ዘመንንና ፡ ያባት ፡ ዘመንን (ማትሪያርካልና ፡ ፓትሪያርካል) አልፎአል ። ያባት ፡ ዘመን ፡ ከፍተኛ ፡ ደረጃ ፡ የደረሰው ፡ ጥንታዊው ፡ የጋርዮሽ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ፈርሶ ፡ ወደ ፡ መደባዊ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ሲሸጋገርና ፡ መንግሥት ፡ ሲፈጠር ፡ ነው ። የጥንታዊው ፡ የጋርዮሽ ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ የምርት ፡ ግንኙነቱ ፡ መሠረት ፡ የነበሩት ፡ የምርት ፡ መገልገያዎች ፡ የኅብረተ ፡ ሰቡ ፡ ይዞታ ፡ መሆንና ፡ እኩል ፡ የምርት ፡ መከፋፈል ፡ ናቸው ። ይህ ፡ በመሠረቱ ፡ የሚያመለክተው ፡ የምርት ፡ ኃይሎችን ፡ ዝቅተኛ ፡ የእድገት ፡ ደረጃና ፡ በጊዜው ፡ የነበረው ፡ ባህርያቸውን ፡ ነው ።

ገጽ ፤ ፲፯



7 ይህ ፡ የሚያመለክተው ፡ የማርክሱ ፡ ሥራ ፡ « የጎታው ፡ ፕሮግራም ፡ ሂስ » (ክፍል ፡ IV) እና ፡ የኤንግልሱ ፡ « አንቲ-ዱሪንግግን » (« ፀረ-ዱሪንግግን ») ፤ እንደዚሁም ፡ በመጋቢት ፡ ፲፰-፳፰ ፤ ፲፰፻፸፭ ዓ. ም. ኤንግልስ ፡ ለቤቤል ፡ የጻፈውን ፡ ደብዳቤ ፡ ነው ።

ገጽ ፤ ፴፪

8 ማርክስ « ካፒታል » ቅፅ ፡ ፩ ን ፡ ተመልከት ።

ገጽ ፤ ፴፫

9 <u>የ ፲፮፻፲፰-፲፮፻፵፰ ዓ. ም. የሰላሳ ፡ ዓመቱ ፡ ጦርነት</u> — የመጀመሪያው ፡ የመላ ፡ አውሮፓ ፡ ጦርነት ፡ ነው ። ጦርነቱ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ የአውሮፓ ፡ መንግሥታት ፡ ቡድኖች ፡ መካከል ፡ የቅራኔ ፡ መካረር ፡ ውጤት ፡ ሲሆን ፤ የትግሉ ፡ ቅርፅ ፡ ግን ፡ በፕሮቴስታንቶችና ፡ በካቶሊኮች ፡ መካከል ፡ የተደረገ ፡ ጦርነት ፡ ነው ። ጀርመን ፡ የዚህ ፡ ትግል ፡ ዋና ፡ የትግል ፡ መስክ ፤ የጦርነቱ ፡ የዘረፋና ፡ የወረራ ፡ ዓላማ ፡ ሆና ፡ ነበር ። ጦርነቱን ፡ ያቆመው ፡ በ ፲፮፻፵፰ ዓ. ም. በዌስትፋሊያ ፡ የተፈራረሙት ፡ የሠላም ፡ ድርድር ፡ ሲሆን ፡ ጀርመን ፡ በፖለቲካ ፡ መሰነጣጠቋን ፡ አረጋግጧል ።

ገጽ ፤ ፴፫

10 <u>የጎታው ፡ ፕሮግራም</u> — የጀርመን ፡ ሶሺያሊስት ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ፓርቲ ፡ ፕሮግራም ፡ ነው ። የፀደቀው ፡ በ ፲፰፻፸፭ ዓ. ም. እስከዛ ፡ ጊዜ ፡ ድረስ ፡ ለየብቻ ፡ የነበሩት ፡ ሁለት ፡ የጀርመን ፡ ሶሺያሊስት ፡ ፓርቲዎች ፡ በተባበሩበት ፡ በጎታ ፡ ጉባዔ ፡ ላይ ፡ ነበር ። ፓርቲዎቹ — ኤይዘናኮች (በአውጉስት ፡ ቤቤልና ፡ ዊልኼልም ፡ ሊብክነኽት ፡ የሚመራውና ፡ በአይዲኦሎጂ ፡ በማርክስና ፡ በኤንግልስ ፡ ተፅእኖ ፡ ስር ፡ የነበረው) እና ፡ ላሳልያኖች ፡ ነበሩ ።



ኤይዘናኮች ፡ በአበይት ፡ ጥያቄዎች ፡ ላይ ፡ ለላሳልያኖች ፡ ስለተበገሩና ፡ የላሳልያኖች ፡ ምንባቦችን ፡ ስለተቀበሉ ፡ ፕሮግራሙ ፡ የኤክሌክቲሲዝም ፡ ደካማነት ፡ ነበረው ። ማርክስ « የጎታ ፡ ፕሮግራም ፡ ሂስ » በተባለው ፡ ሥራውና ፡ ኤንግልስ ፡ ለቤቤል ፡ በመጋቢት ፡ ፲፰-፳፰ ፤ ፲፰፻፸፭ ዓ. ም. በላከው ፡ ደብዳቤ ፡ የጎታ ፡ ፕሮግራም ፡ ረቂቅ ፡ ከ ፲፰፻፷፱ ዓ. ም. የኤይዘናኮች ፡ ፕሮግራም ፡ ጋር ፡ ሲነፃፀር ፡ ትልቅ ፡ እርምጃ ፡ ወደኋላ ፡ መሆኑን ፡ በመገንዘብ ፡ ከፍተኛ ፡ ወቀሳ ፡ አቅርበውበታል ።

ገጽ ፤ ፴፭

11 በ ፲፱ኛው ፡ ምእት ፡ ዓመት ፡ መጨረሻና ፡ በ ፳ ኛው ፡ ምእት ፡ ዓመት ፡ መጀመሪያ ፡ በብዙ ፡ አገሮች ፡ ገዢ ፡ የቡርዥዋ ፡ አካባቢዎች ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ ንቅናቄ ፡ ለመከፋፈልና ፤ በጠቃቅን ፡ ሬፎርሞች ፡ ወዝ ፡ አደሩን ፡ ከአብዮታዊ ፡ ትግል ፡ ለመቀልበስ ፡ ሞክረዋል ። ይህን ፡ ዓላማ ፡ እግቡ ፡ ለማድረስ ፡ ብዙ ፡ ተንኮል ፡ ሰርተዋል ፤ አንዳንድ ፡ የሶሺያሊስት ፡ ፓርቲዎች ፡ ሬፎርሚስት ፡ ... ዎችን ፡ በአድሃሪ ፡ የቡርዥዋ ፡ መንግሥታት ፡ እን... ፈሉ ፡ አድርገዋል ። በእንግሊዝ ፡ በ ፲፰፻፺፪ ዓ. ም. « የወዝ ፡ አደሩን ፡ መደብ ፡ ፍጹም ፡ ከከዱትና ፡ ለሚኒ... ትርነት ፡ ሹመት ፡ ራሳቸውን ፡ ከሸጡት » (ጥቅስ ፡ የሌ... ኒን) አንዱ ፤ ጆን ፡ በርንስ ፡ ወደ ፡ ፓርላማ ፡ ተመርጧል ፡ በፈረንሳይ ፡ በ ፲፰፻፺፱ ዓ. ም. ሶሺያሊስቱ ፡ አሌክሳ... ንደር ፡ ኤትዬን ፡ ሚልየራን ፡ የቫልዴክ-ሩሶ ፡ የቡር... ዥዋ ፡ መንግሥት ፡ አባል ፡ በመሆን ፡ ቡርዥዋው ፡ ፖለቲካውን ፡ እንዲያካሂድ ፡ ረድቷል ። የሚልየራን ... ወደ ፡ አድኃሪ ፡ የቡርዥዋ ፡ መንግሥት ፡ መቀላቀል ፡ በፈረንሳይ ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ ንቅናቄ ፡ ላይ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ የማይባል ፡ ከፍተኛ ፡ ጉዳት ፡ አድርሷል ። ሌኒን ፡ ሚ... እንደከዳተኝነትና ፡ እ... የራናዊነትን ፡ የተመለከተው ...

ደበራኸርነት (ሪቪዢኒዝም) ነው ። በኢጣልያ ፡ በ ፳ ኛው ፡ ምእት ፡ ዓመት ፡ መጀመሪያ ፡ ላይ ፡ ከመንግሥቱ ፡ ጋር ፡ የመቀላቀልን ፡ ቀጥተኛ ፡ ደጋፊዎች ፡ ሶሺያሊስቶቹ ፡ ሌኦኒዳ ፡ ቢሶላቲ ፤ ኢቫኖኤ ፡ ቦኖሚና ፡ ሌሎቹ ፡ ነበሩ ። እነሱም ፡ በ ፲፱፻፲፪ ዓ. ም. ከሶሺያሊስት ፡ ፓርቲው ፡ ተወግደዋል ።

በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ ወቅት ፡ የብዙ ፡ አገሮች ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ ፓርቲዎች ፡ የቀኝ ፡ አክራሪ ፡ አድርባይ ፡ መሪዎች ፡ በግልፅ ፡ የሶሺያል-ሾቪኒዝም ፡ አቋም ፡ ወስደዋል ። በየአገራቸው ፡ ከመንግሥታቸው ፡ ጋር ፡ በመቀላቀል ፡ የፖለቲካ ፡ አቀነባባሪዎች ፡ ሆነዋል ።

ገጽ ፤ ፴፱

12 በየካቲቱ ፡ ፳፯ (መጋቢት ፡ ፲፪) ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. ሁለተኛ ፡ የቡርዥዋ-ዴሞክራቲክ ፡ አብዮት ፡ ምክንያት ፡ የዘውድ ፡ አገዛዙ ፡ ተገርስሷል ። በቦታው ፡ የቡርዥዋ ፡ ጊዜያዊ ፡ መንግሥት ፡ ተቋቋመ ።

ገጽ ፤ ፴፯

13 ካዴቶች — የሕጋዊ ፡ ዴሞክራቲክ ፡ ፓርቲ ፡ አባሎች ፡ ናቸው ። የታወቀ ፡ የሩሲያ ፡ የሊበራላዊ ፡ ሞናርኪያዊ ፡ ቡርዥዋ ፡ ፓርቲ ። የካዴቶች ፡ ፓርቲ ፡ የተመሠረተው ፡ በ ፲፱፻፭ ዓ. ም. በጥቅምት ፡ ወር ፡ ነው ። የፓርቲው ፡ አባሎች ፡ የቡርዥዋ ፡ ተወካዮች ፤ የመሬት ፡ ከበርቴዎችና ፡ የቡርዥዋ ፡ ምሁራን ፡ ነበሩ ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ ካዴቶች ፡ በሰፊው ፡ የዘውድ ፡ አገዛዙ ፡ የወረራ ፡ የውጭ ፡ ፖለቲካን ፡ ደግፈዋል ። በየካቲቱ ፡ የቡርዥዋ-ዴሞክራቲክ ፡ አብዮት ፡ ወቅት ፡ የዘውድ ፡ አገዛዝን ፡ ለማዳን ፡ ያልተሳካ ፡ ጥረት ፡ አድርገዋል ። ካዴቶች ፡ በቡርዥዋው ፡ ጊዜያዊ ፡ መንግሥት ፡



የመሪነትን ፡ ቦታዎች ፡ በመጨበጥ ፡ ለአሜሪካ-እንግሊዝ-ፈረንሳይ ፡ ኢምፔሪያሊስቶች ፡ ጠቃሚ ፡ የሆነ ፡ ፀረ-ሕዝብና ፡ ፀረ-አብዮት ፡ ፖለቲካ ፡ አካሂደዋል ። ከጥቅምቱ ፡ ሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ ድል ፡ በኋላ ፡ ካዴቶች ፡ የሶቪዬት ፡ መንግሥት ፡ ዋና ፡ ጠላት ፡ በመሆን ፡ ታግለዋል ። በሁሉም ፡ ፀረ-አብዮታዊ ፡ የሰርጎ ፡ ገቦች ፡ አድማዎችና ፡ ወረራዎች ፡ ተካፍለዋል ።

ገጽ ፤ ፵፯ ፤ ፷፪

14 «Die Neue Zeit» (« አዲስ ፡ ዘመን ») — የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ ፓርቲ ፡ የቴዎሪ ፡ መጽሔት ። ከ ፲፰፻፹፫ ዓ. ም. እስከ ፡ ፲፱፻፳፫ ዓ. ም. በስቱትጋርት ፡ ይታተም ፡ ነበር ። እስከ ፡ ጥቅምት ፡ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. ድረስ ፡ አዘጋጁ ፡ ካውትስኪይ ፡ ነበር ፤ በኋላም ፡ ኩኖቭ ፡ ሆነ ። በ «Die Neue Zeit» ነበር ፡ በመጀመሪያ ፡ ጊዜ ፡ ብዙ ፡ የማርክስና ፡ የኤንግልስ ፡ ሥራዎች ፡ የታተሙት ። ኤንግልስ ፡ ለመጽሔቱ ፡ አዘጋጆች ፡ ምክር ፡ በመስጠት ፡ እርዳታውን ፡ አበርክቷል ። ከማርክሲዝም ፡ ወለም ፡ ዘለም ፡ በማለቱ ፡ ኤንግልስ ፡ መጽሔቱን ፡ የወቀሰው ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ነበር ። ከ ፺ ኛዎቹ ፡ ዓመታት ፡ ሁለተኛ ፡ አጋማሽ ፡ ጀምሮ ፤ ኤንግልስ ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፤ በተቀነባበረ ፡ አኳኋን ፡ በመጽሔቱ ፡ ሬቪዢኒስት (በራዥ) ጽሑፎች ፡ መታተም ፡ ጀምረዋል ። ከነዚህ ፡ መካከል ፤ በማርክሲዝም ፡ ላይ ፡ የበራዥነት ፡ ወረራውን ፡ የከፈቱት ፤ « የሶሺያሊዝም ፡ ችግሮች » የሚሉ ፡ የቤርንስተይን ፡ ጽሑፎች ፡ ታትመዋል ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ ወቅት (፲፱፻፲፬-፲፱፻፲፰ ዓ. ም.) መጽሔቱ ፡ በመሠረቱ ፡ የደገፈው ፡ ሶሺያል-ሾቪኒዝምን ፡ ነው ።

ገጽ ፤ ፶፩

15 ይህ ፡ የሚያመለክተው « የዓለም ፡ አቀፍ ፡ ወዝ ፡ አደሮ

13—230





ች ፡ አንድነት ፡ ስለ ፡ ፍራንኮ-ፕሩሺያ ፡ ጦርነት ፤ በአ ውሮፓና ፡ በተባበረው ፡ አሜሪካ ፡ ላሉ ፡ የዓለም ፡ አቀፍ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ አንድነት ፡ አባሎች ፡ ያደረገው ፡ ሁለተኛ ፡ ጥሪን » ነው ። ማርክስ ፡ ይህን ፡ ጽሑፍ ፡ የጻፈው ፡ በለንደን ፤ በመስከረም ፡ ፯-፱ ፤ ፲፰፻፸ ዓ. ም. ነው ።

ገጽ ፤ ፶፫

16 ማርክስ ፡ ለኩገልማን ፡ በሚያዝያ ፡ ፲፪ ፤ ፲፰፻፸፩ ዓ. ም. የጻፈውን ፡ ደብዳቤ ፡ ተመልከት ።

ገጽ ፤ ፶፯

17 ማርክስ ፡ የጻፈውን « የእርስ ፡ በርስ ፡ ጦርነት ፡ በፈረንሳይ » ተመልከት ። ቀጥሎ ፡ በገጾች ፤ ፷፯ ፤ ፷፱ ፤ ፸፯ ፤ ፹፫ ፤ ፹፬ ላይ ፡ ሌኒን ፡ የሚጠቅሰው ፡ ጥቅስ ፡ ከዚሁ ፡ የማርክስ ፡ ሥራ ፡ ውስጥ ፡ ነው ።

ገጽ ፤ ፷፰

18 « ዴሎ ፡ ናሮዳ » (« የሕዝብ ፡ ጉዳይ ») — እለታዊ ፡ ጋዜጣ ፤ የሶሺያሊስት-አብዮታውያን ፡ ፓርቲ ፡ ልሳን ። ብዙውን ፡ ጊዜ ፡ ስም ፡ በመለዋወጥ ፡ ከመጋቢት ፡ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሐምሌ ፡ ፲፱፻፲፰ ዓ. ም. ድረስ ፡ በፔትሮግራድ ፡ ይታተም ፡ ነበር ። ጋዜጣው ፡ የመከላከልና ፡ የመስማማትን ፡ አቋም ፡ በመያዝ ፡ ቡ ርዡዋው ፡ ጊዜያዊ ፡ መንግሥትን ፡ ደግፏል ። ጋዜጣው ፡ እንደገና ፡ መታተም ፡ የጀመረው ፡ በሳማራ ፡ ከተማ ፡ በጥቅምት ፡ ፲፱፻፲፰ ዓ. ም. (፲ ቁጥሮች ፡ ታትመዋል) እና ፡ በሞስኮ ፡ በመጋቢት ፲፱፻፲፱ ዓ. ም. (፲ ቁጥሮች ፡ ታትመዋል) ። ጋዜጣው ፡ በፀረ-አብዮታዊ ፡ ተግባሩ ፡ ተዘጋ ።

ገጽ ፤ ፸፬



19 ዢሮንዲስቶች — በ ፲፰ኛው ፡ ምእት ፡ ዓመት ፡ መ ጨረሻ ፡ የፈረንሳይ ፡ ቡርዡዋ ፡ አብዮት ፡ ወቅት ፡ የነበ ረ ፡ ቡርዡዋ ፡ የፖለቲካ ፡ ቡድን ። ዢሮንዲስቶች ፡ የመለስተኛ ፡ ቡርዡዋ ፡ ጥቅም ፡ ጠባቂዎች ፡ ሲሆኑ ፤ በአብዮትና ፡ በፀረ-አብዮት ፡ መካከል ፡ ሲዋዥቁ ፡ ነበር ። ከዘውድ ፡ አገዛዝ ፡ ጋር ፡ ስምምነት ፡ አድር ገዋል ።

ገጽ ፤ ፹፫

20 ኤንግልስ ፡ የጻፈውን « የመኖሪያ ፡ ቤት ፡ ጥያቄ » ተመልከት ። ቀጥሎ ፡ በ ፹፰ ፡ እና ፡ ፺ ፡ ገጾች ፡ ሌኒን ፡ የሚጠቅሰው ፡ ይህንኑ ፡ የኤንግልስ ፡ ሥራን ፡ ነው ።

ገጽ ፤ ፹፯

21 ብላንኪስቶች — በፈረንሳይ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ንቅናቄ ፡ ውስጥ ፡ የነበረ ፤ በጣም ፡ በታወቀው ፡ አብዮታዊና ፡ ዝነኛ ፡ የፈረንሳይ ፡ ተምኔታዊ ፡ ኮሙኒዝም ፡ ደጋፊዎ ች ፡ አንዱ ፡ በሆነው ፡ በሉዊ ፡ አውጉስት ፡ ብላንኪ (፲፰፻፭-፲፰፻፹፩ ዓ. ም.) ይመራ ፡ የነበረው ፡ ማኅ መር ፡ ደጋፊዎች ፡ ናቸው ። በብላንኪስቶች ፡ እምነት « የሰው ፡ ዘር ፡ ከቅጥር ፡ ባርነት ፡ ነፃ » የሚወጣው በወዝ ፡ አደሩ ፡ የመደብ ፡ ትግል ፡ ሳይሆን ፤ በጥቂት ፡ ምሁራን ፡ አድማ ፡ ነው » የአብዮታዊ ፡ ፓርቲ ፡ ተግ ባ ርን ፡ በጥቂቶች ፡ ምሥጢራዊ ፡ አድማ ፡ በመተካት ፤ አድማው ፡ ድል ፡ እንዲመታ ፡ የሚያስፈልጉትን ፡ የተ ጨበጡ ፡ ሁኔታዎችን ፡ አልተገነዘቡም ። ከሰፊ ፡ ሕዝብ ፡ ግንኙነት ፡ አልነበራቸውም ።

ገጽ ፤ ፹፱

22 ፕሩዶናውያን — ፀረ-ሳይንሳዊ ፡ የሆነ ፡ የንዑስ ፡ ቡር ዡዋ ፡ ሶሺያሊዝም ፡ ደጋፊዎች ፡ ናቸው ። ፕሩዶናው

ያን ፡ ማርክሲዝምን ፡ በጠላትነት ፡ ይመለከታሉ ። ስማቸው ፡ የወሰዱት ፡ ከአይዲኦሎጂ ፡ መሪያቸው ፡ ከፈረንሳዩ ፡ ሥርዓተ-አልበኛ ፡ ከገፃዘፍ ፡ ፕሩዶን ፡ ነው ። ፕሩዶን ፡ ታላቅ ፡ የካፒታሊስት ፡ ንብረት ፡ በንዑስ ፡ ከቡርዥዋ ፡ አቋም ፡ ቢቃወምም ፡ ጠቃቅን ፡ የንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ንብረትን ፡ ዘለአለማዊ ፡ ለማድረግ ፡ ምኞት ፡ ነበረው ። « ሕዝባዊ » እና « የልውውጥ » ባንኮች ፡ እንዲመሠረቱ ፡ ሀሳብ ፡ አቅርቧል ። በሱ ፡ አስተያየት ፡ በዚህም ፤ ወዝ ፡ አደሮች ፡ የራሳቸው ፡ የምርት ፡ መገልገያዎችን ፡ ለመያዝ ፤ ባለ ፡ ዕደ ፡ ጥበቦች ፡ ለመሆንና ፡ የራሳቸውን ፡ ምርት « በትክክል » ለመሸጥ ፡ ይችላሉ ። ፕሩዶን ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ ታሪካዊ ፡ ቦታና ፡ አብዮትን ፡ እንዲሁም ፡ ደግሞ ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ አይቀበልም ፤ ይቃወማል ። በሥርዓተ-አልበኝነት ፡ አቋም ፡ የመንግሥት ፡ አስፈላጊነትን ፡ አይቀበልም ። ማርክስና ፡ ኤንግልስ ፡ ፕሩዶኒስቶች ፡ በርዕዮቶቻቸው ፡ አንደኛው ፡ ኢንተርናሽናልን ፡ እንዳያወናብዱ ፡ የተቀነባበረ ፡ ትግል ፡ አድርገዋል ።

ገጽ ፤ ፺፩ ፤ ፻፷፫

23 ይህ ፡ የሚያመለክተው ፡ በታህሳስ ፡ ፲፰፻፸፫ ዓ. ም. በኢጣልያው «Almanacco Republicano per l'anno 1874» በተባለው ፡ መጽሐፍና ፡ ከዚያም ፡ በጀርመንኛ ፡ ተተርጉመው ፡ በ«Die Neue Zeit» መጽሔት ፡ የታተሙትን ፡ የማርክስ « ፖለቲካዊ ፡ ኢንዲፈረንቲዝም » እና ፡ የኤንግልስ « ስለአውቶሪቲ » የተባሉትን ፡ ጽሑፎች ፡ ነው ።

ገጽ ፤ ፺፩

24 ማርክስ ፤ « ፖለቲካዊ ፡ ኢንዲፈረንቲዝም » ።

ገጽ ፤ ፺፩



25 ኤንግልስ ፤ « ስለአውቶሪቲ » ።

ገጽ ፤ ፺፫

26 ኤንግልስ ፤ « ስለአውቶሪቲ »

ገጽ ፤ ፺፭

27 ማርክስ ፤ « የጎታ ፡ ፕሮግራም ፡ ሂስ » ተመልከት ።

ገጽ ፤ ፺፯

28 ይህ ፡ የሚያመለክተው « የፍልስፍና ፡ ድህነት » የተባለው ፡ የማርክስን ፡ ሥራ ፡ ነው ።

ገጽ ፤ ፺፰

29 <u>የኤርፉርቱ ፡ ፕሮግራም</u> — በጥቅምት ፡ ወር ፡ ፲፰፻፺፩ ዓ. ም. በኤርፉርቱ ፡ ጉባዔ ፡ የፀደቀ ፡ የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ ፓርቲ ፡ ፕሮግራም ፡ ነው ። የኤርፉርቱ ፡ ፕሮግራም ፡ ከጎታው ፡ ፕሮግራም ፡ (፲፰፻፸፭ ዓ. ም.) ጋር ፡ ሲነፃፀር ፡ አንድ ፡ እርምጃ ፡ ወደፊት ፡ ነበር ። በፕሮግራሙ ፡ እንደ ፡ መሠረት ፡ የተጠቀመው ፡ የማርክሲዝም ፡ ትምህርት ፡ ካፒታሊስታዊ ፡ ስልተ ፡ ምርት ፡ የማይቀርለት ፡ ፈራሽ ፡ ነው ፤ በሱ ፡ ቦታም ፡ ሶሺያሊስታዊ ፡ ስልተ ፡ ምርት ፡ ይተካል ፡ የሚለውን ፡ ነው ። በፕሮግራሙ ፡ ውስጥ ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ መደብ ፡ የፖለቲካ ፡ ትግል ፡ ማካሄድ ፡ እንደሚያስፈልገው ፡ በአፅንኦት ፡ ተጠቅሷል ። በዚህ ፡ ትግል ፡ ውስጥ ፡ የፓርቲን ፡ የመሪነት ፡ ሚና ፡ አመልክቷል ፤ ወዘተ ። ይሁን ፡ እንጂ ፤ በኤርፉርቱ ፡ ፕሮግራም ፡ ውስጥ ፡ ለአድርባይነት ፡ የሚመቹ ፡ በጣም ፡ አብይ ፡ የሆኑ ፡ ቀዳዳዎችን ፡ ትቷል ። በዚህ ፡ የፕሮግራም ፡ ረቂቅ ፡ ላይ ፤ « በ ፲፰፻፺፩ ዓ. ም. የሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ ፕሮግራም ፡ ረቂቅ ፡ ላይ ፡ ሂስ » በሚል ፡ አርእስት ፡ ለመጀመሪያ ፡ ጊዜ ፡ ሰፊ ፡ የሆነ ፡ ሂስ ፡ ያቀረበው ፡ ኤንግልስ ፡ ነው ። ይህ ፡ ሂስ ፡ በመሠ





ረቱ ፡ የቀረበው ፡ በጠቅላላው ፡ በሁለተኛ ፡ ኢንተርናሽናል ፡ አድርባይነት ፡ ላይ ፡ ነበር ። ቢሆንም ፡ የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ ፓርቲ ፡ መሪዎች ፡ ይህን ፡ የኤንግልስ ፡ ሂስ ፡ ከሰፊ ፡ የፓርቲ ፡ አባላት ፡ ደብቀውታል ። እንደዚሁም ፡ የፕሮግራሙ ፡ የመጨረሻ ፡ ይዘት ፡ ሲቀነባበር ፡ በጣም ፡ ጠቃሚ ፡ የሆኑትን ፡ አስተያየቶች ፡ አልተገነዘቡም ። ሌኒን ፡ እንዳለው ፡ የኤርፉርት ፡ ፕሮግራም ፡ ዋና ፡ ጉድለትና ፡ ለአድርባይነት ፡ በፍራቻ ፡ መበገር ፡ ምልክቱ ፤ በፕሮግራሙ ፡ ውስጥ ፡ ስለ ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ የበላይ ፡ ገዥነት ፡ አለመጥቀሱ ፡ ነው ።

ገጽ ፤ ፻፪

30 ፍጹም ፡ ልዩ ፡ የሆነ ፡ ፀረ-ሶሺያሊስት ፡ ሕግ ፡ በጀርመን ፡ የታወጀው ፡ በ ፲፰፻፸፰ ዓ. ም. በቢስማርክ ፡ መንግሥት ፡ ሲሆን ፤ ዓላማው ፡ የወዝ ፡ አደሩንና ፡ የሶሺያሊስትን ፡ ንቅናቄ ፡ ለመታገል ፡ ነው ። በዚህ ፡ ሕግ ፡ መሠረት ፡ ሁሉም ፡ የሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ ፓርቲ ፡ ድርጅቶች ፤ ሰፊ ፡ ሕዝባዊ ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ ድርጅቶች ፤ የወዝ ፡ አደሩ ፡ ጋዜጦች ፡ ታግደዋል ። ሶሺያሊስታዊ ፡ ሥነ ፡ ጽሑፎች ፡ ተወርሰዋል ። ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ በመሳደድ ፡ ተሰቃይተዋል ፤ ስደትም ፡ ሄደዋል ። በ ፲፰፻፺ ዓ. ም. በሰፊውና ፡ በመጠናከር ፡ ላይ ፡ በነበረው ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ ንቅናቄ ፡ ኃይለኛ ፡ ግፊት ፡ ምክንያት ፡ ፍጹም ፡ ልዩ ፡ የሆነው ፡ ፀረ-ሶሺያሊስት ፡ ሕግ ፡ ተነስቶአል ።

ገጽ ፤ ፻፳

31 « ፕራቭዳ » (« እውነት ») — እለታዊ ፡ ሕጋዊ ፡ የቦልሼቪኮች ፡ ጋዜጣ ፡ ነው ። የጋዜጣው ፡ የመጀመሪያ ፡ ቁጥር ፡ የወጣው ፡ በፔተርቡርግ ፡ (ባሁኑ ፡ ጊዜ ፡ ሌኒን ግራድ) በሚያዝያ ፳፪ (ግንቦት ፭) ፤ ፲፱፻፲፪ ዓ. ም. ነው ።



ሌኒን « የፕራቭዳ » የአይዲኦሎጂ ፡ መሪዋ ፡ ነበር ። በየእለቱ ፡ ለጋዜጣው ፡ ጽሑፎች ፡ አቅርቦአል ። ጋዜጣው ፡ ታጋይና ፡ አብዮታዊ ፡ በሆነ ፡ መንፈስ ፡ እንዲሠራ ፡ ሌኒን ፡ ለአዘጋጆቹ ፡ ሁልጊዜ ፡ መምሪያ ፡ ምክር ፡ ሰጥቷል ።

« በፕራቭዳ » አማካይነት ፡ አብዛኛው ፡ የፓርቲ ፡ ድርጅታዊ ፡ ሥራ ፡ ይከናወነው ፡ ነበር ። በጋዜጣው ፡ ጽሕፈት ፡ ቤት ፡ ከቀበሌ ፡ የፓርቲ ፡ ክበቦች ፡ ጋር ፡ ግንኙነቶች ፡ ይደረጉ ፡ ነበር ። የፋብሪካዎች ፡ የፓርቲ ፡ ሥራ ፡ መልእክቶች ፡ የሚመጡት ፡ ወደዚህ ፡ ጽሕፈት ፡ ቤት ፡ ነበር ። የፓርቲው ፡ የማእከላዊ ፡ ኮሚቴና ፡ የፔተርቡርግ ፡ ኮሚቴ ፡ የፓርቲ ፡ መመሪያዎች ፡ የሚተላለፉት ፡ ከዚሁ ፡ ጽሕፈት ፡ ቤት ፡ ነበር ።

« ፕራቭዳን » ሁልጊዜ ፡ ያለ ፡ ማቋረጥ ፡ ፖሊሶች ፡ ያሳድዷት ፡ ነበር ። በሀምሌ ፰ (፳፩)፤ ፲፱፻፲፬ ዓ. ም. ጋዜጣው ፡ ታገደ ።

« የፕራቭዳ » እትም ፡ እንደገና ፡ የጀመረው ፡ ከ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የየካቲቱ ፡ የቡርዥዋ-ዴሞክራቲክ ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ ነው ። ከመጋቢት ፡ ፭ (፲፰) ፤ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. ጀምሮ « ፕራቭዳ » የሩሲያ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ ፓርቲ ፡ የማእከላዊና ፡ የፔተርቡርግ ፡ ኮሚቴዎች ፡ ልሳን ፡ ሆነ ።

ሌኒን ፡ ወደፔትሮግራድ ፡ እንደመጣ ፡ የአዘጋጆቹ ፡ አባል ፡ ሆነ ። « ፕራቭዳ » የቡርዥዋ-ዴሞክራቲክ ፡ አብዮትን ፡ ወደ ፡ ሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ ማሸጋገር ፡ የሚለውን ፡ የሌኒን ፡ ፕላን ፡ በሰፊው ፡ ዘረጋች ።

በሀምሌ-ጥቅምት ፡ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. በፀረ-አብዮታዊው ፡ ጊዜያዊ ፡ መንግሥት ፡ መሳደድ ፡ ምክንያት ፤ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ስሟን ፡ በመለዋወጥ « ሊስቶክ ፡ ፕራቭዲ » (« የፕራቭዳ ፡ ገጽ ») ፤ « ፕሮሌታሪይ » (« ወዝ ፡ አደር ») ፤ « ራቦቺይ » (« ሠራተኛ ») ፤ « ራቦቺይ ፡

ፑት » (« የሠራተኛ ፡ ጉዳና ») በሚሉ ፡ ስሞች ፡ ታትማለች ። ከጥቅምቱ ፡ ሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ ድል ፡ መምታት ፡ በኋላ ፤ ከጥቅምት ፡ ፳፭ (ህዳር ፡ ፯) ፤ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. ወዲህ ፡ ጋዜጣዋ ፡ በድሮ ፡ ስምዋ « ፕራቭዳ » ትታተም ፡ ጀመር ።

ገጽ ፤ ፪፲፱

32 የኤንግልስ « ለማርክሱ « የእርስ ፡ በርስ ፡ ጦርነት ፡ በፈረንሳይ » መግቢያ » ተመልከት ።

ቀጥሎ ፡ በ፪፲፫-፪፳፮ ገጾች ፡ ሌኒን ፡ የሚጠቅሰው ፡ ይህንኑ ፡ የኤንግልስ ፡ ጽሑፍ ፡ ነው ።

ገጽ ፤ ፪፲፫

33 ይህ ፡ የሚያመለክተው ፡ የጊዜያዊው ፡ መንግሥት ፡ ሚኒስትር ፡ ሜንሼቪኩ ፡ ጸረተሊ ፡ በሰኔ ፲፩ (፳፬) ፤ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. በአንደኛው ፡ የመላ ፡ ሩሲያ ፡ ሶቪዬቶች ፡ ጉባዔ ፤ የፔትሮግራዱ ፡ የወዝ ፡ አደርና ፡ የተወካይ ፡ ወታደሮች ፡ ሶቪዬት ፡ ሥራ ፡ አስኪያጅ ፡ ኮሚቴ ፤ የአርሶ ፡ አደሮች ፡ ተወካዮች ፡ ሶቪዬት ፡ ሥራ ፡ አስኪያጅ ፡ ኮሚቴና ፡ የሁሉም ፡ በጉባዔው ፡ የነበሩ ፡ ቢሮዎች ፡ የፕሬዚድዩም ፡ ጠቅላላ ፡ ስብሰባ ፡ ላይ ፡ ያደረገውን ፡ ንግግር ፡ ነው ። ንግግሩ ፡ የተደረገው ፡ ቦልሼቪኮች ፡ ለሰኔ ፲ (፳፫) አቅደውት ፡ በነበረው ፡ የፔትሮግራድ ፡ ወዝ ፡ አደሮችና ፡ ወታደሮች ፡ ሰላማዊ ፡ ሰልፍ ፡ ጥያቄ ፡ ላይ ፡ ሲወያዩ ፡ ነው ። የጸረተሊ ፡ ንግግር ፡ የሀሰት ፡ ዘለፋና ፡ አድኅሪ ፡ ነበር ። ቦልሼቪኮችን ፡ በአገዛዙ ፡ ላይ ፡ አድመዋል ፤ ፀረ-አብዮትን ፡ ረድተዋል ፡ በሚል ፡ በማውገዝ ፤ ጸረተሊ ፡ በቦልሼቪኮች ፡ ደጋፊዎች ፡ ላይ ፡ ጥብቅ ፡ እርምጃ ፡ እወስዳለሁ ፡ ሲል ፡ አስፈራርቶአል ።

ገጽ ፤ ፪፲፭



34 Los-von-Kirche-Bewegung (ከቤተ ፡ ክርስትያን ፡ የመለየት ፡ ንቅናቄ) ወይም Kirchenaustrittsbewegung (ከቤተ ፡ ክርስትያን ፡ የመውጣት ፡ ንቅናቄ) ከአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ በፊት ፡ በጀርመን ፡ በጣም ፡ ተስፋፍቶ ፡ ነበር ። በጥር ፡ ፲፱፻፲፬ ዓ. ም. በ «Die Neue Zeit» መጽሔት ፡ ላይ ፡ ሬቪዢኒስቱ ፡ ፓወል ፡ ጌዮረ ፡ ባቀረበው «Kirchenaustrittsbewegung und Sozialdemokratie» (« ከቤተ ፡ ክርስትያን ፡ የመውጣት ፡ ንቅናቄና ፡ ሶሺያል-ዴሞክራሲ ») የተነሳ ፡ የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ ፓርቲ ፡ በዚህ ፡ ንቅናቄ ፡ላይ ፡ ያለውን ፡ የአቋም ፡ ጥያቄ ፡ መወያየት ፡ ጀመረ ። ክርክሩ ፡ ሲካሄድ ፡ ጌዮረ ፡ ከቤተ ፡ ክርስትያን ፡ የመውጣት ፡ ንቅናቄውን ፡ በሚመለከት ፡ ፓርቲው ፡ ኒውትራል ፡ መሆን ፡ አለበት ፤ እንደዚሁም ፡ አባሎቹን ፡ በፓርቲው ፡ ስም ፡ ፀረ-ሃይማኖትና ፡ ፀረ-ቤተ ፡ ክርስትያን ፡ ፕሮፓጋንዳ ፡ እንዳያካሂዱ ፡ ማገድ ፡ አለበት ፡ ሲል ፡ የታወቁት ፡ የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ ምንም ፡ ተቃውሞ ፡ አላሳዩም ።

ገጽ ፤ ፪፲፮

35 በሌኒን ፡ የተጠቀሰው ፡ መሀከለኛ ፡ ደመወዝ ፡ በ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. ሁለተኛው ፡ አጋማሽ ፡ ላይ ፡ በነበረው፡ የወረቀት ፡ ገንዘብ ፡ ምንዛሪ ፡ ነው ።

በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ ጊዜ ፡ የሩሲያው ፡ የወረቀት ፡ ሩብል ፡ ምንዛሪ ፡ በጣም ፡ ወድቆ ፡ ነበር ።

ገጽ ፤ ፪፲፯

36 ላሳልያኖች — የጀርመናዊው ፡ የንዑስ ፡ ቡርዧዋ ፡ ሶሺያሊስት ፡ የፈርዲናንድ ፡ ላሳል ፡ ደጋፊዎችና ፡ ተከታዮች ፡ ናቸው ። ላሳልያኖች ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብን ፡





በተፅእኖአቸው ፡ ስር ፡ ለማድረግ ፡ ሲጣጣሩ ፡ የነበሩት ፡ ቡርዥዋ ፡ ፕሮግሬሲስቶችን ፡ ለመቋቋም ፡ በ ፲፰፻፷፫ ዓ. ም. በሌፕዚግ ፡ በወዝ ፡ አደር ፡ ማኅበራት ፡ ጉባዔ ፡ የተመሠረተው ፡ የመላ ፡ ጀርመን ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ ኅብረት ፡ አባላት ፡ ናቸው ። የማኅበሩ ፡ የመጀመሪያ ፡ ፕረዚዳንት ፤ የማኅበሩ ፡ ፕሮግራምና ፡ መሠረታዊ ፡ ታክቲክ ፡ ያቀነባበረው ፡ ላሳል ፡ ነበር ። የማኅበሩ ፡ የፖለቲካ ፡ ፕሮግራሙ ፡ ለአጠቃላይ ፡ የምርጫ ፡ መብት ፡ መታገል ፡ ሲሆን ፤ የኤኮኖሚ ፡ ፕሮግራሙ ፡ ከመንግሥት ፡ በመበደር ፡ የወዝ ፡ አደሮች ፡ አምራች ፡ ድርጅቶችን ፡ መመሥረት ፡ ነው ። ላሳልና ፡ ደጋፊዎቹ ፡ የፕሩሲያውን ፡ መሪነት ፡ በመደገፍ ፡ የቢስማርክ ፡ የትምክህተኝነት ፡ ፖሊሲውን ፡ ደግፈዋል ።

ገጽ ፤ ፻፳፫

37 የሚያመለክተው ፡ በ ፲፱፻፫ ዓ. ም. ከሀምሌ ፲፯ ፡ እስከ ፡ ነሀሴ ፲ (ከሀምሌ ፡ ፴ እስከ ፡ ነሀሴ ፡ ፳፫) ድረስ ፡ የተካሄደውን ፡ የሩሲያ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ፓርቲ ፡ ሁለተኛ ፡ ጉባዔን ፡ ነው ። የጉባዔው ፡ የመጀመሪያዎቹ ፡ ፲፫ ስብሰባዎች ፡ የተካሄዱት ፡ በብራሴልስ ፡ ከተማ ፡ ሲሆን ፤ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ፖሊስ ፡ ጉባዔውን ፡ ማሳደድ ፡ ስለያዘ ፡ የቀሩት ፡ የጉባዔው ፡ ስብሰባዎች ፡ የተካሄዱት ፡ በለንደን ፡ ነው ።

ገጽ ፤ ፻፳፬

38 የማርክሱን « የእርስ ፡ በርስ ፡ ጦርነት ፡ በፈረንሳይ » ተመልከት ።

ገጽ ፤ ፻፴፫

39 ሸይሎክ — « የቬነሲያው ፡ ነጋዴ » በተባለው ፡ የሼክስፒር ፡ ኮሚዲ ፡ የታሪኩ ፡ ተካፋይ ፡ ሰው ፡ ነው ። ጨካኝ ፡ አረመኔ ፡ የሆነ ፡ ገንዘብ ፡ አበዳሪ ፡ ነበር ።



በውሉ ፡ መሠረት ፤ ብድሩን ፡ መመለስ ፡ ያልቻለ ፡ ተበዳሪ ፤ ያለአንዳች ፡ ርህራሄ ፡ አንድ ፡ ፉንት (ግማሽ ፡ ኪሎ ፡ ያህል) ስጋ ፡ ከአካሉ ፡ እንዲቆርጡለት ፡ ይጠይቃል ።

ገጽ ፤ ፻፵፪

40 ለቀልድ ፡ ያህል ፡ በከንቱ — በመንፈሳዊ ፡ ትምህርት ፡ ቤት ፡ ስለሚማሩት ፡ ተማሪዎች ፤ ስለኑሮአቸው ፡ ሩሲያዊው ፡ ደራሲ ፡ ፖምያሎቭስኪይ ፡ እንደጻፉት ።

ገጽ ፤ ፻፵፯

41 የአንደኛው ፡ ኢንተርናሽናል ፡ የሄግ ፡ ኮንግሬስ ፡ የተካሄደው ፡ በመስከረም ፡ ፪-፯ ፤ ፲፰፻፸፪ ዓ. ም. ነው ። በኮንግሬሱ ፡ የ ፲፭ ብሄራዊ ፡ ድርጅቶች ፡ ፷፭ ልዑካን ፡ ተካፍለውበታል ። ማርክስና ፡ ኤንግልስ ፡ ጉባኤውን ፡ ባዘጋጁበት ፡ ጊዜ ፡ ወዝ ፡ አደራዊ ፡ አብዮታዊ ፡ ኃይሎችን ፡ ለማስተባበር ፡ ከፍተኛ ፡ ሥራ ፡ አከናውነዋል ። በማርክስና ፡ በኤንግልስ ፡ አሳሳቢነት ፡ የአጀንዳው ፡ ይዘትና ፡ የጉባዔው ፡ ቀን ፡ ተወስኗል ። በጉባዔው ፡ አጀንዳ ፡ ሁለት ፡ መሠረታዊ ፡ ጥያቄዎች ፡ ነበሩ ፤ ፩. የጠቅላይ ፡ ኮሚቴው ፡ መብቶች ፤ ፪. የወዝ ፡ አደሩ ፡ ፖለቲካዊ ፡ ተግባር ።

ጉባዔው ፡ የጠቅላይ ፡ ኮሚቴው ፡ መብቶችን ፡ የሚያስፋፉ ፤ የጠቅላይ ፡ ኮሚቴው ፡ የሥራ ፡ ቦታን ፡ መለወጥ ፡ የሚመለከቱ ፤ በምሥጢራዊው « የሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ አንድነት » ተግባርና ፡ በመሳሰሉት ፡ ውሳኔዎች ፡ አሳልፏል ። የነዚህ ፡ ውሳኔዎች ፡ አብዛኛው ፡ ክፍል ፡ የተጻፈው ፡ በማርክስና ፡ በኤንግልስ ፡ ነው ። በሌሎችም ፡ ውሳኔዎች ፡ እንደ ፡ መሠረት ፡ አድርገው ፡ የተጠቀሙባቸው ፡ የነሱ ፡ አስተያየቶችን ፡ ነው ።





በሁለተኛው ፡ ጥያቄ ፡ ላይ ፡ የጉባዔው ፡ ውሳኔ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፤ « የፖለቲካ ፡ ሥልጣን ፡ መቀዳጀት ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ ከፍተኛ ፡ ግዳጅ ፡ ሆኖአል ። ስለሆነም « ሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ ግቡን ፡ እንዲመታና ፡ የዚህም ፡ የመጨረሻ ፡ ዓላማ ፡ የሆነው ፡ የመደቦች ፡ መጥፋት ፡ እንዲከናወን » የወዝ ፡ አደሩ ፡ የራሱ ፡ የሆነ ፡ የፖለቲካ ፡ ፓርቲ ፡ ማደራጀት ፡ አለበት ።

በዚህ ፡ ጉባዔ ፡ ላይ ፡ የማርክስ ፤ የኤንግልስና ፡ የነሱ ፡ ደጋፊዎች ፡ በሁሉም ፡ ዓይነቶች ፡ የንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ የጠባብ ፡ ቡድን ፡ ስሜቶች ፡ ላይ ፡ ያደረጉት ፡ የብዙ ፡ ዓመታት ፡ ትግል ፡ ድሉን ፡ ተጎናጽፏል ። የሥርዓተ-አልበኝነት ፡ መሪዎች ፡ ባኩኒን ፤ ጊልአምና ፡ ሌሎችም ፡ ከኢንተርናሽናል ፡ ተባረዋል ።

በማርክስና ፡ በኤንግልስ ፡ ቀጥተኛ ፡ መሪነትና ፡ በነሱ ፡ ከፍተኛ ፡ ተሳትፎ ፡ የተካሄደው ፡ የሄጉ ፡ ጉባዔ ፡ ውሳኔዎች ፡ የማርክሲዝም ፡ በንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ሥርዓተ-አልበኝነት ፡ ርዕዮተ ፡ ዓለም ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ድልን ፡ አበስረዋል ። ይህ ፡ ጉባዔ ፡ ነው ፤ ለወደፊቱ ፡ ራሳቸውን ፡ የቻሉ ፡ ብሔራዊ ፡ የወዝ ፡ አደር ፤ የፖለቲካ ፡ ፓርቲዎች ፡ እንዲቋቋሙ ፡ መሠረት ፡ የጣለው ።

ገጽ ፤ ፻፺፯

[42] የኤንግልስን « ለማርክሱ « የጎታ ፡ ፕሮግራም ፡ ሂስ » መግቢያ » ተመልከት ።

ገጽ ፤ ፻፺፯

[43] « ዛርያ » (« ጎህ ») ማርክሳዊ ፡ ሳይንሳዊ ፡ የፖለቲካ ፡ መጽሔት ። በሕግ ፡ ተፈቅዶለት ፡ የታተመው ፡ ከ ፲፱፻፩ እስከ ፡ ፲፱፻፪ ዓ. ም. በስቱትጋርት « በኢስክራ » (« ብልጭታ ») አዘጋጅነት ፡ ነበር ። ያወጣቸው ፡ ፬ ቁጥሮች ፡ ብቻ ፡ ነው ።



መጽሔቱ ፡ የማርክሲዝም ፡ ቴዎሪ ፡ መሠረት ፡ ሀሳቦችን ፡ ከግድፈት ፡ እየተከላከለ ፤ የዓለም ፡ አቀፍና ፡ የሩሲያ ፡ ሪቪዢኒስቶችን ፡ ተዋግቷል ።

ገጽ ፤ ፻፺፱

[44] ይህ ፡ የሚያመለክተው ፡ የሁለተኛው ፡ ኢንተርናሽናል ፡ አምስተኛ ፡ ዓለም ፡ አቀፍ ፡ ኮንግሬስን ፡ ነው ። የተካሄደው ፡ በመስከረም ፡ ፳፫-፳፯ ፤ ፲፱፻ ዓ. ም. በፓሪስ ፡ ከተማ ፡ ነው ። ሚልየራን ፡ በፀረ-አብዮታዊው ፡ የቫልዴክ-ሩሶ-መንግሥት ፡ ውስጥ ፡ በመግባቱ ፡ ምክንያት ፡ የተነሳ « የፖለቲካ ፡ ሥልጣን ፡ መቀዳጀትና ፡ ከቡርዥዋ ፡ ፓርቲዎች ፡ ጋር ፡ መተባበር » የሚለው ፡ መሠረታዊ ፡ ጥያቄን ፡ በሚመለከት ፡ ካውትስኪይ ፡ ያቀረበው፡ ውሳኔ ፡ ጉባዔው ፡ በድምፅ ፡ ብልጫ ፡ ተቀብሎታል ። « የአንድ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ግለ ፡ ሰብ ፡ በቡርዥዋ ፡ መንግሥት ፡ መሳተፍ ፡ እንደ ፡ የፖለቲካ ፡ ሥልጣን ፡ የመቀዳጀት ፡ ትክክለኛ ፡ መጀመሪያ ፡ ሆኖ ፡ ሊቆጠር ፡ አይችልም ። ይህ ፡ ጊዜያዊና ፡ ልዩ ፡ የሆነ ፡ የቀውጢ ፡ ቀን ፡ የትግል ፡ መሳሪያ ፡ እንጂ ፤ ሌላ ፡ ሊሆን ፡ አይችልም » ። አድርባዮች ፡ ከቡርዥዋው ፡ ጋር ፡ የሚያደርጉት ፡ ትብብርን ፡ ለመሸፋፈን ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ይህን ፡ ነጥብ ፡ ይጠቃቅሳሉ ።

ገጽ ፤ ፻፺፱

[45] ቤርንስተይንነት ፤ ቤርንስተይኖች — በዓለም ፡ አቀፍ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ አድርባይና ፡ ፀረ-ማርክሲዝም ፡ የሆነ ፡ መስመር ። መንስኤው ፡ በጀርመን ፡ በ፲፱ ኛው ፡ ምእት ፡ ዓመት ፡ መጨረሻ ፡ ላይ ። ስሙን ፡ ያገኘው ፤ በጣም ፡ ግልፅ ፡ የሪቪዢኒዝም ፡ አፈቀላጤ ፡ ከሆነው ፡ ከኤድዋርድ ፡ ቤርንስተይን ፡ ነው ።

ገጽ ፤ ፻፳፩





46 የማርክስን « ፲፰ ኛው ፡ የሉዊ ፡ ቦናፓርት ፡ ብሩሜር » ተመልከት ።

ገጽ ፤ ፻፰፩

47 የማርክስና ፡ የኤንግልስ ፤ ለጀርመኑ ፡ የ ፲፰፻፵፰ ዓ. ም. « የኮሙኒስት ፡ ፓርቲ ፡ ማኒፌስቶ » እትም ፡ መግቢያን ፤ ተመልከት ።

ገጽ ፤ ፻፰፫

48 የማርክስን ፤ « የእርስ ፡ በርስ ፡ ጦርነት ፡ በፈረንሳይ » ተመልከት ።

ገጽ ፤ ፻፰፯

49 የማርክስንና ፡ የኤንግልስን ፤ « የማእከላዊው ፡ ኮሚቴ ፡ ለኮሙኒስቶች ፡ ኅብረት ፡ ጥሪን » ፡ ተመልከት ።

ገጽ ፤ ፻፱፫

50 የማርክስን ፤ « የእርስ ፡ በርስ ፡ ጦርነት ፡ በፈረንሳይ » ተመልከት ።

ገጽ ፤ ፻፱፯

51 ይህ ፡ የሚያመለክተው ፡ የባልና ፡ ሚስቱ ፡ ዌቦች « የእን ግሊዝ ፡ የሠራተኞች ፡ ማኅበር ፡ ቴዎሪና ፡ ተግባር » የሚለው ፡ መጽሐፍን ፡ ነው ።

ገጽ ፤ ፻፱፯

52 « ወርሃዊ ፡ ሶሺያሊስታዊ » («Sozialistische Monatshefte») — መጽሔት ፤ የጀርመን ፡ አድርባዮች ፡ ዋና ፡ ልሳንና ፡ ከዓለም ፡ አቀፍ ፡ የሪቪዢኒስቶች ፡ ልሳኖች ፡ አንዱ ። ከ ፲፰፻፺፯ ዓ. ም. ጀምሮ ፡ እስከ ፲፱፻፴፫ ዓ. ም. ድረስ ፡ በበርሊን ፡ ይታተም ፡ ነበር ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት (፲፱፻፲፬-፲፱፻፲፰) ሶሺያል-ሾቪኒስት ፡ አቋም ፡ ነበረው ።

ገጽ ፤ ፻፲፩

53 ዠረሲስቶች — በፈረንሳይና ፡ በዓለም ፡ አቀፍ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ንቅናቄ ፡ የታወቀው ፡ መሪ ፡ የዠረስ ፡ ደጋፊዎች ። ዠረስ ፡ ለዴሞክራሲ ፤ ለሕዝቦች ፡ ነፃነት ፤ ለሰላም ፤ የኢምፔሪያሊስት ፡ ጭቆናንና ፡ የወረራ ፡ ጦርነቶችን ፡ በመቃወም ፡ ታግሏል ። ይሁን ፡ እንጂ ፡ ዠረስና ፡ ደጋፊዎቹ ፡ የማርክሲዝምን ፡ መሠረታዊ ፡ ነጥቦች ፡ ለመበረዝ ፡ ሞክረዋል ። በዠረሲስቶች ፡ አስተሳሰብ ፡ ሶሺያሊዝም ፡ ድል ፡ የሚመታው ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ ከቡርዥዋው ፡ ጋር ፡ በሚያደርገው ፡ የመደብ ፡ ትግል ፡ ሳይሆን ፤ «ከዴሞክራሲያዊ ፡ ሀሳብ ፡ ማበብ » ውጤት ፡ ነው ። በጨቋኞችና ፡ በተጨቋኞች ፡ መካከል ፡ የመደብ ፡ እርቅ ፡ እንዲሰፍን ፡ ሰብከዋል ። የጋራ ፡ መረዳጃ ፡ ንቅናቄ ፡ በካፒታሊዝም ፡ ሥር ፡ ማደግ ፡ ቀስ ፡ በቀስ ፡ ወደ ፡ ሶሺያሊዝም ፡ እንዲሸጋገር ፡ ያደርጋል ፤ የሚለውን ፡ የፕሩዶን ፡ ወዥንብር ፡ ይቀበላሉ ። በ ፲፱፻፪ ዓ. ም. ዠረሲስቶች ፡ ሪፎርሚስት ፡ አቋም ፡ ያለው ፡ የፈረንሳይ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ፓርቲን ፡ መስርተዋል ። በ ፲፱፻፭ ዓ. ም. ይህ ፡ ፓርቲ ፡ ከጌዲስት ፡ የፈረንሳይ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ፓርቲ ፡ በመዋሀድ ፡ አንድ ፡ የተባበረ ፡ የፈረንሳይ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ፓርቲን ፡ አቋቁመዋል ። ሌኒን ፡ የዠረስና ፡ የዠረሲስቶች ፡ ሪፎርሚስት ፡ ርዕዮቶችን ፡ በጣም ፡ ወቅሷል ። ዠረስ ፡ ለሠላም ፡ ባደረገው ፡ ትግልና ፡ በማኅበረሰብ ፡ ላይ ፡ የነበረውን ፡ ጦርነት ፡ በመቃወም ፡ በመታገሉ ፡ ኢምፔሪያሊስት ፡ ቡርዥዋ ፡ በሱ ፡ ላይ ፡ ጥላቻ ፡ አደረበት ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ መፈንዳት ፡ አጥቢያ ፡ ዠረስ ፡ በአድርባዮች ፡ በተገዙ ፡ ነብሰ ፡ ገዳዮች ፡ ተገደለ ።

በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ ወቅት ፡ የፈረን ሳይ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ፓርቲን ፡ መሪነት ፡ የጨበጡት ፡ የኢምፔሪያሊስት ፡ ጦርነትን ፡ በግልፅ ፡ በመደገፍ ፡ የሶሺያል-ሾቪኒስት ፡ አቋም ፡ ወስደዋል ፡፡

ገጽ ፤ ፪፻፩

54 የእንግሊዝ ፡ ነፃ ፡ ሌበር ፡ ፓርቲ (Independent labour party) — ሪፎርሚስት ፡ ድርጅት ፡፡ የተመሠ ረተው ፡ በ ፲፰፻፺፫ ዓ. ም. የሥራ ፡ ማቆም ፡ አድማ ፡ ትግል ፡ በጠነከረበት ፡ ሁኔታዎችና ፡ የእንግሊዝ ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ መደብ ፡ ከቡርዥዋው ፡ ፓርቲ ፡ ነፃ ፡ ለመሆን ፡ ከፍተኛ ፡ ንቅናቄ ፡ ባካሄደበት ፡ ጊዜ ፡ ነው ፡፡ በነ ፃው ፡ የሌበር ፡ ፓርቲ « የአዲሶች ፡ የሠራተኛ ፡ ማኅበራ ት » አባሎችና ፡ ብዙ ፡ የድሮ ፡ የሠራተኛ ፡ ማኅበራት ፡ አባሎች ፤ በፋቢያኖች ፡ ተፅእኖ ፡ ሥር ፡ የነበሩ ፡ ንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ተወካዮች ፡ በአባልነት ፡ ገብተዋል ፡፡ የፓርቲ ው ፡ መሪዎች ፡ ከይር ፡ ሀርዲና ፡ ራምሰይ ፡ ማክዶናልድ ፡ ሆኑ ፡፡ ነፃው ፡ የሌበር ፡ ፓርቲ ፡ ከተመሠረተ ፡ ጊዜ ፡ ጀምሮ ፡ የቡርዥዋ-ሪፎርሚስት ፡ አቋምን ፡ እንደያዘ ፡ ነው ፡፡ በመሠረቱ ፡ ያተኮረው ፡ በፓርላማዊ ፡ የትግል ፡ መንገድና ፡ ከሊበራል ፡ ፓርቲ ፡ ጋር ፡ ፓርላማዊ ፡ ስም ምነት ፡ ማድረግን ፡ ነው ፡፡ ነፃው ፡ ሌበር ፡ ፓርቲን ፡ በሚመለከት ፡ ሌኒን ፡ ሲጽፍ « በተግባር ፡ ፓርቲው ፡ ሁልጊዜ ፡ የቡርዥዋ ፡ ጥገኛ ፡ የሆነ ፡ አድርባይ ፡ ፓርቲ ፡ ነው » ብሏል ፡፡

የአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ እንደጀመረ ፡ ነፃው ፡ ሌበር ፡ ፓርቲ ፡ ጦርነቱን ፡ በመቃወም ፡ ማኒፌ ስቶ ፡ አውጥቷል ፡፡ ሆኖም ፡ ከጥቂት ፡ ጊዜ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስት ፡ አቋም ፡ ተዘፍቋል ፡፡

ገጽ ፤ ፪፻፪

## የስሞች ፡ ማጣቀሻ ፡፡

ሃይንድማን ፤ ሄንሪ (Hyndman) (፲፰፻፵፪ - ፲፱፻፳፩ ዓ. ም.) — እንግሊዛዊ ፡ ሶሺያሊስት ፤ ሬፎርሚስት ፡፡ በ ፲፰፻፹፩ ዓ. ም. ዴሞክራቲክ ፡ ፌዴሬሽንን ፡ መሠረተ ፡፡ ይህ ፡ ፌዴሬሽን ፡ በ ፲፰፻፹፬ ዓ. ም. ወደ ፡ ሶሺያል-ዴሞክ ራቲክ ፡ ፌዴሬሽን ፡ ተለውጧል ፡፡ ከ ፲፱፻ እስከ ፡ ፲፱፻፲ ዓ. ም. የዓለም ፡ አቀፍ ፡ የሶሺያሊስት ፡ ቢሮ ፡ አባል ፡፡ ከብ ሪታንያ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ፓርቲ ፡ መሪዎች ፡ አንዱ ፡፡ ፓር ቲው ፡ በሶልፎርድ ፡ ባደረገው ፡ ኮንፈረንስ ፡ በኢምፔሪ ያሊስት ፡ ጦርነት ፡ በወሰደው ፡ በሶሺያል-ሾቪኒስትነት ፡ አቋሙ ፡ ስላወገዘው ፡ ሃይንድማን ፡ በ ፲፱፻፲፮ ዓ. ም. ከፓርቲው ፡ ወጥቷል ፡፡

ገጽ ፡ ፳

ሄንደርሶን ፤ አርቱር (Henderson) (፲፰፻፷፫-፲፱፻፴፭ ዓ. ም.) — ከታወቁት ፡ ሌበር ፡ ፓርቲና ፡ የእንግሊዝ ፡ ሠራተኞች ፡ ንቅናቄ ፡ መሪዎች ፡ አንዱ ፡፡ በአንደኛው ፡ የዓ ለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስት ፡፡ በተደጋጋሚ ፡ በእንግሊዝ ፡ የቡርዥዋ ፡ መንግሥት ፡ አገዛዝ ፡ ውስጥ ፡ ተካፍሏል ፡፡

ገጽ ፡ ፸





ሄጌል ፤ ጆርጅ ፡ ዊልኼልም ፡ ፍሬደሪክ (Hegel) (፲፯፻፷፪-፲፰፻፳፫ ዓ. ም.) — ታላቅ ፡ ጀርመናዊ ፡ ፈላስፋ ፤ ኦብጀክቲቭ ፡ አይዲያሊስት ፤ የጀርመን ፡ ቡርዥዋ ፡ አይዲኦሎጂስት ። የሄጌል ፡ ታሪካዊ ፡ አስተዋፅኦ ፡ ጥልቅና ፡ ሰፊ ፡ በሆነ ፡ መንገድ ፡ ዲያሌክቲክስን ፡ ማበልፀጉ ፡ ነው ፤ ይህም ፡ ለዲያሌክተካዊ ፡ ማተሪያሊዝም ፡ ምንጭ ፡ ከሆኑት ፡ አንዱ ፡ ነው ። ይሁን ፡ እንጂ ፡ የሄጌል ፡ ዲያሌክቲክስ ፡ ከራሱ ፡ ባጠቃላይ ፡ ወግ ፡ አጥባቂ ፡ ሜታፊዚካዊ ፡ የፍልስፍና ፡ ርዕየቱ ፡ ጋር ፡ በጣም ፡ የተያያዘ ፡ አይዲያሊስት ፡ ባህርይ ፡ ነበረው ።

ገጽ ፤ ፲፫

ሉክሴምቡርግ ፤ ሮዛ (Luxemburg) (፲፰፻፷፬-፲፱፻፲፩ ዓ. ም.) — እጅግ ፡ የታወቀች ፡ የዓለም ፡ አቀፍ ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ንቅናቄ ፡ ታጋይ ፤ በሁለተኛ ፡ ኢንተርናሽናል ፡ የግራው ፡ ክንፍ ፡ ከመሩት ፡ አንዷ ። የፖላንድን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ ፓርቲ ፡ ከመሠረቱትና ፡ ከመሩት ፡ አንዷ ። ከ ፲፰፻፺፯ ዓ. ም. ጀምሮ ፡ በጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ እንቅስቃሴ ፡ ውስጥ ፡ በጣም ፡ ተካፍላለች ። የጀርመን ፡ ኮሙኒስት ፡ ፓርቲን ፡ ከመሠረቱት ፡ አንዷ ። በጥር ፡ ፲፱፻፲፩ ዓ. ም. ታሰረች ፤ ከዚያም ፡ በፀረ-አብዮተኛውያን ፡ በአሰቃቂ ፡ ሁኔታ ፡ ተገደለች ።

ገጽ ፡ ፻፳፱

ሉዊ ፡ ናፖሌዎን (Napoléon) — ናፖሌዎን ፡ ሳላሳዊን ፡ ተመልከት ።

ሊብክነኽት ፤ ዊልኼልም (Liebknecht) (፲፰፻፲፰-፲፱፻ ዓ. ም.) — የታወቀ ፡ የጀርመንና ፡ የዓለም ፡ አቀፍ ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ንቅናቄ ፡ ታጋይ ፤ የጀርመን ፡ ሶሺያል-



ዴሞክራቲክ ፡ ፓርቲ ፡ ከመሠረቱትና ፡ ከመሪዎቹ ፡ አንዱ ።

ገጽ ፤ ፻፩ ፤ ፻፬

ላሳል ፤ ፈርዲናንድ (Lassalle) (፲፰፻፲፯-፲፰፻፶፮ ዓ. ም.) — ጀርመናዊ ፡ የንዑስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ሶሺያሊስት ። በጀርመን ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ ንቅናቄ ፡ ውስጥ ፡ ላሳልያኒዝም ፡ የተባለው ፡ የአድርባይነት ፡ ልዩ ፡ ዓይነት ፡ መስራች ። ላሳል ፡ ጠቅላላ ፡ የጀርመን ፡ የወዝ ፡ አደሮች ፡ ማኅበርን (፲፰፻፶፭ ዓ. ም.) ከመሠረቱት ፡ አንዱ ፡ ነው ። የዚህ ፡ ማኅበር ፡ መመሥረት ፡ ለወዝ ፡ አደሩ ፡ ንቅናቄ ፡ በጣም ፡ ጠቃሚ ፡ ነበር ፤ ቢሆንም ፡ ላሳል ፡ የማኅበሩ ፡ ፕሬዚዴንት ፡ ሆኖ ፡ ተመርጦ ፡ ማኅበሩን ፡ ወደ ፡ አድርባይነት ፡ መርቶታል ። ላሳል ፡ በአድሃሪው ፡ ፕሩሲያ ፡ የበላይነት ፡ የጀርመን « ከበላይ » የመዋሃድን ፡ ፖሊሲ ፡ ይደግፍ ፡ ነበር ። የላሳልያውያን ፡ አድርባይ ፡ ፖለቲካ ፡ የአንደኛው ፡ ኢንተርናሽናልና ፡ በጀርመን ፡ ትክክለኛ ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ ፓርቲ ፡ ለማቋቋም ፡ በተደረገው ፡ ጥረት ፡ እንቅፋት ፡ ሆኖ ፡ ነበር ። ወዝ ፡ አደሩ ፡ መደባዊ ፡ ንቃቱን ፡ እንዳያጐለምስበትም ፡ እንቅፋት ፡ ሆኗል ።

ገጽ ፤ ፻፷፰ ፤ ፻፴፱ ፤ ፻፵ ፤ ፻፵፩

ሌጊን ፤ ካርል (Legien) (፲፰፻፶፫-፲፱፻፲፪ ዓ. ም.) — ጀርመናዊ ፡ የቀኝ ፡ ክንፍ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራት ፤ የጀርመን ፡ የሠራተኞች ፡ ማኅበር ፡ መሪ ፤ ሪቪዢኒስት ። ከ ፲፰፻፹፪ ዓ. ም. ጀምሮ ፡ የጀርመን ፡ ሠራተኛ ፡ ማኅበሮች ፡ ጠቅላላ ፡ ኮሚስዮን ፡ ሊቀ ፡ መንበር ። ከ ፲፱፻፫ ዓ. ም. ጀምሮ — ጸሐፊ ፤ ከ ፲፱፻፲፫ ዓ. ም. የዓለም ፡ አቀፍ ፡ ሠራተኞች ፡ ማኅበራት ፡ ጽሕፈት ፡ ቤት ፡ ሊቀ ፡ መንበር ። ከ ፲፰፻፹፫ ዓ. ም. (ከማቋረጥ ፡ ጋር) በሬይኽስታግ ፡ እስከ ፡ ፲፱፻፲፪ ዓ. ም. በአንደኛው ፡ የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ እንደራሴ ።





የዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ ፡ አክራሪ ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስት ። የቡርዥዋ ፡ ፖለቲካ ፡ ደጋፊ ፤ የወዝ ፡ አደር ፡ አብዮታዊ ፡ እንቅስቃሴን ፡ ተዋግቷል ።

ገጽ ፤ ፳ ፤ ፴ ፤ ፴፫ ፤ ፻፹፩

<u>ሚልየራን ፤ አሌክሳንደር ፡ ኤትዬን (Millerand)</u> (፲፰፻፶፱-፲፱፻፵፫ ዓ. ም.) — ፈረንሳዊ ፡ የፖለቲካ ፡ ሰው ። በ ፺ኛዎቹ ፡ ዓመታት ፡ ከሶሺያሊስቶች ፡ ጋር ፡ ተቀላቀለ ፤ በፈረንሳዩ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ንቅናቄ ፡ ውስጥ ፡ የአድርባይነት ፡ መስመርን ፡ መርቷል ። በ ፲፰፻፺፱ ዓ. ም. ወደ ፡ ቫልደክ-ሩሶ ፡ አድሃሪ ፡ የቡርዥዋ ፡ መንግሥት ፡ አገዛዝ ፡ ውስጥ ፡ ገብቶ ፤ የፓሪስ ፡ ኮሙንን ፡ ከደመሰሰ ፡ ከጄኔራል ፡ ጋሊፈት ፡ ጋር ፡ ሰርቷል ።

በ ፲፱፻፬ ዓ. ም. ከሶሺያሊስት ፡ ፓርቲው ፡ ከተወገደ ፡ በኋላ ፡ ሚልየራን ፡ ከሌሎች ፡ ሶሺያሊስት ፡ ከነበሩት (ብሪአን ፤ ቪቪያኒ) ጋር ፡ አብሮ « ነፃ ፡ ሶሺያሊስቶች » የተባለውን ፡ ቡድን ፡ መሠረተ ። በ ፲፱፻፱-፲፱፻፲ ፤ ፲፱፻፲፪-፲፱፻፲፫ ፤ ፲፱፻፲፬-፲፱፻፲፭ ዓመታት ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ የሚኒስትርነት ፡ ቦታዎችን ፡ ይዞ ፡ ነበር ፤ በ ፲፱፻፳-፲፱፻፳፬ ዓመታት — የፈረንሳይ ፡ ሪፑብሊክ ፡ ፕሬዚደንት ።

ገጽ ፡ ፻፵፱

<u>ሚኻይሎቭስኪይ ፤ ኒኮላይ</u> (፲፰፻፵፪-፲፱፻፬ ዓ. ም.) — የታወቀ ፡ የሊበራል ፡ እንቅስቃሴ ፡ ቴዎሬቲክ ፤ ፑብሊሲስት ፤ የሥነ ፡ ጽሑፍ ፡ ክሪቲክ ፤ ፖዘቲቪስት-ፈላስፋ ፤ በሶሺኦሎጂ ፡ የሳብጀክቲቭ (ህሊናዊ) ትምህርት ፡ ቤት ፡ ሊቅ ። በ ፲፰፻፺፪ ዓ. ም. (« የሩሲያ ፡ ሃብት ») የተባለው ፡ ፍጹም ፡ ፀረ-ማርክሲስት ፡ የሆነ ፡ መጽሔት ፡ መሪ ፡ ሆነ ።

ገጽ ፡ ፲፰

<u>ማርክስ ፤ ካርል (Marx)</u> (፲፰፻፲፰-፲፰፻፹፫ ዓ. ም.) — የሳይንሳዊ ፡ ኮሙኒዝም ፡ መሥራች ፤ የዓለም ፡ ላብ ፡ አደሮች ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ መሪና ፡ መምህር ፡ ነው ።

ገጽ ፤ ፫ ፤ ፲፪ ፤ ፲፬ ፤ ፲፯ ፤ ፳፭ ፤ ፴፪-፵፪ ፤ ፵፭ ፤ ፵፯ ፤ ፵፫ ፤ ፵፱ ፤ ፶፩-፷፪ ፤ ፷፯ ፤ ፷፷-፸፯ ፤ ፸፬ ፤ ፸፫-፹፪ ፤ ፹፬-፹፯ ፤ ፺-፺፪ ፤ ፺፫-፺፱ ፤ ፻፫ ፤ ፻፱ ፤ ፻፲ ፤ ፻፲፫ ፤ ፻፳፫ ፤ ፻፳፯-፻፵፩ ፤ ፻፵፫ ፤ ፻፵፮-፻፶፬ ፤ ፻፶፮ ፤ ፻፶፱ ፤ ፻፷፫ ፤ ፻፷-፻፷፫ ፤ ፻፷፭ ፤ ፻፷፯ ፤ ፻፷፱ ፤ ፻፸፪ ፤ ፻፸፫ ፤ ፻፸፭ ፤ ፻፸፯ ፤ ፻፸፷

<u>ሜሪንግ ፤ ፍራንጽ (Mehring)</u> (፲፰፻፵፮-፲፱፻፲፱ ዓ. ም.) — የታወቀ ፡ የጀርመን ፡ ወዝ ፡ አደር ፡ ንቅናቄ ፡ ታጋይ ። የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ ግራ ፡ ክንፍ ፡ ከመሪዎቹና ፡ ከቴዎሪ ፡ አፍላቂዎቹ ፡ አንዱ ። «Die Neue Zeit» (« አዲስ ፡ ዘመን ») የተባለው ፡ የፓርቲው ፡ የቴዎሪ ፡ ልሳን ፡ ከአዘጋጆቹ ፡ አንዱ ። የጀርመንን ፡ ኮሙኒስት ፡ ፓርቲ ፡ ለማቋቋም ፡ ከፍተኛ ፡ ሚና ፡ ተጫውቷል ።

ገጽ ፤ ፺፩

<u>ሞንተስክዬ ፤ ሻርል ፡ ሉዊ (Montesquieu)</u> (፲፮፻፹፱-፲፯፻፶፭ ዓ. ም.) — የታወቀ ፡ ፈረንሳዊ ፡ ቡርዥዋ ፡ ሶሺኦሎጂስት ፤ የኤኮኖሚ ፡ ሊቅና ፡ ደራሲ ። የ ፲፰ ኛው ፡ ክፍለ ፡ ዘመን ፡ የቡርዥዋ ፡ ትንሳኤ ፡ እንደራሴ ፤ የፓርላማዊ ፡ የዘውድ ፡ አገዛዝ (constitutional monarchy) ቴዎሪ ፡ አፍላቂ ።

ገጽ ፤ ፹፫

<u>ሩሳኖቭ ፤ ኒኮላይ</u> (በ ፲፰፻፶፱ ዓ. ም. ተወለደ) — ጋዜ





ጠኛ ፤ የሕዝብ ፡ ንቅናቄ ፡ ደጋፊ ፤ በኋላ ፡ ሶሺያሊስት-አብዮታዊ ።

ገጽ ፡ ፸፱

ሩባኖቪች ፤ ኢሊያ (፲፰፻፷-፲፱፻፳ ዓ. ም.) — ከሶሺያሊስት-አብዮታውያን ፡ መሪዎች ፡ አንዱ ። የዓለም ፡ አቀፍ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ቢሮ ፡ አባል ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስት ።

ገጽ ፡ ፷

ራዴክ ፤ ካርል (Radek) (፲፰፻፹፭-፲፱፻፴፱ ዓ. ም.) — ከ፺ኛዎቹ ፡ ዓመታት ፡ ጀምሮ ፡ በጋሊሲ ፤ በፖላንድና ፡ በጀርመን ፡ በሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ ንቅናቄዎች ፡ ተካፍሏል ። በጀርመን ፡ የግራ ፡ ክንፍ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ የጽሑፍ ፡ ሥራዎች ፡ ተካፍሏል ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ ኢንተርናሽናሊስት ፡ አቋም ፡ ነበረው ። ቢሆንም ፡ ወደ ፡ ሴንትሪዝም ፡ ማወላወልን ፡ አሳይቷል ። በብሄሮች ፡ ጥያቄ ፤ ብሄሮች ፡ የራሳቸውን ፡ እድል ፡ በራስ ፡ የመወሰን ፡ መብትን ፡ በሚመለከት ፡ ስህተተኛ ፡ አቋም ፡ ነበረው ።

ገጽ ፡ ፻፷፱

ሬኖደል ፤ ፕየር (Renaudel) (፲፰፻፸፩-፲፱፻፴፭ ዓ. ም.) — በፈረንሳይ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ፓርቲ ፡ ከሬፎርሚስት ፡ መሪዎች ፡ አንዱ ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ ፡ ሶሺያሊስት-ሾቪኒስት ።

ገጽ ፤ ፷ ፤ ፸

ሳምባት ፤ ማርሴል (Sembat) (፲፰፻፷፪-፲፱፻፳፪ ዓ. ም.) — በፈረንሳይ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ፓርቲ ፡ ከሬፎርሚስት ፡ መሪዎች ፡ አንዱ ፤ ጋዜጠኛ ። በአንደኛው ፡ ዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስት ። ከነሐሴ ፡ ፲፱፻፲፬





ዓ. ም. ጀምሮ ፡ እስከ ፡ መስከረም ፡ ፲፱፻[illegible] ዓ. ም. [illegible] የፈረንሳይ ፡ ኢምፔሪያሊስት « [illegible] ፡ መከላከል ፡ አገዛዝ » የሕዝባዊ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስትር ። በየካቲት ፡ ፲፱፻፲፭ ዓ. ም. በለንደን ፡ በተደረገው ፡ የኤንተንተ (Entente) አገሮች ፡ ሶሺያሊስቶች ፡ ኮንፈረንስ ፡ ተካፍሏል ። ኮንፈረንሱ ፡ የተጠራበት ፡ ዓላማ ፡ ሶሺያሊስቶችን ፡ በሶሺያል-ሾቪኒዝም ፡ መሰረት ፡ ለማስተባበር ፡ ነበር ።

ገጽ ፤ ፸ ፤ ፸፫

ስታውኒንግ ፤ ቶርቫልድ ፡ አውጉስት ፡ ማሪኑስ (Stauning) (፲፰፻፸፫-፲፱፻፵፪ ዓ. ም.) — የደንማርክ ፡ የመንግሥት ፡ ሠራተኛ ። የደንማርክ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶችና ፡ የሁለተኛው ፡ ኢንተርናሽናል ፡ የቀኝ ፡ ክንፍ ፡ ከመሪዎቹ ፡ አንዱ ። በሥራ ፡ መስክ — ፑብሊሲስት ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ የነበረው ፡ አቋም ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስት ። በ ፲፱፻፲፮-፲፱፻፳ ዓመታት ፡ በቡርዥዋው ፡ የደንማርክ ፡ አገዛዝ (ቦርሳ ፡ አልባ) ሚኒስትር ። ከዚያ ፡ በኋላ ፡ የሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ መንግሥት ፡ እና ፡ የቡርዥዋ ፡ ራዲካሎች (ሥር ፡ ነቀሎች) እና ፡ የቀኝ ፡ ዴሞክራቶች ፡ የትብብር ፡ መንግሥት ፡ መሪ ።

ገጽ ፤ ፸ ፤ ፻፹፩

ስትሩቬ ፤ ፒዮትር (፲፰፻፸-፲፱፻፵፬ ዓ. ም.) — የቡርዥዋ ፡ ኤኮኖሚስትና ፡ ፑብሊሲስት ፤ የኮንስቲቱሽናዊ ፡ ዴሞክራቶች (ካዴቶች) መሪ ። በ ፺ኛዎቹ ፡ ዓመታት ፡ በጣም ፡ የታወቀ « የህጋዊ ፡ ማርክሲዝም » አባል ። ማርክሲዝምንና ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ ንቅናቄ ፡ ከቡርዥዋ ፡ ጋር ፡ እንዲስማማ ፡ ለማድረግ ፡ በማርክስ ፡ የኤኮኖሚና ፡ የፍልስፍና ፡ ቴዎሪ ፡ ላይ « እርማትን » እና « ሂስን » አቅርቧል ።

ገጽ ፡ ፷




ስኮቤሌቭ ፤ ማትቬይ (፲፰፻፹፭-፲፱፻፴፰ ዓ. ም.) — ከ ፲፱፻፫ ዓ. ም. ጀምሮ ፡ በሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ ንቅናቄ ፡ ውስጥ ፡ በሜንሼቪክነት ፡ ተካፍሏል ። በአንደኛ ፡ የዓለም ፡ ጦርነት — ሴንትሪስት ። ከ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የየካቲት ፡ ቡርዥዋ ፡ ዴሞክራቲክ ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ የፔትሮግራድ ፡ ሶቪዬት ፡ ምክትል ፡ ሊቀ ፡ መንበር ፤ የማእከላዊ ፡ ሥራ ፡ አስኪያጅ ፡ ደርግ ፡ አንደኛ ፡ ጥሪ ፡ ስብሰባ ፡ ምክትል ፡ ሊቀ ፡ መንበር ፤ ከግንቦት ፡ እስከ ፡ ነሃሴ ፡ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. በቡርዥዋው ፡ ጊዜያዊ ፡ መንግሥት ፡ አገዛዝ ፡ የሥራ ፡ ሚኒስትር ።

ገጽ ፤ ፳፬ ፤ ፸፪

ስፔንሰር ፤ ሄርቤርት (Spencer) (፲፰፻፳-፲፱፻፫ ዓ. ም.) — እንግሊዛዊ ፡ ፈላስፋ ፤ ሳይኮሎጂስትና ፡ ሶሺኦሎጂስት ። የታወቀ ፡ ፖዘቲቪስት ። የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ኦርጋኒክ ፡ ቴዎሪ ፡ የሚባለውን ፡ ከመሠረቱት ፡ አንዱ ።

ገጽ ፡ ፲፰

ሸይደማን ፤ ፊሊፕ (Scheidemann) (፲፰፻፷፭-፲፱፻፴፱ ዓ. ም.) — የጀርመን ፡ ዴሞክራቲክ ፡ ፓርቲ ፡ የቀኝ ፡ አክራሪው ፡ አድርባይ ፡ ክንፍ ፡ ከመሪዎቹ ፡ አንዱ ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ ፡ የወጣለት ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስት ። በጀርመኑ ፡ የ ፲፱፻፲፰ ዓ. ም. የህዳሩ ፡ አብዮት ፡ የሕዝባዊ ፡ ወኪሎች ፡ ደርግ ፡ የተባለው ፡ አባል ፡ በመሆን ፡ በስፓርታካውያን ፡ ቡድን ፡ አባል ፡ ወኪሎች ፡ ላይ ፡ ከፍተኛ ፡ የማጥቃት ፡ ዘመቻ ፡ አካሂዷል ። በየካቲት — ሰኔ ፡ ፲፱፻፲፱ ዓ. ም. የቬይመር ፡ ሪፑብሊክ ፡ የትብብር ፡ መንግሥት ፡ መሪ ፡ በመሆን ፡ ከ ፲፱፻፲፰-፲፱፻፳፩ዓመታት ፡ ውስጥ ፡ በጀርመን ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ ንቅናቄ ፡ ላይ ፡ አሰቃቂ ፡ ጭፍጨፋዎች ፡ ካደራጁት ፡ አንዱ ፡ ነበር ። በኋላ ፡ የፖለቲካ ፡ ተግባሩን ፡ አቆመ ።

ገጽ ፤ ፰ ፤ ፸ ፤ ፸፫ ፤ ፻፹



ሽቲርነር ፤ ማክስ (Stirner) (፲፰፻፮-፲፰፻[illegible] ዓ. ም.) — ጀርመናዊ ፡ ፈላስፋ [illegible] ግለኝነት (individualism) እና ፡ ሥርዓተ-አልበኝነት ፡ አይዲኦሎጂስት ።

ገጽ ፡ ፪፻፶፯

ቢስማርክ ፤ ኦቶ (Bismarck) (፲፰፻፲፭-፲፰፻፺፰ ዓ. ም.) — የፕሩሲያና ፡ የጀርመን ፡ መንግሥት ፡ ባለሥልጣንና ፡ ዲፕሎማት ። የቢስማርክ ፡ ዋና ፡ ዓላማ ፡ የተቆራረጡት ፡ ትንንሽ ፡ የጀርመን ፡ መንግሥታትን « በደምና ፡ በብረት » አስተባብሮ ፤ በጁንከር ፡ ፕሩሲያ ፡ የበላይነት ፡ አንድ ፡ የጀርመን ፡ ግዛትን ፡ መመሥረት ፡ ነበር ። በጥር ፡ ፲፰፻፸፩ ዓ. ም. ቢስማርክ ፡ የጀርመን ፡ ግዛት (ኢምፓየር) የሬይህ ፡ ቻንስለርነትን ፡ ቦታ ፡ በመያዝ ፤ የመሬት ፡ ከበርቴ — ጁንኬሮችን ፡ ጥቅም ፡ እየጠበቀና ፤ እንደዚሁም ፡ በጁንኬሮችና ፡ በትልልቅ ፡ ቡርዥዋዎች ፡ መካከል ፡ ኅብረትን ፡ ለመመሥረት ፡ እየሞከረ ፤ ለሃያ ፡ ዓመታት ፡ የጀርመን ፡ መላ ፡ የውጭና ፡ የውስጥ ፡ የፖለቲካ ፡ ሕይወትን ፡ መርቷል ። በሱ ፡ አሳሳቢነት ፡ በ ፲፰፻፸፰ ዓ. ም. በተላለፈው ፡ ፀረ-ሶሺያሊስት ፡ አዋጅ ፡ መሠረት ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ መደብ ፡ ንቅናቄ ፡ አንቆ ፡ ለመግደል ፡ ያደረገው ፡ ሙከራ ፡ ስላልተሳካለት ፤ ቢስማርክ ፡ የአንዳንድን ፡ የሠራተኞች ፡ ፈርጆች ፡ ዋስትና ፡ የሚጠብቅ ፡ ሕግ ፡ ያለበትን ፡ ቀኖናዊ ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ሕጋዊ ፡ ፕሮግራም ፡ አቀረበ ። ቢሆንም ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ መደብ ፡ ንቅናቄ ፡ በማይረባ ፡ ምፅዋት ፡ በማዳከም ፤ ለማከፋፈል ፡ ያደረገው ፡ ሙከራ ፡ ውድቅ ፡ ሆኗል ። በ ፲፰፻፺ ዓ. ም. ከሥልጣን ፡ ወረደ ።

ገጽ ፡ ፳፪

ቢሶላቲ ፤ ሌኦኒዳ (Bissolati) (፲፰፻፶፯-፲፱፻፳ ዓ. ም.) — የኢጣልያን ፡ ሶሺያሊስት ፡ ፓርቲ ፡ ከመሠረቱት ፡ አንዱና ፡ የዚሁ ፡ ፓርቲ ፡ የአክራሪው ፡ ጠጋኝ ፡ ቀኝ ፡ ክንፍ ፡ መሪ ።

በ ፲፱፻፲፪ ዓ. ም. ከኢጣልያው ፡ ሶሺያሊስት ፡ ፓርቲ ፡ ተባረረ ፤ ከዚያም « ሶሺያል-ሬፎርሚስት ፡ ፓርቲን » መሠረተ ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስት ። ኢጣልያ ፡ በጦርነቱ ፡ ወቅት ፡ በኤንተንተ (Entente) ጐን ፡ ተሰልፋ ፡ እንድትዋጋ ፡ ደግፏል ። ከ ፲፱፻፲፮ እስከ ፡ ፲፱፻፲፰ ዓ. ም. በመንግሥቱ ፡ እንደ ፡ ሚኒስትር ፡ ሆኖ ፡ ሰርቷል ።

ገጽ ፡ ፸

<u>ባኩኒን ፤ ሚኻኢል</u> (፲፰፻፲፬-፲፰፻፸፮ ዓ. ም.) — የናሮድኒዝምና ፡ የሥርዓተ-አልበኝነት ፡ ርዕዮተ ፡ ዓለም ፡ ከአይዲኦሎጂስቶቹ ፡ አንዱ ። ከ ፲፰፻፵ ዓ. ም. ጀምሮ ፡ ከሩሲያ ፡ ውጭ ፡ ይኖር ፡ ነበር ። በጀርመኑ ፡ ፲፰፻፵፰-፲፰፻፵፱ ዓመታት ፡ አብዮት ፡ ተካፍሏል ። የአንደኛው ፡ ኢንተርናሽናል ፡ አባል ፡ ነበር ፤ በዚሁም ፡ የማርክሲዝም ፡ ጠላት ፡ መሆኑን ፡ አሳይቷል ። ባኩኒን ፡ ማንኛውም ፡ ዓይነት ፡ መንግሥት ፤ የወዝ ፡ አደሩን ፡ የበላይ ፡ ሥልጣን ፡ ጭምር ፡ ይቃወማል ፤ አይቀበልም ። በዓለም ፡ ታሪክ ፡ ውስጥ ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ ሚና ፡ ስላልተገነዘበ ፡ ወዝ ፡ አደሩ ፡ የፖለቲካ ፡ እንቅስቃሴ ፡ ውስጥ ፡ ከመካፈል ፡ መቆጠብ ፡ አለበት ፡ በሚል ፡ እምነት ፤ ነፃ ፡ ሆኖ ፡ ራሱን ፡ የቻለ ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ የፖለቲካ ፡ ፓርቲ ፡ ማቋቋምን ፡ አምርሮ ፡ተቃውሚል ። ማርክስና ፡ ኤንግልስ ፡ የባኩኒን ፡ አድኅሪ ፡ ርዕዮቶችን ፡ በጥብቅ ፡ ተቃውመዋል ። በከፋፋይነት ፡ ተግባሩም ፡ ባኩኒን ፡ በ ፲፰፻፷፰ ዓ. ም. በኢንተርናሽናል ፡ ተባሯል ።

ገጽ ፤ ፹፩ ፤ ፪ ፤ ፩፻፶፯

<u>ቤርንስተይን ፤ ኤድዋርድ (Bernstein)</u> ፲፰፻፶-፲፱፻፴፪ ዓ. ም.) — የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ ፓርቲ ፡ የአድርባይነት ፡ አክራሪ ፡ ክንፍና ፡ የሁለተኛው ፡ ኢንተርናሽናል ፡ መሪ ። የበላበነትና ፡ የጠጋኝነት ፡ ተዋሪዎች ፡ አፍላቂ ። ከ ፸ኛዎቹ ፡ ዓመታት ፡ አጋማሽ ፡ ጀምሮ ፡ በሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ እንቅስቃሴ ፡ ውስጥ ፡ ተካፍሏል ። ከ ፲፰፻፹፩ እስከ ፡ ፲፰፻፹፱ ዓ. ም. ድረስ «Der Sozial-demokrat» (« ሶሺያል-ዴሞክራት ») የተባለውን ፡ የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ ፓርቲ ፡ ማዕከላዊ ፡ ልሳን ፡ አዘጋጅ ፡ ነበር ። በ ፲፰፻፺፮-፲፰፻፺፰ ዓመታት ፡ ውስጥ «Die Neue Zeit» (« አዲስ ፡ ዘመን ») በተባለው ፡ መጽሔት ፡ ውስጥ « የሶሺያሊዝም ፡ ፕሮብሌሞች »በሚል ፡ ተከታታይ ፡ ጽሑፎች ፡ አቅርቧል ። በኋላም « የሶሺያሊዝም ፡ ተቀዳሚ ፡ መሠረታዊ ፡ ሃሳቦችና ፡ የሶሺያል-ዴሞክራሲ ፡ ተግባሮች » በሚል ፡ ርዕስ ፡ በመጽሐፍ ፡ መልክ ፡ ታትሞ ፡ ወጥቷል ። በነዚህ ፡ ስራዎች ፡ ውስጥ ፡ ቤርንስተይን ፡ የአብዮታዊውን ፡ ማርክሲዝም ፡ የፍልስፍና ፡ የኤኮኖሚና ፡ የፖለቲካ ፡ መርሆችን ፡ ለመቀልበስ ፤ ለመከለስ ፤ ለመበረዝ ፡ ይሞክራል ። በቤርንስተይን ፡ አባባል ፡ የወዝ ፡ አደሩን ፡ የኤኮኖሚ ፡ ሁኔታ ፡ ለማሻሻል ፡ በካፒታሊዝም ፡ ሥር ፡ ለጥገናዊ ፡ ለውጥ ፡ መታገል ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ መደብ ፡ እንቅስቃሴ ፡ ዋና ፡ አላማ ፡ መሆን ፡ አለበት ፡ ነው ። በዚህም ፡ ምክንያት « እንቅስቃሴ ፡ ሁሉም ፡ ነው ፤ የመጨረሻው ፡ ዓላማው — ምንም » የሚል ፡ የአድርባይ ፡ ፎርሙላ ፡ አቅርቧል ። በኢምፔሪያሊስቱ ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ ጊዜ ፡ የሶሺያል-ሾቪኒስትነቱን ፡ በኢንተርናሽናሊዝም ፡ አረፍተ ፡ ነገሮች ፡ በመሸፋፈን ፤ የሴንትሪስት (የመሃል) አቋም ፡ ይዞ ፡ ነበር ። በኋላ ፡ የኢምፔሪያሊስት ፡ ቡርዥዋ ፡ መመሪያዎችን ፡ ደግፏል ። የጥቅምቱ ፡ ሶሺያሊስት ፡ አብዮትንና ፡ የሶቪዬት ፡ መንግሥትን ፡ ተቃውሟል ።

ገጽ ፤ ፰፯ ፤ ፷፱-፹፪ ፤ ፩፻፶፱-፩፻፰፪ ፤
፩፻፰፯ ፤ ፩፻፷፫ ፤ ፩፻፷፯ ፤

<u>ቤቤል ፤ አውጉስት (Bebel)</u> (፲፰፻፵-፲፱፻፲፫ ዓ. ም.) —

የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራሲና ፡ የዓለም ፡ አቀፍ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ እንቅስቃሴ ፡ የታወቀ ፡ ታጋይ ።

ገጽ ፤ ፺፯ ፤ ፻፩ ፤ ፻፳፯ ፤ ፻፳፰ ፤ ፻፴፩

ብራንቲንግ ፤ ካርል ፡ ያልማር (Branting) (፲፰፻፷-፲፱፻፳፭ ዓ. ም.) — የስዊድን ፡ ሶሺያል ፡ ዴሞክራቲክ ፡ ፓርቲ ፡ መሪ ፤ ከ ፪ኛ ፡ ኢንተርናሽናል ፡ መሪዎች ፡ አንዱ ። አቋሞቹ ፡ የአድርባይ ፡ ነበሩ ። በ ፲፱፻፳ ዓ. ም. በሊበራል ፡ ሶሺያሊስታዊ ፡ የትብብር ፡ የኤደን ፡ መንግሥት ፡ ውስጥ ፡ ገብቶ ፡ ነበር ።

ገጽ ፤ ፸ ፤ ፻፹፩

ብራኬ ፤ ዊልኼልም (Bracke) (፲፰፻፵፪-፲፰፻፹ ዓ. ም.) — ጀርመናዊ ፡ ሶሺያሊስት ፡ አታሚና ፡ የመጻሕፍት ፡ ነጋዴ ። የኤይዘናክ ፡ ፓርቲ (፲፰፻፷፱ ዓ. ም.) ከመሥራቾቹና ፡ ከመሪዎቹ ፡ አንዱ ።

ገጽ ፤ ፺፯ ፤ ፻፳፯

ብሬሽኮ-ብሬሽኮቭስካያ ፤ ኤካቴሪና (፲፰፻፵፬-፲፱፻፴፬ ዓ. ም.) — የሶሺያሊስት-አብዮታዊ ፡ ፓርቲ ፡ ከአደራጅዎቹና ፡ ከመሪዎቹ ፡ አንዷ ፤ የዚህ ፡ ፓርቲ ፡ የቀኝ ፡ አክራሪ ፡ ክንፍ ፡ ወገን ፡ ነበረች ። ከ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የየካቲቱ ፡ የቡርዥዋ ፡ ዴሞክራቲክ ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ ጊዜያዊውን ፡ መንግሥት ፡ በጣም ፡ ትደግፍ ፡ ነበር ። የኢምፔሪያሊስቱ ፡ ጦርነት « እስከ ፡ መጨረሻው ፡ ድል ፡ ድረስ » እንዲቀጥል ፡ ደግፋለች ። ከጥቅምቱ ፡ የሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ የሶቪዬት ፡ ሥልጣንን ፡ በጣም ፡ ተቃውማለች ።

ገጽ ፡ ፳

ቦናፓርት ፤ ሉዊ — ናፖሌዎን ፡ ሳልሳዊን ፡ ተመልከት ።



ቱራቲ ፡ ፊሊፖ (Turati) (፲፰፻፶፯-፲፱፻፴፪ ዓ. ም.) — የኢጣልያ ፡ የሠራተኛ ፡ ንቅናቄ ፡ ተካፋይ ፤ የኢጣልያ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ፓርቲ ፡ (፲፰፻፺፪ ዓ. ም.) ካደራጁት ፡ አንዱ ፡ ሲሆን ፡ የዚሁ ፡ ፓርቲ ፡ የጠጋኙ ፡ የቀኝ ፡ ክንፍ ፡ መሪ ።

ገጽ ፡ ፻፹፩

ቱጋን-ባራኖቭስኪይ ፤ ሚኻኢል (፲፰፻፷፭-፲፱፻፲፱ ዓ. ም.) — ሩሲያዊ ፡ የቡርዥዋ ፡ ኤኮኖሚስት ። በ፺ኛዎቹ ፡ ዓመታት « የሕጋዊ ፡ ማርክሲዝም » የታወቀ ፡ ደጋፊ ። በ ፲፱፻፭-፲፱፻፯ ዓመታቱ ፡ አብዮት ፡ የኮንስቲቱሽናል ፡ ዴሞክራቶች (የካዴቶች) ፓርቲ ፡ አባል ። ከጥቅምቱ ፡ ሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ በኡክራይና ፡ በነበረው ፡ ፀረ-አብዮት ፡ ተግባር ፡ ተካፍሏል ።

ገጽ ፡ ፻፸፩

ትሬቨስ ፤ ክላውዲኦ (Treves) (፲፰፻፷፰-፲፱፻፴፫ ዓ. ም.) — የኢጣልያ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ፓርቲ ፡ ከጠጋኝ ፡ መሪዎቹ ፡ አንዱ ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ ፡ ሴንትሪስት ።

ገጽ ፡ ፻፹፩

ቼርኖቭ ፤ ቪክተር (፲፰፻፸፫-፲፱፻፶፪ ዓ. ም.) — የሶሺያሊስት-አብዮታዊ ፡ ፓርቲ ፡ መሪና ፡ የቴዎሪ ፡ አፍላቂ ። በአንደኛ ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፤ ምንም ፡ እንኳ ፡ በግራ ፡ ቃላት ፡ ለመሸፋፈን ፡ ቢሞክርም ፡ እውነተኛ ፡ አቋሙ ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስት ፡ ነበር ። በ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የቡርዥዋው ፡ ጊዜያዊ ፡ መንግሥት ፡ አገዛዝ ፡ የእርሻ ፡ ሚኒስትር ። ከታላላቅ ፡ ባለመሬቶች ፡ መሬት ፡ የነጠቁ ፡ አርሶ ፡ አደሮችን ፡ በሚመለከት ፡ ፖሊሲው ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ ከፍተኛ ፡ ጭቆናንና ፡ ግፍን ፡ አካሂዷል ። ከጥቅምቱ ፡ ሶሺያሊስት ፡

አብዮት ፡ በኋላ ፡ ፀረ-ሶቪዬት ፡ አድማዎችን ፡ አደራጅ ቷል ፡፡

ገጽ ፤ ፰ ፤ ፳፬ ፤ ፸፪ ፤ ፻፳፪ ፤ ፻፵፪ ፤ ፻፵፫ ፤ ፻፷፩ ፤

<u>ናፖሌዎን ፡ ቀዳማዊ (ቦናፓርት)</u> (፲፯፻፷፱-፲፰፻፳፩ ዓ. ም.) — ከ ፲፰፻፬-፲፰፻፲፬ እና ፡ በ ፲፰፻፲፭ ዓ. ም. የፈረንሳይ ፡ ንጉሥ (Emperor) ፡፡

ገጽ ፤ ፹፫ ፤ ፻፲፯

<u>ናፖሌዎን ፡ ሳልሳዊ (ቦናፓርት ፡ ሉዊ ፤ ሉዊ ፡ ናፖሌዎን)</u> (፲፰፻፰-፲፰፻፸፫ ዓ. ም.) — ከ ፲፰፻፶፪ እስከ ፡ ፲፰፻፸ ዓ. ም. ድረስ ፡ የፈረንሳይ ፡ ንጉሥ ፡፡ የናፖሌዎን ፡ ቀዳማዊ ፡ የአ ጐቱ ፡ ልጅ ፡፡

ገጽ ፡ ፳፯

<u>አቭክሴንትዬቭ ፤ ኒኮላይ</u> (፲፰፻፸፰-፲፱፻፵፫ ዓ. ም.) — የሶሺያሊስት-አብዮታዊ ፡ ፓርቲ ፡ መሪና ፡ የማእከላዊው ፡ ኮሚቴ ፡ አባል ፡፡ በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስት ፡፡ ከ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የየካቲት ፡ ቡር ዥዋ ፡ ዴሞክራሲ ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ የመላ ፡ ሩሲያ ፡ ገበሬ ዎች ፡ እንደራሴዎች ፡ ሥራ ፡ አስኪያጅ ፡ ኮሚቴ ፡ ሊቀ ፡ መንበር ፡፡ በሁለተኛው ፡ የትብብር ፡ ጊዜያዊ ፡ መንግሥት ፡ የአገር ፡ ግዛት ፡ ሚኒስትር ፤ በኋላ ፡ የፀረ-አብዮቱ « የሩ ሲያ ፡ ሪፑብሊክ ፡ ጊዜያዊ ፡ ምክር ፡ ቤት » ሊቀ ፡ መንበር (በቅደመ ፡ ፓርላማ) ፡፡ ከጥቅምቱ ፡ ሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ ፀረ-አብዮታዊ ፡ አድማዎችን ፡ አደራጅቷል ፡፡

ገጽ ፤ ፳፬ ፤ ፸፪

<u>ኤንግልስ ፤ ፍሬደሪክ (Engels)</u> (፲፰፻፳-፲፰፻፺፭ ዓ. ም.) — የሳይንሳዊ ፡ ኮሙኒዝምን ፡ ከመሠረቱት ፡ አንዱ ፤



የዓለም ፡ አቀፍ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ መሪ ፤ የማርክስ ፡ ጓደኛና ፡ የሥራ ፡ ጓድ ፡፡

ገጽ ፤ ፰ ፤ ፲፪ ፤ ፲፮-፳፩ ፤ ፳፫-፳፮ ፤ ፳፯-፴፩ ፤ ፴፪ ፤ ፵፮ ፤ ፵፱ ፤ ፶፮ ፤ ፷፪ ፤ ፸፮ ፤ ፸፱-፹፩ ፤ ፹፫-፻፳፫ ፤ ፻፳፬-፻፳፯ ፤ ፻፴፩ ፤ ፻፵፩ ፤ ፻፵፯ ፤ ፻፶፫ ፤ ፻፶፯ ፤ ፻፷፩-፻፷፫ ፤ ፻፷፮ ፤ ፻፷፯ ፤ ፻፸፫

<u>ኩገልማን ፤ ሉድቪግ (Kugelmann)</u> (፲፰፻፴-፲፱፻፪ ዓ. ም.) — ጀርመናዊ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራት ፤ የማርክስ ፡ ጓደኛ ፡፡ በ ፲፰፻፵፰-፲፰፻፵፱ ዓመታት ፡ በጀርመን ፡ በተካ ሄደው ፡ አብዮት ፡ ተካፍሏል ፡፡ የአንደኛው ፡ ኢንተርናሽ ናል ፡ አባል ፡፡

ገጽ ፤ ፶፫

<u>ካውትስኪይ ፤ ካርል (Kautsky)</u> (፲፰፻፶፬-፲፱፻፴፰ ዓ. ም.) — የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራሲና ፡ የሁለተኛው ፡ ኢንተርናሽናል ፡ ከመሪዎቹ ፡ አንዱ ፡፡ በመጀመሪያ ፡ ማርክ ሲስት ፡ ነበር ፤ በኋላ ፡ ግን ፡ ማርክሲዝምን ፡ ካደ ፡፡ «Die Neue Zeit» (« አዲስ ፡ ዘመን ») የተባለውን ፡ የጀርመን ፡ ሶሺያል ፡ ዴሞክራሲ ፡ የቴዎሪ ፡ መጽሔት ፡ አዘጋጅ ፡፡

በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስትነ ቱን ፡ በኢንተርናሽናሊስት ፡ ሀረጎት ፡ በመሸፋፈን ፡ የሴ ንትሪስት ፡ አቋም ፡ ነበረው ፡፡ « ኡልትራ-ኢምፔሪያሊ ዝም » የተባለው ፡ አድኃሪ ፡ ቴዎሪ ፡ ፈጠረ ፡፡ ከጥቅምቱ ፡ ሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ አብዮትን ፤ የወዝ ፡ አደሩ ፡ የበላይ ፡ ሥልጣንንና ፡ የሶቪዬት ፡ መንግ ሥትን ፡ በግልፅ ፡ ተቃውሟል ፡፡

ገጽ ፤ ፱ ፤ ፲፪ ፤ ፳፪ ፤ ፵፬ ፤ ፶፬ ፤

፸ ፣ ፹ ፣ ፻፩ ፣ ፻፪ ፣ ፻፲፯ ፣ ፻፶፯ ፣ ፻፶፰ ፣ ፻፶፱ ፣ ፻፷፩-፻፸፯ ፣ ፻፸፱-፻፹፩

ኬሬንስኪይ ፣ አሌክሳንደር (፲፰፻፹፩-፲፱፻፸ ዓ. ም.) — ሶሺያሊስት-አብዮታዊ ። ከ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የየካቲቱ ፡ ቡርዥዋ ፡ ዴሞክራቲክ ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ የፍርድ ፡ ሚኒስትር ፣ የጦር ፡ ሚኒስትር ፣ የባሕር ፡ ኃይል ፡ ሚኒስትር ፣ ከዚያም ፡ የጊዜያዊው ፡ መንግሥት ፡ ጠቅላይ ፡ ሚኒስትርና ፡ የበላይ ፡ ጠቅላይ ፡ አዛዥ ፡ ነበር ። ከጥቅምቱ ፡ ሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ የሶቪዬት ፡ መንግሥትን ፡ በመቃወም ፡ በጣም ፡ ታግሏል ። በ ፲፱፻፲፰ ዓ. ም. ከሩሲያ ፡ ሸሽቶ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አገር ፡ ሄደ ።

ገጽ ፣ ፳፫ ፣ ፻፲፪

ክሮፖትኪን ፣ ፒዮትር (፲፰፻፵፪-፲፱፻፳፩ ዓ. ም.) — ዋና ፡ የሥርዓተ-አልበኝነት ፡ ደጋፊና ፡ የቴዎሪ ፡ አፍላቂ ። በአንደኛው ፡ ዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ ፡ ሾቪኒስት ። በ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. ከስደት ፡ ተመለሰ ፣ የቡርዥዋ ፡ ርዕዮተ ፡ ዓለም ፡ ደጋፊ ። ቢሆንም ፡ በ ፲፱፻፳ ዓ. ም. ለአውሮፓ ፡ ወዝ ፡ አደሮች ፡ ባቀረበው ፡ ጽሑፍ ፡ ውስጥ ፡ የጥቅምቱ ፡ ሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ ታሪካዊነት ፡ ትርጉም ፡ በማመን ፣ ወዝ ፡ አደሮችን ፡ በሶቪዬት ፡ መንግሥት ፡ ላይ ፡ የሚደረገውን ፡ የጦር ፡ ወረራን ፡ እንዲያደናቅፉ ፡ ጥሪ ፡ አቅርቧል ።

ገጽ ፣ ፻፵፫ ፣ ፻፸፫

ኮልብ ፣ ዊልኼልም (Kolb) (፲፰፻፸-፲፱፻፲፰ ዓ. ም.) — የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራት ፣ አክራሪ ፡ አድርባይ ፡ ሪቪዢኒስት ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስት ።

ገጽ ፡ ፻፹፩



ኮርኔሊሰን ፣ ኽሪስቲአን (Cornelissen) — ሆላንዳዊ ፡ ሥርዓተ-አልበኛና ፡ የክሮፖትኪን ፡ ተከታይ ። ፀረ-ማርክሲስት ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ ፡ ሾቪኒስት ።

ገጽ ፡ ፻፵፫

ዘንዚኖቭ ፣ ቭላዲሚር (በ ፲፰፻፹፫ ዓ. ም. ተወለደ) — የሶሺያሊስት-አብዮታዊ ፡ ፓርቲ ፡ ከመሪዎቹ ፡ አንዱ ፣ የማእከላዊ ፡ ኮሚቴ ፡ አባል ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት « የአባት ፡ አገርን ፡ ተከላከሉ! » የሚለው ፡ ታክቲክ ፡ አፈቀላጤ ፡ ነበር ። በ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የፔትሮግራድ ፡ ሶቪዬት ፡ ሥራ ፡ አስኪያጅ ፡ ኮሚቴ ፡ አባል ፣ ከቡርዥዋው ፡ ጋር ፡ ኅብረት ፡ ይመሥረት ፡ ባይ ፡ ነበር ። ዘንዚኖቭ « ዴሎ ፡ ናሮዳ » (« የሕዝብ ፡ ጉዳይ ») የተባለው ፡ የሶሺያሊስት-አብዮታዊ ፡ ፓርቲ ፡ ልሳን ፡ ከአዘጋጆቹ ፡ አንዱ ። ከጥቅምቱ ፡ ሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ የሶቪዬት ፡ መንግሥት ፡ ጠላት ።

ገጽ ፡ ፸፪

ዠረስ ፣ ዣን (Jaures) (፲፰፻፶፱-፲፱፻፲፬ ዓ. ም.) — የፈረንሳይና ፡ የዓለም ፡ አቀፍ ፡ የሶሺያሊስት ፡ ንቅናቄ ፡ የታወቀ ፡ ሰው ፣ የታሪክ ፡ ጸሐፊ ። በ ፲፰፻፹፭-፲፰፻፹፱ ፣ በ ፲፰፻፺፫-፲፰፻፺፰ ፣ በ ፲፱፻፪-፲፱፻፲፬ ዓመታት ፡ የፓርላማ ፡ አባል ። በፓርላማ ፡ ውስጥ ፡ የሶሺያሊስት ፡ ቡድን ፡ መሪ ። በ ፲፱፻፲፬ ዓ. ም. ፣ እስከ ፡ መጨረሻ ፡ ሕይወቱ ፡ ድረስ ፡ አዘጋጅ ፡ ሆኖ ፡ የሠራበትን «L'Humanite» (ሰብአዊነት) የተባለውን ፡ ጋዜጣ ፡ መሠረተ ። ዠረስ ፡ ለዴሞክራሲ ፣ ለሕዝቦች ፡ ነፃነት ፣ ለሰላም ፡ እየታገለ ፣ የኢምፔሪያሊስት ፡ ብዝበዛንና ፡ የወረራ ፡ ጦርነቶችን ፡ ተዋግቷል ። ጦርነትንና ፡ የቅኝ ፡ ግዛት ፡ ጭቆናን ፡ አንዴና ፡ እስከ ፡ መጨረሻ ፡ ለማጥፋት ፡ የሚችለው ፡ ሶሺያሊዝም ፡ ብቻ ፡





እንደሆነ ፡ ገ፦ረስ ፡ በእርግጥ ፡ ያምን ፡ ነበር ። ይሁን ፡ እንጂ ፤ በገ፦ረስ ፡ እምነት ፡ ሶሺያሊዝም ፡ ግቡን ፡ የሚመታው ፡ በወዝ ፡ አደሩና ፡ በቡርዥዋው ፡ መካከል ፡ በሚደረገው ፡ የመደብ ፡ ትግል ፡ ሳይሆን ፤ « በዴሞክራቲካዊ ፡ ሀሳቦች ፡ ማበብ » ውጤት ፡ ነው ። ወደ ፡ አድርባይነት ፡ ሰፈር ፡ የገፋፉት ፡ የገ፦ረስ ፡ ጥገናዊ ፡ ርእየቶችን ፡ ሌኒን ፡ በጣም ፡ ተቃውሟል ።

ገ፦ረስ ፡ ለሰላምና ፡ በማንዣበብ ፡ ላይ ፡ የነበረውን ፡ ጦርነት ፡ በመቃወም ፡ በመታገሉ ፡ የኢምፔሪያሊስት ፡ ቡርዥዋ ፡ በሱ ፡ ላይ ፡ ጥላቻ ፡ አደረበት ። በአንደኛው ፡ ዓለም ፡ ጦርነት ፡ ዋዜማ ፡ ገ፦ረስ ፡ በአድሃሪዎች ፡ በተገዙ ፡ ነፍሰ ፡ ገዳዮች ፡ ተገደለ ።

ገጽ ፤ ፻፶፱

ዱሪንግ ፤ የቨጌኒይ (Dühring) (፲፰፻፴፫-፲፱፻፳፩ ዓ. ም.) — ጀርመናዊ ፡ ፈላስፋና ፡ የኤኮኖሚ ፡ ሊቅ ፤ የንኡስ ፡ ቡርዥዋ ፡ አይዲኦሎጂስት ።

ገጽ ፡ ፳፫ ፤ ፴፫

ዳቪድ ፤ ኤድዋርድ (David) (፲፰፻፷፫-፲፱፻፴ ዓ. ም.) — የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ ፓርቲ ፡ ቀኝ ፡ ክንፍ ፡ ከመሪዎቹ ፡ አንዱ ፤ ከላሽ ። በትምህርቱ ፡ የኤኮኖሚ ፡ ሊቅ ። ከ ፲፱፻፫ ዓ. ም. ጀምሮ ፡ የሬይኽስታግ ፡ እንደራሴ ። በአንደኛው ፡ ዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ — ሶሺያል-ሾቪኒስት ።

ገጽ ፤ ፫ ፤ ፸ ፤ ፻፹፩

ጌ ፤ አሌክሳንደር (በ ፲፱፻፲፱ ዓ. ም. ሞተ) — ሩሲያዊ ፡ ሥርዓተ-አልበኛ ። በጥቅምቱ ፡ ሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ በኋላ — የሶቪዬት ፡ መንግሥት ፡ ደጋፊ ።

ገጽ ፡ ፻፵፫



ጌድ ፤ ዡል (Guesde) (ባዚል ፤ ማትየ) (፲፰፻፵፭-፲፱፻፳፪ ዓ. ም.) — የፈረንሳይ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ንቅናቄንና ፡ የ፪ኛ ፡ ኢንተርናሽናልን ፡ ከአደራጇዎቹና ፡ ከመሪዎቹ ፡ አንዱ ። ጌድና ፡ ደጋፊዎቹ ፡ በ ፲፱፻፩ ዓ. ም. የፈረንሳይ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ፓርቲን ፡ መሠረቱ ። ይህ ፡ ፓርቲ ፡ በ ፲፱፻፭ ዓ. ም. ከጠጋኙ ፡ የፈረንሳይ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ፓርቲ ፡ ጋር ፡ በመጣመር ፡ የተባበረ ፡ የፈረንሳይ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ፓርቲ ፡ መሠረቱ ። ጌድ ፡ የማርክሲስት ፡ ሃሳቦችን ፡ ለማስፋፋትና ፡ በፈረንሳይ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ንቅናቄውን ፡ ለማሳደግ ፡ በጣም ፡ ብዙ ፡ ሠርቷል ።

ይሁን ፡ እንጂ ፡ ጌድ ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ ቀኝ ፡ ክንፍ ፡ ሶሺያሊስቶችን ፡ ቢዋጋም ፡ በቴዎሪም ፡ ሆነ ፡ በታክቲክ ፡ ጥያቄዎች ፡ ላይ ፡ ሴክታርያን ፡ ስልትን ፡ በመከተል ፡ ስህተት ፡ ፈጽሟል ። አንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ ሲጀመር ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስት ፡ አቋም ፡ ወስዷል ፤ በፈረንሳይ ፡ የቡርዥዋ ፡ መንግሥት ፡ ሠርቷል ።

ገጽ ፡ ፫

ግራቭ ፤ ዣን (Grave) (፲፰፻፵፬-፲፱፻፴፱ ዓ. ም.) — የፈረንሳይ ፡ የንኡስ ፡ ቡርዥዋ ፡ ሶሺያሊስት ፤ የሥርዓተ-አልበኝነት ፡ ቴዎሪ ፡ ከአፈለቁት ፡ አንዱ ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ — ሶሺያል-ሾቪኒስት ።

ገጽ ፡ ፻፵፫

ጸረተሊ ፤ ኢራክሊይ (፲፰፻፹፩-፲፱፻፶፱ ዓ. ም.) — ከሜንሼቪኮች ፡ መሪዎች ፡ አንዱ ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ ፡ ሴንትሪስት ። ከ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የየካቲቱ ፡ ቡርዥዋ ፡ ዴሞክራቲክ ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ በቡርዥዋው ፡ ጊዜያዊ ፡ መንግሥት ፡ የፖስታና ፡ የቴሌግራፍ ፡ ሚኒስትር ፤ በኋላ ፡ የአገር ፡ ግዛት ፡ ሚኒስትር ። የቦልሼቪኮችን ፡ የማሳደድ ፡ ተግባር ፡ ዋና ፡ አዘጋጅ ። ከጥቅምቱ ፡



ሶሺያሊስት ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ ጻረተሊ ፡ የጆርጅያ ፡ የፀረ-አብዮታዊው ፡ የሜንሼቪኮች ፡ መንግሥት ፡ ከመሪዎቹ ፡ አንዱ ፡ ነበር ። የሶቪዬት ፡ ሥልጣን ፡ በጆርጅያ ፡ ውስጥ ፡ ድል ፡ ከተቀዳጀ ፡ በኋላ ፡ ነጭ ፡ ስደተኛ ።

ገጽ ፤ ፰ ፤ ፳፬ ፤ ፸፪ ፤ ፻፲፬ ፤ ፻፲፭ ፤ ፻፳፪ ፤ ፻፴፪ ፤ ፻፵፯ ፤ ፻፵፰ ፤ ፻፹፩

ፓልቺንስኪይ ፤ ፒዮትር (፲፰፻፷፯-፲፱፻፳፩ ዓ. ም.) — መሃንዲስ ፤ « የፕሮዱጎል » ሲንዲኬት ፡ አደራጅ ። ከየካቲቱ ፡ ፲፱፻፲ ዓ. ም. ቡርዥዋ ፡ ዴሞክራቲክ ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፤ በጊዜያዊው ፡ ቡርዥዋ ፡ መንግሥት ፡ ውስጥ ፡ የንግድና ፡ የኢንዱስትሪ ፡ ዴፑቲ ፡ ሚኒስትር ፡ ሆነ ። የኢንዱስትሪ ፡ አሻጥር ፡ ዋና ፡ አዘጋጅ ፤ የዴሞክራቲክ ፡ ድርጅቶች ፡ ፀር ።

ገጽ ፤ ፴፫ ፤ ፴፩

ፓኔኩክ ፤ አንቶኒ (Panneckock) (፲፰፻፷፭-፲፱፻፶፪ ዓ. ም.) — ሆላንዳዊ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራት ። ከ ፲፱፻፪ ዓ. ም. ጀምሮ ፡ ከግራ ፡ የጀርመን ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቶች ፡ ጋር ፡ ጥብቅ ፡ ግንኙነት ፡ ነበረው ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ ፡ ኢንተርናሽናሊስት ። «Vorbote» (« ዋዜማ ») በተባለው ፡ የግራ ፡ የዚመርቫልድ ፡ የቴዎሪ ፡ ልሳን ፡ መጽሔት ፡ በአዘጋጅነት ፡ ተካፍሏል ። በ ፲፱፻፲-፲፱፻፲፫ ዓ. ም. የሆላንድ ፡ ኮሙኒስት ፡ ፓርቲ ፡ አባል ፤ የኮሚንተርን ፡ ሥራ ፡ ተካፍሏል ። አቋሙ ፡ ግራ ፡ ቀደምት ፤ ሴክታሪያን ።

ገጽ ፤ ፻፷፱-፻፸፩ ፤ ፻፸፪

ፕሌኻኖቭ ፤ ጌኦርጊይ (፲፰፻፵፰-፲፱፻፲ ዓ. ም.) — በሩሲያና ፡ በዓለም ፡ አቀፍ ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ ንቅናቄ ፡ ውስጥ ፡ በጣም ፡ የታወቀ ፡ ሰው ። በሩሲያ ፡ የመጀመሪያ ፡ የማርክሲዝም ፡ ፕሮፓጋንዲስት ። በ ፲፰፻፸፭ ዓ. ም. ፕሌኻኖቭ ፡ በጄኔቭ « የወዝ ፡ አደር ፡ ነፃ ፡ አውጪ » የተባለውን ፡ የመጀመሪያውን ፡ የሩሲያ ፡ ማርክሲስታዊ ፡ ድርጅት ፡ መሠረተ ። ፕሌኻኖቭ ፡ ናሮድኒዝምን ፡ ታግሏል ። በዓለም ፡ አቀፍ ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ ንቅናቄ ፡ ውስጥ ፡ ከላሽነትን ፡ ተዋግቷል ። በ ፲፱፻ ዎቹ ፡ ዓመታት ፡ መጀመሪያ « ኢስክራ » (« ብልጭታ ») የተባለው ፡ ጋዜጣንና ፡ « ዛርያ »(« ጎህ ») የተባለውን ፡ መጽሔት ፡ ከሚያዘጋጁ ፡ አንዱ ፡ ነበር ።

ከ ፲፰፻፸፭ እስከ ፡ ፲፱፻፫ ዓ. ም. ባለው ፡ ጊዜ ፡ ውስጥ ፡ ፕሌኻኖቭ ፡ ማቴሪያሊስታዊ (ቁስ ፡ አካላዊ) ርዕዮተ ፡ ዓለምን ፡ በመከላከልና ፡ ፕሮፓጋንዳ ፡ በማስፋፋት ፡ ከፍተኛ ፡ ሚና ፡ የተጫወቱ ፡ ብዙ ፡ ሥራዎች ፡ ጽፏል ። ሆኖም ፡ ያኔም ፡ ቢሆን ፡ ከባድ ፡ ስህተቶች ፡ ነበሩት ። እነዚህ ፡ ስህተቶች ፡ ለወደፊት ፡ የሜንሼቪክ ፡ ርዕዮቱ ፡ መሠረቶች ፡ ሆነዋል ። ከሁለተኛው ፡ የሩሲያ ፡ ሶሺያል-ዴሞክራቲክ ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ ፓርቲ (ሩ. ሶ. ዴ. ወ. ፓ.) ጉባኤ ፡ በኋላ ፡ ፕሌኻኖቭ ፡ ከአድርባይነት ፡ ጋር ፡ የመታረቅን ፡ አዝማሚያ ፡ ያዘ ፤ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ከሜንሼቪኮች ፡ ጋር ፡ ተቀላቀለ ። በአንደኛው (የ፲፱፻፭ ዓ. ም.) የሩሲያ ፡ አብዮት ፡ ዋና ፡ ዋና ፡ ጥያቄዎች ፡ በሙሉ ፡ አቋሙ ፡ ሜንሼቪክ ፡ ነበር ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስት ። ከ ፲፱፻፲ ዓ. ም. የየካቲቱ ፡ የቡርዥዋ ፡ ዴሞክራቲክ ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሩሲያ ፡ ተመልሶ ፡ የቀኝ ፡ አክራሪው ፡ የሜንሼቪኮች ፡ ቡድንን ፡ መርቷል ። ሩሲያ ፡ ወደ ፡ ሶሺያሊዝም ፡ ለመሸጋገር ፡ ገና ፡ አልደረሰችም ፡ በማለት ፡ ቦልሼቪኮችንና ፡ ሶሺያሊስታዊ ፡ አብዮትን ፡ ተቃውሚል ። የጥቅምቱ ፡ ሶሺያሊስት ፡ አብዮትን ፡ አልደገፈም ፤ ይሁን ፡ እንጂ ፡ የሶቪዬት ፡ መንግሥት ፡ በመቃወም ፡ በተደረገው ፡ ትግል ፡ አልተካፈለም ።

ገጽ ፤ ፰ ፤ ፺፮ ፤ ፸ ፤ ፹ ፤ ፻፵፰ ፤ ፻፶፮ ፤ ፻፶፯ ፤ ፻፹ ፤ ፻፹፩

ፕሩዶን ፤ ፕየር-ዦዘፍ (Proudhon) (፲፰፻፱-፲፰፻፷፭ ዓ. ም.) — ፈረንሳዊ ፡ ፑብሊሲስት ፤ ኤኮኖሚስትና ፡ ሶሺአሎጂስት ። የንኡስ ፡ ቡርዥዋ ፡ አይዲኦሎጂስት ። ሥርዓተ-አልበኝነትን ፡ ከመሠረቱት ፡ አንዱ ።

ገጽ ፤ ፸፱-፹፩ ፤ ፺፰ ፤ ፻፵፯ ፤ ፻፰

ፖምያሎቭስኪይ ፤ ኒኮላይ (፲፰፻፴፭-፲፰፻፷፫ ዓ. ም.) — ሩሲያዊ ፡ ደራሲ ፡ ዴሞክራት ። በጽሑፎቹ ፡ የሩሲያን ፡ ቢሮክራቲክ-አውቶክራሲን ፤ ግፍንና ፡ ገደብ ፡ አልባ ፡ ጭቆናን ፡ ተቃውሟል ።

ገጽ ፡ ፻፵፯

ፖትሬሶቭ ፤ አሌክሳንደር (፲፰፻፷፱-፲፱፻፴፬ ዓ. ም.) — ከሜንሼቪዝም ፡ መሪዎች ፡ አንዱ ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስት ። ከጥቅምት ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡ ሩሲያን ፡ ለቆ ፡ ሄደ ።

ገጽ ፤ ፰ ፤ ፻፹፩

ቨይደመየር ፤ ጆዜፍ (Weydemeyer) (፲፰፻፲፰-፲፰፻፷፮ ዓ. ም.) — የታወቀ ፡ የጀርመንና ፡ የአሜሪካ ፡ የወዝ ፡ አደር ፡ እንቅስቃሴ ፡ ታጋይ ፤ የማርክስና ፡ የኤንግልስ ፡ ጓደኛና ፡ የሥራ ፡ ጓድ ።

ገጽ ፡ ፶፩

ቫንደርቬልድ ፤ ኤሚል (Vandervelde) (፲፰፻፷፮-፲፱፻፴፰ ዓ. ም.) — የበልጀግም ፡ የሠራተኛ ፡ ፓርቲ ፡ መሪ ፤ የሁለተኛው ፡ ኢንተርናሽናል ፡ ዓለም ፡ አቀፍ ፡ ሶሺያሊስት ፡ ቢሮ ፡ ሊቀ ፡ መንበር ፤ በአቋሙ ፡ አክራሪ ፡ አድርባይ ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ — ሶሺያል-ሾቪኒስት ። የቡርዥዋው ፡ መንግሥት ፡ አባል ። ከ ፲፱፻፲፯ ዓ. ም. የየካቲቱ ፡ ቡርዥዋ ፡ ዴሞክራቲክ ፡ አብዮት ፡ በኋላ ፡



የኢምፔሪያሊስቱ ፡ ጦርነት ፡ እንዲቀጥል ፡ ቅስቀሳ ፡ ለማድረግ ፡ ወደ ፡ ሩሲያ ፡ መጥቶ ፡ ነበር ።

ገጽ ፤ ፰ ፤ ፸ ፤ ፸፫ ፤ ፻፹ ፤ ፻፹፩

ዌብ ፤ ሲድኒ (Webb) (፲፰፻፶፱-፲፱፻፵፯ ዓ. ም.) — የታወቀ ፡ እንግሊዛዊ ፤ ሬፎርሚስት ። ከሚስቱ ፡ ከቤአትሪስ ፡ ዌብ ፡ ጋር ፡ ሆኖ ፡ ስለ ፡ እንግሊዝ ፡ ሠራተኞች ፡ ንቅናቄ ፡ ታሪክና ፡ ቴዎሪ ፡ ብዙ ፡ ጽፏል ። የንኡስ ፡ ቡርዥዋና ፡ የሠራተኛ ፡ አሪስቶክራት ፡ ርዕዮተ ፡ ዓለም ፡ አመንጪ ። ሲድኒ ፡ ዌብ ፡ በሥራዎቹ ፡ ውስጥ ፡ የሚሰብከው ፡ የወዝ ፡ አደሩ ፡ ጥያቄ ፡ በካፒታሊስት ፡ ኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ሥር ፡ በሰላም ፡ እንዲፈታ ፡ ነው ። ሬፎርሚስት ፡ ፋቢያን ፡ ማኅበር ፡ ከመሠረቱን ፡ አንዱ ፡ ነበር ። በአንደኛው ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ አቋሙ ፡ ሶሺያል-ሾቪኒስት ። በአንደኛው (፲፱፻፳፬ ዓ. ም.) እና ፡ በሁለተኛው (፲፱፻፳፱-፲፱፻፴፩ ዓ. ም.) የሌበር ፡ መንግሥት ፡ አባል ።

ገጽ ፡ ፻፸፯

ዌብ ፤ ቤአትሪስ (Webb) (፲፰፻፶፰-፲፱፻፵፫ ዓ. ም.) — በእንግሊዝ ፡ የኅብረተ ፡ ሰብ ፡ ጉዳይ ፡ የታወቀች ፡ ሴት ።

ገጽ ፡ ፻፸፯







## አንባብያን ፡ ሆይ!

የፕሮግሬስ ፡ የመጻሕፍት ፡ ማዘጋጃና ፡ ማሳተሚያ ፡ ቤት ፡ ስለዚች ፡ መጽሐፍ ፡ ትርጉም ፤ ዝግጅትና ፡ እትም ፡ ያላችሁን ፡ አስተያየትና ፡ አሳባችሁን ፡ ብትገልጹለት ፡ በደስታ ፡ ይቀበላል ።

አድራሻው ፤

17, Zubovsky Boulevard,
Moscow, U.S.S.R.





